# ማኅደረ ፡ ብርሃን ።

## ሀገረ ፡ ጃፓን ።

ተጻፈ ፡

ከኅሩይ ፡ ወልደ ፡ ሥላሴ ።

በጎሀ ፡ ጽባሕ ፡ ማተሚያ ፡ ታተመ ።

፲፱፻፳፬ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡ አዲስ ፡ አበባ ።

# ከአዲስ ፡ አበባ ፡ እስከ ፡ ጂቡቲ ።

## መጀመሪያ ፡ ትልቅ ፡ ክፍል ።

### ከአዲስ ፡ አበባ ፡ እስከ ፡ ጃፓን ፡ የወደብ ፡ ከተማ ፡ እስከ ፡ ኮቤ ፡ ስለ ፡ ሆነው ፡ ነገር ።

ከጃንሆይ ፡ መሰናበት ። ከቤተ ፡ ዘመድ ፡ መሰነባበት ። በባቡር ፡ መቋሚያ ። አንበጣና ፡ አዋሽ ። ድሬዳዋ ። ጂቡቲ ። አንዱሬሊቦን ፡ መርከብ ። አደን ። ኮሎምቦ ። ሲንጋፑር ። ሳይጎን ። ሆንግኮንግ ። ሻንጋሂ ። የፔሲፊክ ፡ ውቅያኖስ ።

### ምዕራፍ ፡ ፩ ።

ወደ ፡ ጃፓን ፡ የምንወስደው ፡ ማናቸውም ፡ ነገር ፡ ከተዘጋጀ ፡ በኋላ ፡ በመስከረም ፡ ፳፩ ፡ ቀን ፡ ከማታው ፡ በ፫ ፡ ሰዓት ፡ በሚነሣው ፡ ባቡር ፡ ለመሔድ ፡ ቁርጥ ፡ የሆነ ፡ ትእዛዝ ፡ በተቀበልሁ ፡ ጊዜ ፡ የምነሣበትን ፡ ቀን ፡ ለሚጠይቁኝ ፡ ወዳጆቼ ፡ ሁሉ ፡ አስታወቅኋቸው ።

ለመሔድም ፡ የታዘዝሁበት ፡ ቀን ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ለጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የማቀርበውን ፡ የጃንሆይን ፡ ደብዳቤና ፡ የኒሻኑን ፡ ሽልማት ፤ ሌላውንም ፡ እንደ ፡ ገጸ ፡ በረከት ፡ ሆኖ ፡ የሚቀርበውን ፡ ሁሉ ፡ ተቀብዬ ፡ በጃንሆይ ፡ ፊት ፡ እጅ ፡ ነሥቼና ፡ ተሰናብቼ ፡ ወጣሁ ።

ወዲያውም ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ ሔጄ ፡ ከቤተ ፡ ዘመዶቼ ፡ ተሰነባበትሁ ። ነገር ፡ ግን ፤ ከዚህ ፡ ቀድሞ ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ ያህል ፡ ወደ ፡ አውሮጳ ፡ በመሔዴ ፡ የባቡሩንና ፡ የመርከቡን ፡ መንገድ ፡ መልመዴ ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ የታወቀ ፡ ቢሆን ፡ የዛሬው ፡ መንገዴ ፡ ከአውሮጳ ፡ ሁለት ፡ እጅ ፡ የሚርቅ ፡ መሆኑን ፡ ቤተ ፡ ዘመዶቼ ፡ ስለ ፡ ሰሙ ፡ የሁሉም ፡ ልብ ፡ ከማዘኑ ፡ የተነሣ ፡ ዓይናቸው ፡ በእንባ ፡ ይታጠብ ፡ ጀመር ። እኔ ፡ ግን ፡ ልባቸው ፡ በጣም ፡ እንዳይባባ ፡ ስለ ፡ አሰብሁ ፡ እንባዬን ፡ ታግሼ ፡ በፍጥነት ፡ ተሰነባብቻቸው ፡ ወደ ፡ ባቡር ፡ መቋሚያ ፡ ወረድሁ ። በደረስሁም ፡ ጊዜ ፡ ከመሳፍንቱና ፡ ከመኳንንቱ ፡ ወገን ፡ ብዙዎቹ ። ደግሞ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ የሚኖሩ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሚኒስትሮችና ፡ ቆንስሎች ፡ ሌሎችም ፡ ወዳጆቼ ፡ የሆኑ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ትልልቅ ፡ ሰዎች ፡ ሊሸኙኝ ፡ መጥተው ፡ አገኘኋቸው ።

## መቅድም ።

ኢትዮጵያ ፡ ከቀድሞ ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ ከውጭ ፡ አገር ፡ መንግሥቶች ፡ ጋራ ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ እየተገናኘች ፡ ስትኖር ፤ እስካሁን ፡ ከጃፓን ፡ መንግሥት ፡ ጋራ ፡ ሳትገናኝ ፡ የቆየችበትንና ፡ አሁን ፡ ከመቃረብና ፡ ከመገናኘት ፡ የደረሰችበትን ፡ ለዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ አንባቢዎች ፡ አጭር ፡ ማስረጃ ፡ እጽፋለሁ ።

ይህንም ፡ ስጽፍ ፡ ከንግሥተ ፡ ሳባ ፡ ወዲህ ፡ ባለው ፡ ዘመን ፡ ውስጥ ፡ የሆነውን ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከዚያ ፡ አስቀድሞ ፡ የነበረውን ፡ በጭራሽ ፡ አላነሣሁትም ።

ማክዳ ፡ የተባለችው ፡ ንግሥተ ፡ ሳባ ፡ የነገሠችው ፡ ከክርስቶስ ፡ ልደት ፡ አስቀድሞ ፡ በሺ ፡ ዓመት ፡ ነው ። እርስዋ ፡ በነገሠች ፡ በ፳ኛው ፡ ዓመት ፡ የሰሎሞንን ፡ ጥበብ ፡ ለመስማት ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወርዳ ፡ ነበርና ፡ ከሰሎሞን ፡ ፀንሳ ፡ ተመልሳ ፡ ቀዳማዊ ፡ ምኒልክን ፡ ወለደች ።

ቀዳማዊ ፡ ምኒልክም ፡ ካደገ ፡ በኋላ ፡ አባቱን ፡ ሰሎሞንን ፡ ለማየት ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወርዶ ፡ ሲመለስ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ተከትለውት ፡ ወደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ መጥተው ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ ክብረ ፡ ነገሥት ፡ የሚባለው ፡ የታሪክ ፡ መጽሐፋችን ፡ ያስረዳናል ።

ከዚያም ፡ ወዲህ ፡ ከአረብ ፡ አገርና ፡ ከህንድ ፡ አገር ፡ በንግድም ፡ በሌላም ፡ ሥራ ፡ ምክንያት ፡ አንዳንድ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ መምጣታቸው ፡ አልቀረም ።

ደግሞ ፡ በ፲፬፻፴ ፡ ዓ ፡ ም ፡ በአጼ ፡ ዘርአ ፡ ያዕቆብና ፡ በልጁ ፡ በአጼ ፡ በእደ ፡ ማርያም ፡ ዘመን ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ መጥተው ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ የአጼ ፡ ዘርአ ፡ ያዕቆብና ፡ የበእደ ፡ ማርያም ፡ ታሪክና ፡ መጽሐፈ ፡ ምስጢር ፡ የሚባለው ፡ ያባ ፡ ጊዮርጊስ ፡ መጽሐፍ ፡ ያስረዳናል ።

ቀጥሎም ፡ በ፲፭፻፲፭ ፡ ዓ ፡ ም ፡ መሐመድ ፡ ግራኝ ፡ የሚባል ፡ እስላም ፡ ከዘይላ ፡ ተነሥቶ ፡ በአዳል ፡ አገር ፡ መጥቶ ፡ ኢትዮጵያን ፡ ባጠፋ ፡ ጊዜ ፡ በአጼ ፡ ልብነ ፡ ድንግል ፡ ልመና ፡ ብዙ ፡ ፖርቱጊዞች ፡ መጥተው ፡ ግራኝን ፡ ወግተው ፡ በዚሁ ፡ በኢትዮጵያ ፡ እየተራቡ ፡ መኖራቸውን ፡ ታሪከ ፡ ነገሥት ፡ ይመሰክራል ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ከአጼ ፡ ሱስንዮስ ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ አጼ ፡ ፋሲል ፡ ዘመን ፡ ብዙ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ እንደመጡ ፤ ለአጼ

ፋሲልም ፡ የጎንደርን ፡ ግንብና ፡ የዓባይን ድልድይ ፡ እንደ ፡ ሠሩለት ፡ በሙሉ ፡ ኢትዮጵያ ፡ የታወቀ ፡ ነገር ፡ ነው ።

ቀጥሎም፡ በአጼ ፡ ኢያሱ፡ አድያም ፡ ሰገድ ፡ ዘመን ፡ የፈረንሣዊ፡ መንግሥት ፡ ሙሴ ፡ ፔንዞ ፡ የሚባል ፡ ቆንስል ፡ ልኮ ፡ ነበር ።

ከዚያ ፡ ወዲህ ፡ ግን ፡ አገር ፡ እየዞሩ ፡ የሚያዩና ፡ ታሪክ ፡ የሚጽፉ ፡ እንደነ ፡ ጀምስ ፡ ብሩስ ፤ እንደነ ፡ እንጦንዮስ ፡ ዳባዲ ፤ እንደ ፡ ሌሎችም፡ እነዚህን ፡ እንደ ፡ መሰሉ ፡ አንዳንድ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ይመጡ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ በመንግሥት ፡ መላክተኛነት ፡ የመጡ ፡ አልነበሩም ።

በኋላ ፡ ግን ፡ በ፲፰፻፶፪ ፡ ም ፡ አጼ ፡ ቴዎድሮስ ፡ በነገሡ ፡ ጊዜ ፡ የውጭ ፡ አገር፡ ሚሲዮኖች ፡ ወደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ስለ ፡ መጡ ፡ በዚህ፡ምክንያት፡ የእንግሊዝና ፡ የፈረንሣዊ ፡ መንግሥቶች ፡ ቆንስሎች ፤ ልከው ፡ ነበር ።

በአጼ ፡ ዮሐንስም ፡ ዘመን ፡ ከእንግሊዝና ፡ ከኢጣልያ ፡ ከፈረንሣዊም ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ መላክተኞች ፡ እየተላኩና ፡ እየመጡ ፡ ይመለሱ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ በኢትዮጵያ ፡ ነዋሪ ፡ የሆነ ፡ ቆንስል ፡ አልመጣም ፡ ነበር ።

በጃንሆይ ፡ በዳግማዊ ፡ ምኒልክ ፡ ዘመን ፡ ግን ፡ የፈረንሳዊና ፡ የእንግሊዝ ፤ የኢጣልያና ፡ የጀርመን ፤ የአሜሪካና ፡ የመስኮብ ፡ መንግሥቶች ፡ የወዳጅነትና ፡ የንግድ ፡ ውል ፡ እየተዋዋሉ ፡ የቆንስል ፤ ቤትና ፡ ሌጋሲዮን ፡ እስከ ፡ ማቆም ፡ ደረሱ ።

አጼ ፡ ምኒልክም ፡ የወዳጅነትና ፡ የንግድ ፡ ውል ፡ ተዋውለው ፡ ሕዝባቸውን ፡ እስከ ፡ ማቃረብ ፡ ያደረሱት ፡ ከምዕራብ ፡ አውሮጳ ፡ መንግሥቶች ፡ ጋራ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከምሥራቅ ፡ እስያ ፡ መንግሥቶች ፡ ከጃፓን ፤ ከሺን ፤ ከሲያም ፤ ከአናም ፤ ከሌሎቹም ፡ እነዚህን ፡ ከመሰሉት ፡ ካንዳቸውም ፡ ጋራ ፡ የመገናኛ ፡ ውል ፡ አልተዋዋሉም ፡ ነበር ። መዋዋላቸውም ፡ ይቅርና ፡ እስከ ፡ ፲፰፻፺፯ ፡ ም ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ የተቆጠሩት ፡ የምሥራቅ ፡ መንግሥት ፡ አገሮች ፡ መኖራቸው ፡ እንኳ ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ አልታወቀም ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ በ፲፰፻፺፯ ፡ ም ፡ ጃፓንና ፡ መስኮብ ፡ ተዋግተው ፡ ጃፓን ፡ ድል ፡ ባደረገ ፡ ጊዜ ፡ በዚያ ፡ ዘመን ፡ ብዙ ፡ መስኮቦች ፡ በአዲስ ፡ አበባ ፡ ነበሩና ፡ ጃፓን ፡ የሚባል፡ መንግሥት ፡ መኖሩ ፡ ከመስኮቦች ፡ አፍ ፡ ተሰምቶ፡ነበር ።

ከዚያም ፡ ወዲህ ፡ ግርማዊት ፡ ንግሥተ ፡ ነገሥታት ፡ ዘውዲቱ ፡ በነገሡ ፡ ልዑል ፡ ተፈሪ ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ አልጋ ፡ ወራሽና፡ ባለ ፡ ሙሉ ፡ ሥልጣን ፡ እንደራሴ ፡ በሆኑ ፡ በ፳ኛው ፡ ዓመት ፡ የኢት

ዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ ወደ ፡ መንግሥታት ፡ ማኅበር ፡ በገባች ፡ ጊዜ ፡ የ ኢትዮጵያና ፡ የጃፓን ፡ መንግሥት ፡ መላክተኞች ፡ በጄኔብ ፡ ላይ ፡ ተ ገናኝተው ፡ ከመተዋወቅ ፡ ደረሱ ።

በዚያም ፡ ዘመን ፡ ከኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ መላክተኞች ፡ አንደ ኛው ፡ እኔ ፡ ራሴ ፡ ነበርሁ ።

ከዚያም ፡ ወዲህ ፡ ዛሬ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የሆኑት ፡ ልዑል ፡ ተፈሪ ፡ ገና ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ አልጋ ፡ ወራሽና ፡ ባለ ፡ ሙሉ ፡ ሥልጣን ፡ እንደራሴ ፡ ሆነው ፡ ሳሉ ፡ ከውጭ ፡ አገር ፡ መንግሥቶች ፡ ጋራ ፡ ወዳጅ ነት ፡ ለማጽናት ፡ ንግድ ፡ ለማስፋት ፡ ሙሉ ፡ ፈቃድ ፡ እንዳላቸው ፡ በተ ሰማ ፡ ጊዜ ፡ የምሥራቅ ፡ አገር ፡ መጨረሻ ፡ የሚሆን ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ በ፲፱፻፲፯ ዓ ፡ ም ፡ ፖርት ፡ ሳይድ ፡ ላይ ፡ የጃፓን ፡ ቆንስል ፡ ሆኖ ፡ የሚኖረውን ፡ ሙሴ ፡ ክሮኪ ፡ የሚባለውን ፡ ወደ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ልከው ፡ ነገሩን ፡ ሁሉ ፡ አስመረመሩ ።

ልዑል ፡ አልጋ ፡ ወራሽም ፡ ሙሴ ፡ ክሮኪን ፡ በመልካም ፡ አቀባበል ፡ ተቀብለው ፡ ኢትዮጵያን ፡ ወደ ፡ ትልቅ ፡ የሥልጣኔ ፡ ደረጃ ፡ ለማድረስና ፡ ሕዝባቸውን ፡ ለማሠልጠን ፡ ፈቃዳቸው ፡ መሆኑን ፡ ገልጠው ፡ ስለ ፡ ነ ገሩትና ፡ ስለ ፡ አሳዩት ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ ተመልሶ ፡ በአዲስ ፡ አበባ ፡ ያየውንና ፡ የሰማውን ፡ ሁሉ ፡ ለመንግሥቱ ፡ ባስታወቀ ፡ ጊዜ ፡ በ፲፱፻፳ ዓ ፡ ም ፡ ሌላ ፡ ባለ ፡ ሙሉ ፡ ሥልጣን ፡ መላክተኛ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ተልኮ ፡ መጥቶ ፡ የወዳጅነትና ፡ የንግድ ፡ ውል ፡ ተዋውሎና ፡ ተፈራርሞ ፡ ተመለሰ ።

ደግሞ ፡ በ፲፱፻፳፫ ዓ ፡ ም ፡ ግርማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ የንጉሠ ፡ ነገ ሥት ፡ ዘውድ ፡ በሚጭኑበት ፡ ጊዜ ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ስለ ፡ ሁለቱ ፡ መንግሥቶች ፡ ወዳጅነት ፡ የዘውዱን ፡ በዓል ፡ ለማክበር ፡ ምስተ ር ፡ ዮሺዳ ፡ የሚባል ፡ ልዩ ፡ አምባሳደር ፡ ልከው ፡ ነበርና ፡ የዘውዱ ፡ በዓ ል ፡ ሲጨረስ ፡ የወዳጅነቱንና ፡ የንግዱን ፡ ውል ፡ አሳድሶ ፡ ተመልሶ ፡ ነበር ።

የሁለቱም ፡ መንግሥቶች ፡ ወዳጅነት ፡ ይህን ፡ በመሰለ ፡ በጠንካራ ፡ መሠረት ፡ መመሥረቱ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ሆነ ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ጃንሆይ ፡ አፄ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ይህን ፡ መሠረት ፡ ለማጽናትና ፡ በመሠረቱ ፡ ላይ ፡ ሥራ ፡ ለመሥራት ፡ ስለ ፡ ፈቀዱ ፡ እንደ ፡ ዓለም ፡ ነገሥታት ፡ ደንብ ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ለዘውድ ፡ በዓ ላቸው ፡ ልዩ ፡ አምባሳደር ፡ ስለ ፡ መላካቸው ፡ የወዳጅነት ፡ ብድር ፡ ለመ መለስ ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ ልዩ ፡ አምባሳደር ፡ ለመላክ ፡ አሰቡ ።

ይህም ፡ ትልቅ ፡ አሳብ ፡ በታሰበበት ፡ ወራት ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ አልጋ ፡ ወራሽ ፡ ልዑል ፡ መርድ ፡ አዝማች ፡ አስፋ ፡ ወሰን ፡ አውሮጳን ፡ ለመጎብኘት ፡ እንዲሔዱ ፡ ስለ ፡ ታሰበ ፡ እኔ ፡ ልዑልነታቸውን ፡ ተከትዬ ፡ ለመሔድ ፡ ነገሩ ፡ ተቆርጦ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ በሁለቱ ፡ መንግሥቶች ፡ መካከል ፡ የተደረገውን ፡ የወዳጅነትና ፡ የንግድ ፡ ውል ፡ በግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ፈቃድና ፡ በውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስቴርነቴ ፡ ከጃፓን ፡ ልዩ ፡ መላክተኛ ፡ ጋራ ፡ ተነጋግሬ ፡ የተጻጻፍሁትና ፡ የተፈራረምሁት ፡ እኔ ፡ ስለ ፡ ሆንሁ ፡ በልዩ ፡ አምባሳደርነቴ ፡ ላይ ፡ ወዲያውም ፡ የውሉን ፡ አሳብና ፡ አፈጻጸም ፡ በቃል ፡ ለማስረዳት ፡ የእኔ ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ መሔድ ፡ የጃንሆይ ፡ አፄ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ፈቃድ ፡ ስለ ፡ ሆን ፡ የአውሮጳ ፡ መንገዴ ፡ ቀርቶ ፡ ለጃፓን ፡ መንገዴ እንድሰናዳ ፡ ታዘዝሁ ።

ከዚህም ፡ ቀድሞ ፡ በግርማዊነታቸው ፡ ቸርነት ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ መላክተኛ ፡ እየሆንሁ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ እየተመላለስሁ ፡ አውሮጳንና ፡ አሜሪካን ፡ በማየቴ ፡ ደስ ፡ ሲለኝ ፡ እኖር ፡ ነበርና ፡ አሁን ፡ ደግሞ ፡ ከዚህ ፡ ቀደም ፡ ማንም ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ መላክተኛ ፡ ያልሔደበትን ፡ እሩቁን ፡ የፀሐይ ፡ መውጫ ፡ የሚባለውን ፡ የጃፓንን ፡ አገር ፡ በማዕርግና ፡ በክብር ፡ ለማየት ፡ በመታዘዜ ፡ ከታዘዝሁበት ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ በልቤ ፡ ውስጥ ፡ የደስታ ፡ ጐርፍ ፡ ሲጐርፍ ፡ ይሰማኝ ፡ ነበር ።

ለዚህም ፡ ለትልቁ ፡ መልእክቴ ፡ ጂቡቲ ፡ ላይ ፡ ያለው ፡ የኢትዮጵያ ፡ ቆንስል ፡ ልጅ ፡ ተፈራ ፡ ገብረ ፡ ማርያም ፡ ዋና ፡ ጸሐፊ ፡ ሆኖ ፡ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ እንዲሔድ ፡ ታዘዘልኝ ።

ደግሞ ፡ ከግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ዝምድና ፡ ያለው ፡ ልጅ ፡ አርአያ ፡ አበበ ፡ በኦፊሴል ፡ ሳይሆን ፡ አገር ፡ ለማየት ፡ ብቻ ፡ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ እንዲሔድ ፡ ከግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ተፈቀደለት ።

ለአስተርጓሚነትም ፡ በውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስቴር ፡ የአስተርጓሚነት ፡ ሥራ ፡ የሚሠራ ፡ አቶ ፡ ዳባ ፡ ብሩ ፡ ታዘዘልኝ ።

ስለዚህ ፡ መንገዳችን ፡ ሁሉ ፡ የደስታና ፡ የፍቅር ፡ መንገድ ፡ ሆኖ ፡ ነበር ።

ለማናቸውም ፡ ቢሆን ፡ ከአዲስ ፡ አበባ ፡ ተነሥቼ ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ ደርሼ ፡ መልእክቴን ፡ ፈጽሜ ፡ ወደ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ እስከ ፡ ተመለስሁበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ በየለቱ ፡ ከሠራሁትና ፡ ካየሁት ፡ ሁሉ ፡ ፍሬ ፡ ነገሩን ፡ እየለየሁ ፡ ጽፌዋለሁና ፡ ለአንባቢዎቹ ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ትምሕርት ፡ እንዲሆናቸው ፡ እርግጥ ፡ ነው ።

ደግሞ ፡ ለነገሩ ፡ ማያያዣና ፡ ለአንባቢዎቹ ፡ ማስረጃ ፡ እንዲሆን ፡ ብዬ ፡ ከጃፓን ፡ አገር ፡ ታሪክ ፡ ባንዳንድ ፡ ስፍራ ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ እያገባሁ ፡ ጽፌዋለሁ ።

ከዚህም ፡ በቀር ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ ከነገሥታቱና ፡ ከሕዝቡ ፡ ኑሮ ፡ ከሀገራችን ፡ ነገሥታትና ፡ ሕዝብ ፡ ኑሮ ፡ ጋራ ፡ ብዙ ፡ የሚመሳሰል ፡ ስለ ፡ አገኘሁ ፡ በየስፍራው ፡ እያገባሁ ፡ ጽፌአለሁ ።

ይልቁንም ፡ ለአሁኑ ፡ መልእክቴ ፡ እጅግ ፡ የረዳኝና ፡ የጠቀመኝ ፡ ያገራችንን ፡ የኢትዮጵያን ፡ የቤተ ፡ መንግሥቱንም ፡ የቤተ ፡ ክህነቱንም ፡ ታሪክ ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ ማንበቤና ፡ ማወቄ ፡ ነው ።

ወደ ፡ ፊትም ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አገር ፡ የሚላክ ፡ መላክተኛ ፡ የኢትዮጵያን ፡ ታሪክ ፡ ያነበበና ፡ ያወቀ ፡ ቢሆን ፡ ትልቅ ፡ ጥቅም ፡ መሆኑን ፡ ለግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥትና ፡ ለሚላከው ፡ መላክተኛ ፡ ማሳሰብ ፡ የሚገባኝ ፡ ነው ።

ይልቁንም ፡ እንደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ ሕዝቡ ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ ለመስማትና ፡ ለማወቅ ፡ በሚፈልጉበት ፡ አገር ፡ የሚላክ ፡ ሰው ፡ ያገሩን ፡ ታሪክ ፡ ተጠይቆ ፡ አላውቅም ፡ ቢል ፡ ትልቅ ፡ ኀፍረት ፡ ይሆንበታልና ፡ በመንግሥት ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ የሚኖር ፡ ስሙ ፡ የታወቀ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የኢትዮጵያን ፡ ታሪክ ፡ ማንበብና ፡ ማወቅ ፡ ያስፈልገዋል ።

ይህንም ፡ ማለቴ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ልጆች ፡ ያገራቸውንና ፡ የነገሥታቱን ፡ ታሪክ ፡ እንዲማሩ ፡ ለማነቃቃት ፡ በቅንነት ፡ አሳብ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ታሪክ ፡ አውቃለሁ ፡ በማለት ፡ የተመከሁ ፡ እንዳይመስላቸው ፡ የዚህን ፡ መጽሐፍ ፡ አንባቢዎች ፡ ሁሉ ፡ እለምናለሁ ።

ኅሩይ ወልደ ሥላሴ

ከነዚህም ፡ በቀር ፡ አብሮ ፡ አደጎቼና ፡ ወዳጆቼ ፡ ከየስፍራው ፡ መጥ ተው ፡ ነበርና፡የባቡሩ ፡ መቋሚያ ፡ ስፍራ ፡ ውጭውም ፡ ግቢውም ፡ ሰው ፡ ብቻ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ መተላለፊያ ፡ እንኳ ፡ ቸግሮ ፡ ነበር ።

አንድ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መላክተኛ ፡ ተልኮ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አገር ፡ ሲሔድ ፡ መሳፍንቱና ፡ መኳንንቱ ፡ ወደ ፡ ባቡር ፡ መቋሚያ ፡ መጥተው ፡ መሸኘታቸው ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱንና ፡ መንግሥታቸውን ፡ ማክበራቸውን ፡ ያስረዳል ፡ እንጂ ፡ የኔን ፡ ክብር ፡ ብቻ ፡ አያስረዳምና ፡ ከትልቅ ፡ የሥ ልጣኔ ፡ ሥራ ፡ ይቆጠርላቸዋል ።

ከማታውም ፡ ፫ሰዓት ፡ ሲሆን ፡ ባቡሩ ፡ የሚነሣ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ከሁሉ ም ፡ ጋራ ፡ ተሰነባብቼ ፡ ወደ ፡ ባቡሩ ፡ ውስጥ ፡ በገባሁ ፡ ጊዜ ፡ በባቡሩ ፡ ዳር ፡ ተሰልፈው ፡ ቆመው ፡ የነበሩት ፡ የከተማ ፡ ዘበኞች ፡ የመሰናበቻ ፡ ጡሩምባ ፡ ነፍተው ፡ ባቡሩ ፡ ተጓዘ ።

ሌሊቱንም ፡ ስንጓዝ ፡ ከአዳማ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ውልንጭቱ፡ ባቡ ሩ ፡ በቀስታ ፡ ይሔድ ፡ ነበርና ፡ ምክንያቱን ፡ ብንጠይቅ ፡ በባቡሩ ፡ መ ንገድ ፡ ላይ ፡ ብዙ ፡ አንበጣ ፡ ስለ ፡ ሰፈረበት ፡ ባቡሩን ፡ እንዳያድጠውና አደጋ ፡ እንዳያገኘው ፡ ለመጠንቀቅ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

በማግሥቱም ፡ ባንድ ፡ ሰዓት ፡ አዋሽ ፡ ደረስንና ፡ አንድ ፡ ሰዓት ፡ ያ ህል ፡ አርፈን ፡ ባቡሩ ፡ ጉዞ ፡ ጀመረ ። በየመንገዱም ፡ ብዙ ፡ አንበጣ ፡ ይታይ ፡ ነበርና ፡ ምናልባት ፡ ያገሩን ፡ ሰብል ፡ ያበላሸው ፡ ይሆንን ፡ በ ማለት ፡ ልባችን ፡ ያዝን ፡ ነበር ።

፲፩ ሰዓት ፡ ሲሆን ፡ ድሬዳዋ ፡ ስለ ፡ ደረስን ፡ የድሬዳዋ ፡ ሹሞች ፡ የ ከተማውን ፡ ዘበኞች ፡ አሰልፈው ፡ ተቀበሉን ። ድሬዳዋም ፡ እራታችን ን ፡ በልተን ፡ ከራት ፡ በኋላ ፡ በድሬዳዋ ፡ ካሉ ፡ ወዳጆቻችን ፡ ተሰነባብ ተን ፡ በ፩ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ወደ ፡ ጂቡቲ ፡ ወረድን ። ጂቡቲም ፡ ከነጋቱ ፡ በ፲፪ሰዓት ፡ ደረስን ። በባቡር ፡ መቋሚያም ፡ የጂቡቲ ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ ዋና ፡ ጸሐፊ ፡ መጥቶ ፡ ያገረ ፡ ገዥውን ፡ ሰላምታ ፡ ከነገረን፡በኋላ ፡ ወዲያውም፡ ምሳ ፡ እንድንጋበዝላቸው ፡ መለመናቸውን ፡ አስታወቀን ። ከዚህም ፡ በኋ ላ ፡ እስከ ፡ ፯ሰዓት ፡ በሆቴል ፡ ቆይተን ፡ ወደ ፡ አገረ ፡ ገዥው ፡ ቤት ፡ ሔደን ፡ ምሳ ፡ ተጋብዘን ፡ ተመለስን ።



ከጂቡቲ ፡ እስከ ፡ ጃፓን ፡ የባሕር ፡ ወደብ ፡ ከተማ ፡ እስከ ፡ ኮቤ ፡ የሔድ
ንበት ፡ አንድሬ ፡ ሊቦን ፡ የሚባለው ፡ የማሳጂረ ፡ ማሪቲም ፡ መርከብ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

በመስከረም ፡ ፳፫ ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ማታ ፡ በ፲ ፡ ሰዓት ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ የምንሔድበት ፡ አንድሬ ፡ ሊቦን ፡ የሚባለው ፡ የማሳጂረ ፡ ማሪትም ፡ ኩምፓንያ ፡ መርከብ ፡ ጂቡቲ ፡ ደረሰ ።

የኩምፓኒያውም ፡ ሹም ፡ መርከቡ ፡ ከጂቡቲ ፡ የሚነሣው ፡ ከሌሊቱ ፡ በ፲ ፡ ሰዓት ፡ መሆኑን ፡ ስለ ፡ አስታወቀን ፡ በ፮ ፡ ሰዓት ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ገባን ።

አንድሬ ፡ ሊቦን ፡ የሚባለው ፡ መርከብ ፡ ከትልልቆቹ ፡ ከፈረንሳዊ ፡ መርከቦች ፡ አንደኛው ፡ ነው ። ከተሠራም ፡ ፲፫ ፡ ዓመቱ ፡ ነው ። አንድሬ ፡ ሊቦን ፡ ተብሎ ፡ የተሰየመበት ፡ ምክንያቱ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ እንዳለው ፡ ነው ።

ሙሴ ፡ አንድሬ ፡ ሊቦን ፡ ከማሳጂረ ፡ ማሪትም ፡ ኩምፓኒዮች ፡ አንደኛው ፡ ነው ። እርሱም ፡ አስቀድሞ ፡ የፈረንሳዊ ፡ መንግሥት ፡ የንግድ ፡ ሚኒስትር ፡ ሆኖ ፡ ተሾሞ ፡ ነበር ። በኋላ ፡ ግን ፡ የኩምፓኒያውን ፡ ሥራ ፡ ይዞ ፡ ፕሬዚዳንነቱን ፡ ስለ ፡ ተሾመ ፡ በኩምፓኒያው ፡ ፕሬዚዳንነቱ ፡ ለማኅበሩ ፡ የሚጠቅም ፡ ብዙ ፡ ሥራ ፡ ሠርቶ ፡ ነበር ። ይልቁንም ፡ በምሥራቅ ፡ አገር ፡ ትልልቅ ፡ መርከቦች ፡ ለመስደድ ፡ አልተለመደም ፡ ነበርና ፡ እርሱ ፡ ማኅበሩን ፡ አደፋፍሮ ፡ ትልልቆች ፡ መርከቦች ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ አገር ፡ እንዲሔዱ ፡ በማድረጉ ፡ ኩምፓኒያው ፡ ትልቅ ፡ ጥቅም ፡ አግኝቶ ፡ ነበር ።

በዚህም ፡ መካከል ፡ ይህ ፡ ትልቅ ፡ መርከብ ፡ በተሠራ ፡ ጊዜ ፡ ኩምፓኒያው ፡ እንደ ፡ ሽልማት ፡ አድርጎ ፡ አንድሬ ፡ ሊቦን ፡ ተብሎ ፡ በስሙ ፡ እንዲጠራ ፡ አደረገለት ።

የመርከቡ ፡ ሞላልነት ፡ ከኋላው ፡ እስከ ፡ ግንባሩ ፡ ፻፷፪ ፡ ሜትር ፤ ስፋቱ ፡ ፲፰ ፡ ሜትር ፤ ክብደቱ ፡ ፳ ሺ ፡ ቶን ፡ ነው ። ፩ ፡ ቶን ፡ ሺ ፡ ኪሎ ፡ ነው ። ስለዚህ፡ ፳ው፡ሺ፡ቶን ፡ ፳ ሚሊዮን ፡ ኪሎ ፡ መሆኑ፡ነው ።

ፍጥነቱም ፡ ባንድ ፡ ሰዓት ፡ ፴፮ ፡ ኪሎ ፡ ሜትር ፡ ለመሔድ ፡ ይችላል ። ባሥራ ፡ ሁለት ፡ ሰዓት ፡ ፬፻፴፪ ፡ ኪሎ ፡ ሜትር ፡ ይሔዳል ።

በመርከቡ ፡ ውስጥ ፡ ያሉት ፡ ሹሞች ፡ ከዋናው ፡ ኮማንዳ ፡ ጋራ ፡ ፳ ፡ ናቸው ። ሠራተኞቹና ፡ አገልጋዮቹም ፡ ፪፻፳ ፡ ናቸው ። በድምሩ ፡ ፪፻፵ ፡ ማለት ፡ ነው ።

2 0 0 0 0
1 0
2 0 0 0 0

ከነዚህም ፡ በቀር ፡ ለዘጠኝ ፡ መቶ ፡ መንገደኞች ፡ የሚበቃ ፡ ስፍራና ፡ አልጋ ፡ አለበት ።

የመርከቡ ፡ ሹሞች ፡ ከኮማንዳው ፡ ጀምሮ ፡ ለሹመት ፡ ምልክት ፡ በ ባርኔጣቸውና ፡ በእጃቸው ፡ ላይ ፡ የወርቅ ፡ ጥብጣብ ፡ አላቸው ። የኮማ ንዳው ፡ ፬ጥብጣብ ፡ ነው ። የቀሩት ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ማዕርጋቸው ፡ ከ፩እስ ከ ፡ ፫ ጥብጣብ ፡ ያደርጋሉ ።

ይህንም ፡ የሚሸልማቸው ፡ ከመንግሥት ፡ እያስፈቀደ ፡ የኩምፓኒያ ው ፡ ፕሬዚዳን ፡ ነው ።

በመስከረም ፡ ፳፬ ቀን ፡ ከሌሊቱ ፡ በ፲ሰዓት ፡ መርከቡ ፡ ጉዞ ፡ ጀመ ረና ፡ በ፳ሰዓት ፡ አደን ፡ ከተማ ፡ ደረስን ። መርከቡም ፡ ፬ሰዓት ፡ ያህ መቆሙን ፡ ኮማንዳው ፡ አስታውቆን ፡ ነበርና ፡ የአደንን ፡ ከተማ ፡ ለ[illegible] ት ፡ በጀልባ ፡ ተሻግረን ፡ ሔድን ።

ከ፳ዓመት ፡ አስቀድሞ ፡ ልዑል ፡ ራስ ፡ ካሣ ፡ ተከትዬ ፡ ወደ [illegible] ንግሊዝ ፡ አገር ፡ በሔድሁ ፡ ጊዜ ፡ የአደንን ፡ ከተማ ፡ አይቼው [illegible] ና ፡ አሁን ፡ በመንገዱም ፡ መታደስ ፤ በከተማውም ፡ ማማር ፡ በ[illegible] ለውጦ ፡ ስለ ፡ አገኘሁት ፡ እጅግ ፡ አደነቅሁ ።

ደግሞ ፡ ከሁለት ፡ ዓመት ፡ በፊት ፡ የአረቢያ ፡ ትሬዲንግ ፡ [illegible]ኒ ያ ፡ ወኪል ፡ ሆኖ ፡ በአዲስ ፡ አበባ ፡ ይኖር ፡ የነበረው ፡ ወዳጃ[illegible] ቤቴል ፡ በአደን ፡ መኖሩን ፡ አውቅ ፡ ነበርና ፡ ወደ ፡ መካከለኛ[illegible] አደ ን ፡ ከተማ ፡ ሔጄ ፡ ከእርሱ ፡ ጋራ ፡ ስለ ፡ ተገናኘን ፡ ሁለታችን[illegible]ጅግ ፡ ደስ ፡ አለን ። ወዲያውም ፡ ለመንገዳችን ፡ የሚያስፈልገንን [illegible]ንድ ፡ ዕቃ ፡ ገዝተን ፡ ወደ ፡ መርከባችን ፡ ተመለስንና ፡ ከማታው[illegible]ኩል ፡ ሰዓት ፡ መርከባችን ፡ ጉዞ ፡ ጀመረ ።

በሁለተኛውም፡ቀን፡የሶኮተራን፡ደሴት፡በስተቀኛችን፡[illegible]፡አለፍን። በጥቅምት ፡ ፩ ቀን ፡ ጧት ፡ በ፲፪ ሰዓት ፡ ኮሎምቦ ፡ [illegible] ፡ ደረስን ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

ኮሎምቦ ፡ የሴሎን ፡ ደሴት ፡ ዋና ፡ የወደብ ፡ [illegible] ፡ ነው ።

መርከባችንም ፡ እንደቆመ ፡ የሴሎን፡ አገረ፡ ገ[illegible]፡ ጸሐፊ፡ ወደ፡ መርከቡ፡ መጥቶ፡ ያገረ ፡ ገዥውን፡ ሰላምታና፡ ወ[illegible]ም፡ለምሳ፡መጥራ ታቸውን ፡ ከነገረን ፡ በኋላ ፡ የኮሎምቦን፡ከተማ ፡ እ[illegible]ለማየት፡ቢፈልጉ፡ አገረ፡ገዥው፡የራሳቸውን ፡ አውቶሞቢል፡ ይልክ[illegible]ሎ፡ አስታወቀኝ ።



ወደ ፡ ጃፓን ፡ ስንሔድ ፡ የኮሎምቦን ፡ ከተማ ፡ ለማየት ፡ ከመርከብ ፡ እንደ ፡ ወረድን ።

ወዲያውም ፡ በ፩ ሰዓት ፡ ወጥተን ፡ እስከ ፡ ፮ ሰዓት ፡ ከተማውን ፡ እየ ዞርን ፡ አየን ። የኮሎምቦ ፡ ከተማና ፡ መንገዱ ፡ በየመንገዱም ፡ ዳር ፡ ያ ሉት ፡ ዛፎች ፡ እጅግ ፡ ያምራሉ ።

ሴሎን ፡ የእንግሊዝ ፡ ቅኝ ፡ አገር ፡ ናት። በየዋናውም፡ ሥራ ፡ ላይ፡ ያሉት ፡ ሹሞችና ፡ አማካሪዎች ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ ፲፱፻፳፪ ዓመት ፡ እንግሊ ዞች ፡ ነበሩ ። አሁን ፡ ግን ፡ የእንግሊዝ ፡ መንግሥት ፡ መክሮ ፡ ለየዋናው፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ሹሞችና ፡ አማካሪዎች ፡ የሚሆኑ ፡ ከባላገሮቹ፡ መካከል ፡ እንዲመረጡ ፡ ፈቅዶላቸዋል ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

፯ ሰዓትም ፡ ሲሆን ፡ ለምሳ ፡ ወደ ፡ አገረ ፡ ገዥው ፡ ቤት ፡ ሔድን ። ከምሳም ፡ በኋላ ፡ የአንቲካ ፡ ቤቱንና ፡ ሌላውንም ፡ በከተማው ፡ ያለውን፡ ማለፊያ ፡ ማለፊያውን ፡ ስፍራ ፡ ስናይ ፡ ቆይተን ፡ ኮሎምቦ ፡ ያለው ፡ የ ማሳጀሪ ፡ ማሪትም ፡ ኩምፓንያ ፡ ወኪል ፡ ራት ፡ ጋብዞን ፡ ነበርና ፡ ከ ማታው ፡ በሁለት ፡ ሰዓት ፡ ወደዚያ ፡ ሔድን ።

የመርከቡም ፡ ኮማንዳ ፡ ከኛው ፡ ጋራ ፡ ለራት ፡ ተጋብዞ ፡ ነበርና ፡ ከ ራት ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ተመልሰን ፡ ከሌሊቱ ፡ በ፮ ሰዓት ፡ መርከባ ችን ፡ ወደ ፡ ሲንጋፑር ፡ ጉዞ ፡ ጀመረ ፡ በነጋም ፡ ጊዜ ፡ ፖርቶስ ፡ የሚ ባለው ፡ የማሳጀሪ ፡ መርከብ ፡ ጃፓን ፡ ደርሶ ፡ ሲመለስ ፡ ባጠገባችን ፡ አለፈ ።

በጥቅምት ፡ ፫ ቀን ፡ ከማታው ፡ በ፩ ሰዓት ፡ ሱማትራ ፡ የሚባለውን ፡ ደሴት ፡ በስተ ፡ ቀኛችን ፡ እያየነው ፡ አለፍን ።

በመርከቡም ፡ ከነበሩ ፡ ሰዎች ፡ የሚበዙት ፡ ፈረንሣዮች ፡ ናቸው፡ ከፖ ርቱጊዝና ፡ ከእስፓንያ ፡ ከቤልጅክም ፡ ጥቂቶች ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ።

ቢሆንም ፡ ሩቅ ፡ መንገድ ፡ ባንድነት ፡ የሚጓዙ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ሁሉም ፡ በንግግር ፡ ተላምደው ፡ ማታ ፡ ማታ ፡ ከራት ፡ በኋላ ፡ ከ፫ ሰዓት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ፮ ሰዓት ፡ ድረስ ፡ በመርከቡ ፡ ወለል ፡ ዳንስ ፡ ( ጭፈራ ፡ ) እያደ ረጉ ፡ ሲጫወቱ ፡ ያመሹ ፡ ነበር ።

ነገር ፡ ግን ፡ ከጥቅምት ፡ ፩ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ጥቅምት ፡ ፯ቀን፡ ልዩ ፡ ጨዋታ ፡ ለማድረግ ፡ አስበው ፡ ነበርና ፡ ለዚሁ ፡ ጨዋታ ፡ ገን ዘብ ፡ መሰብሰቢያ ፡ የተሠራና፡የሚሸጥ ፡ ወረቀት ፡ አሰናድተው ፡ ልጃ ገረዶች ፡ ልጆች፡ ተመርጠው ፡ በመርከቡ ፡ ላለው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ መሸጥ፡ ጀመሩ ። ያንዱ ፡ ወረቀት ፡ ዋጋ ፡ ሁለት ፡ ፍራንክ ፡ ተኩል ፡ ነው ፤ አ ንዳንድ ፡ ሰው ፡ ከሁለት ፡ ወረቀት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሚችለው ፡ ይገዛል ። በዚህም ፡ በተሰበሰበው ፡ ገንዘብ ፡ አሻንጉሊትና ፡ ሌላም ፡ ትንንሽ ፡ ዕቃ ፡

ከመርከቡ ፡ ኩምፓንያ ፡ ተገዝቶ ፡ ባንድ ፡ ክፍል ፡ ቤት ፡ ተቆልሎ ፡ ነበር ።

ለዚሁም ፡ ጨዋታ ፡ አንድ ፡ ፕሬዚዳን ፤ አንድ ፡ ዋይስ ፡ ፕሬዚዳን ፤ አንድ ፡ ዋና ፡ ጸሐፊ ፡ ሾመው ፡ ነበርና ፡ እኔ ፡ ጨዋታውን ፡ የማላውቀው ፡ ስለ ፡ ሆንሁ ፡ ጨዋታውንም ፡ ባታውቅ ፡ የክብር ፡ ፕሬዚዳን ፡ ሁንልን ፡ ስላሉኝ ፡ እሺ ፡ ብዬ ፡ የክብር ፡ ፕሬዚዳንነት ፡ ተሾምሁ ። ሁለተኛውም ፡ ፕሬዚዳን ፡ የቢልጊክ ፡ የውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስትር ፡ አማካሪ ፡ ሙሴ ፡ ዥራር ፡ የሚባለው ፡ ሆነ ። የጨዋታውም ፡ ዓይነት ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ነበር ።

ስለ ፡ ሆነም ፡ ዋና ፡ ዋናውን ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ጽፌዋለሁ ።

፩ኛ ። ወፍራም ፡ ገመድ ፡ ይዘረጋና ፡ በመካከሉ ፡ ወሰን ፡ ተደርጎ ፡ ፭ ሰዎች ፡ አንዱን ፡ ጫፍ ፤ ደግሞ ፡ ፭ ሰዎች ፡ አንዱን ፡ ጫፍ ፡ ይዘው ፡ ይጓተታሉ ። ያንደኛው ፡ ወገን ፡ ደግሞ ፡ እግሩ ፡ ከወሰኑ ፡ ያለፈ ፡ እንደ ሆነ ፡ ተሸነፈ ፡ ተብሎ ፡ ይሳቅበታል ። ላንደኛው ፡ ወገን ፡ ይጨበጨብለታል ።

፪ኛ ። ፭ ሴቶች ፡ ባንድ ፡ ወገን ፡ ክብሪት ፡ እየያዙ ፡ ይቆማሉ ። ደግሞ ፡ ፭ ወንዶች ፡ ባፋቸው ፡ ሲጃራ ፡ እየያዙ ፡ ባንድ ፡ ወገን ፡ በሩቅ ፡ ይቆማሉ ። የጨዋታው ፡ ሹም ፡ ፩ ፡ ፪ ፡ ፫ ፡ ሲላቸው ፡ ወንዶቹ ፡ ሲጃራቸውን ፡ ባፋቸው ፡ እንዳደረጉ ፡ እየሮጡ ፡ ሔደው ፡ ወደ ፡ ሴቶቹ ፡ ሲቀርቡ ፡ ሴቶቹ ፡ በፍጥነት ፡ ክብሪት ፡ እየጫሩ ፡ ያቀርቡላቸዋል ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ወይ ፡ ያንዲቱ ፡ ክብሪት ፡ ስትጭረው ፡ ይጠፋል ፤ ወይም ፡ ወንዱ ፡ ስጃራውን ፡ በቶሎ ፡ ወደ ፡ ክብሪቱ ፡ ማስጠጋትና ፡ እሳቱን ፡ ማያያዝ ፡ ያቅተውና ፡ ሌላው ፡ ሰው ፡ በቶሎ ፡ ስጃራውን ፡ አጢሶ ፡ ተመልሶ ፡ የሮጠና ፡ የቀደመ ፡ እንደ ሆነ ፡ ይጨበጨብለታል ።

፫ኛ ። ፭ ሴቶች ፡ ባንድ ፡ ወገን ፡ በሩቅ ፡ ሆነው ፡ የሰዳ ፡ ጠርሙስ ፡ እየያዙ ፡ ይቆማሉ ፤ ደግሞ ፡ ፭ ፡ ወንዶች ፡ ቡብርጭቆ ፡ ውስኪ ፡ እየያዙ ፡ ይቆማሉ ። የጨዋታው ፡ ሹም ፡ ፩ ፡ ፪ ፡ ፫ ፡ ባላቸው ፡ ጊዜ ፡ ወንዶቹ ፡ እየሮጡ ፡ ሔደው ፡ የውስኪ ፡ ብርጭቋቸውን ፡ ለሴቶቹ ፡ ሲያቀርቡ ፡ ሴቶቹ ፡ ሰዳ ፡ ይቀዱላቸዋል ። በፍጥነት ፡ ሰዳው ፡ ተቀድቶለት ፡ ውስኪውን ፡ ጠጥቶ ፡ በመጀመሪያ ፡ ተመልሶ ፡ የሮጠና ፡ የቀደመ ፡ ይጨበጨብለታል ።

፬ኛ ። ፭ ፡ ሰዎች ፡ እግራቸውን ፡ በጆንያ ፡ ውስጥ ፡ እያገቡ ፡ በትክክል ፡ ይቆማሉ ። የጨዋታው ፡ ሹም ፡ ፩ ፡ ፪ ፡ ፫ ፡ ሲልላቸው ፡ ሩጫ ፡ ጀምረው ፡ አንደኛው ፡ የቀደመ ፡ እንደሆነ ፡ ይጨበጨብለታል ።

፭ኛ ። አምስት ፡ አምስት ፡ ሜትር ፡ የሚሆን ፡ እንደ ፡ ጥብጣብ ፡ በጠባቡ ፡ ሆኖ ፡ የተሠራና ፡ በያይነቱ ፡ ቀለም ፡ የገባ ፡ ስስ ፡ ልብስ ፡ በሞላላ ፡

እንጨት ፡ ላይ ፡ ባንዳንድ ፡ ክንድ፡እርቀት ፡ ይታሠርና ፡ ለ፭ሴቶች ፡ ትንን ሽ ፡ መቀስ ፡ ይሰጧቸዋል ። የጨዋታው ፡ ሹም ፡ ፩ ፡ ፪ ፡ ፫ ፡ ሲላቸው ፡ መቅደድ ፡ ይጀምሩና ፡ መጀመሪያ ፡ ቀዳ ፡ ለጨረሰችው ፡ ይጨበጨብላታል ።

፰ኛ ። ፭ ፡ እንቁላል ፡ ባምስት ፡ ስፍራ ፡ ላይ ፡ ተደርድሮ ፡ ለአምስት ፡ ሴቶች ፡ ትንንሽ ፡ ማንካ ፡ እየሰጡ ፡ በተራ ፡ ያቆሙና ፡ የጨዋታው ፡ ሹም ፡ ፩ ፡ ፪ ፡ ፫ ፡ ሲላቸው ፡ በእጅዋ ፡ ሳትነካ ፡ በማንካዋ ፡ ብቻ ፡ እንቁላሉን ፡ አንሥታ ፡ መጀመሪያ ፡ ቀድማ ፡ የሮጠች ፡ እንደሆነ ፡ ይጨበጨብላታል ።

፱ኛ ። ሁለት ፡ ሜትር ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ እርዝመቱ ፡ ፫ሜትር ፡ የሚሆን ፡ ሳንቃ ፡ ከወደ ፡ ኋላው ፡ ሁለት ፡ ሜትር ፡ ያህል ፡ ከፍ ፡ አድ ርገው ፡ ከወደ ፡ ፊቱ ፡ ዘቅዘቅ ፡ አድርገው ፡ በላዩ ፡ መንኰራኵር ፡ ያላት ፡ መ ቀመጫ ፡ አብጅተው ፡ አንዱን ፡ ሰው ፡ በዚያ ፡ አስቀምጠው ፡ መንኰ ራኵሩ ፡ እንዳይሽከረከር ፡ በእጃቸው ፡ ደግፈው ፡ ይይዙታል ።

በሳንቃው ፡ አጋማሽ ፡ ላይ ፡ በትይዩ ፡ ወሀ ፡ በባልዲ ፡ ሞልተው ፡ በ ሚወዘወዝ ፡ ገመድ ፡ ላይ ፡ ሰቅለው ፡ ያቆዩታል ። ባልዲው ፡ በስተ ፡ ስሩ ፡ የወሀ ፡ ቧምቧ ፡ ያህል ፡ ቀዳዳ ፡ አድርገውለት ፡ በመንኰራኵሩ ፡ የተቀመ ጠው ፡ ሰው ፡ የጦር ፡ ሶማያ ፡ የሚመስል ፡ እንጨት ፡ ይዞ ፡ ይጠብቃልና ፡ የጨዋታው ፡ ሹም ፡ ፩ ፡ ፪ ፡ ፫ ፡ ሲለው ፡ የተቀመጠበትን ፡ መንኰራኵር ፡ ይለቁለታል ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ሶማያውን ፡ በባልዲው ፡ ቀዳዳ ፡ ያገባ ፡ እንደ ሆነ ፡ ውሀው ፡ ሳይፈስበት ፡ ያልፋል ። ቀዳዳውን ፡ ስቶ ፡ ሌላ ፡ ስፍራ ፡ የወጋ ፡ እንደሆነ ፡ ግን ፡ ውሀው ፡ በላዩ ፡ ይፈስበታልና ፡ ይሳቅበታል ።

በዚሁም ፡ ትልልቆች ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ በተጫወቱበት ፡ አይነት ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆችም ፡ እንደዚሁ ፡ ይጫወታሉ ።

በጨዋታውም ፡ መጀመሪያ ፡ የቀደመ ። ሁለተኛ ፡ የቀደመ ። ሶስተኛ ፡ የቀደመ ፡ ስሙ ፡ እየተጻፈ ፡ ይቀመጣል ።

በጥቅምት ፡ ፮ ቀን ፡ ወደ ፡ ማታ ፡ በ፲ ሰዓት ፡ በትልቁ ፡ የመርከብ ፡ አዳራሽ ፡ መርከበኞቹ ፡ ሁሉ ፡ ተሰብስበው ፡ በጨዋታው ፡ ለቀደሙት ፡ ሕፃ ናት ፡ ሁሉ ፡ አሻንጉሊቱ ፡ በጨዋታው ፡ ፕሬዚዳን ፡ በእኔ ፡ እጅ ፡ ታደለ ።

በማግሥቱም ፡ እንደዚሁ ፡ በ፲ ሰዓት ፡ ተሰብስበን ፡ በጨዋታው ፡ ለ ቀደሙት ፡ ለትልልቁ ፡ ሰዎች ፡ ትንንሽ ፡ ዕቃ ፡ ታደለ ።

በማናቸውም ፡ ቢሆን ፡ ይኸን ፡ የመሰለው ፡ ጨዋታ ፡ ሁሉ ፡ በመር ከብ ፡ ላይ ፡ መደረጉ ፡ በመርከብ ፡ ላይ ፡ ሌላ ፡ ሥራ ፡ ስለሌለ ፡ በሳቅና ፡ በ ጨዋታ ፡ ለጊዜና ፡ ለቀን ፡ ማሳለፊያ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሌላ ፡ ጥቅም ፡ ነገር ፡ የለበትም ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በጥቅምት ፡ ፯ቀን ፡ ጧት ፡ በ፲፪ሰዓት ፡ ሲንጋፑር ፡ ከተማ ፡ ደረስን ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

ጧት ፡ በ፲፪ ፡ ሰዓት ፡ መርከባችን ፡ በሲንጋፑር ፡ ዳር ፡ በቆመ ፡ ጊዜ ፡ የጃፓን ፡ ቆንስል ፡ መጥቶ ፡ ተገናኘን ። ወደ ፡ መርከብም ፡ ወጥቶ ፡ እንዲጠይቀን ፡ ከመንግሥቱ ፡ መታዘዙን ፡ አስታወቀን ።

ቀጥሎም ፡ የሲንጋፑር ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ ዋና ፡ ጸሐፊ ፡ መጥቶ ፡ አገረ ፡ ገዥው ፡ ሰላምታቸውን ፡ እንድነግርላቸው ፡ ወዲያውም ፡ ምሳ ፡ መጋበዛቸውን ፡ እንዳስታውቅዎ ፡ አዘውኛል ፡ ብሎ ፡ ነገረን ።

ቀጥሎም ፡ የፈረንሳዊ ፡ ቆንስል ፡ መጥቶ ፡ ከተገናኘን ፡ በኋላ ፡ በአውቶሞቢል ፡ ይዞን ፡ ወጥቶ ፡ የሲንጋፑርን ፡ ከተማና ፡ ዋናውን ፡ የቡዳሃን ፡ መቅደስ ፡ አሳየን ።

በ፮ ፡ ሰዓት ፡ ወደ ፡ አገረ ፡ ገዥው ፡ ቤት ፡ ሔደን ፡ ምሳ ፡ ተጋበዝን ። ከምሳም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሺን ፡ ከተማ ፡ ወደ ፡ ሻንጋሂ ፡ ለመግባት ፡ ሲንጋፑር ፡ ያለው ፡ የሺን ፡ ቆንስል ፡ በይለፍ ፡ ወረቀቱ ፡ ላይ ፡ ካልፈረመበት ፡ አይቻልም ፡ ስላሉን ፡ የይለፍ ፡ ወረቀታችንን ፡ አስፈርመን ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ተመለስን ።

ወደ ፡ ማታ ፡ በ፲፩ ፡ ሰዓት ፡ መርከባችን ፡ ወደ ፡ ሳይጎን ፡ ጉዞ ፡ ጀመረ ።

በጥቅምት ፡ ፱ ፡ ቀን ፡ በ፮ ፡ ሰዓት ፡ ኬፕ ፡ ደ ፡ ዣክ ፡ (የያዕቆብ ፡ የወደብ ፡ መሬት ፡)ከሚባለው ፡ ከኮሺንሺን ፡ አገር ፡ ዳር ፡ ደረስን ። ኮሺንሺን ፡ የፈረንሳዊ ፡ መንግሥት ፡ የቅኝ ፡ አገር ፡ ነው ። በኬፕ ፡ ደ ፡ ዣክም ፡ መርከባችን ፡ ፬ ፡ ሰዓት ፡ ቆመ ። ምክንያቱንም ፡ ብንጠይቅ ፡ ከዚህ ፡ ስፍራ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዋናው ፡ ከተማ ፡ እስከ ፡ ሳይጎን ፡ መርከቡ ፡ የሚሔደው ፡ ሚኮንግ ፡ በሚባለው ፡ በትልቁ ፡ ወንዝ ፡ ላይ ፡ ስለሆነ ፡ የወንዙ ፡ ጥልቀት ፡ ሁለት ፡ መርከቦች ፡ ጐን ፡ ለጐን ፡ አያስተላልፍምና ፡ ከሳይጎን ፡ የተነሡት ፡ መርከቦች ፡ እስቲያልፉ ፡ ድረስ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ማታ ፡ በ፲ ፡ ሰዓት ፡ መርከባችን ፡ መጓዝ ፡ ጀመረና ፡ ከማታው ፡ በ፪ ፡ ሰዓት ፡ ሳይጎን ፡ ከተማ ፡ ደረስን ።

በሳይጎንም ፡ የፈረንሳዊ ፡ የቅኝ ፡ አገር ፡ ሚኒስትር ፡ ሙሴ ፡ ፖል ፡ ሬኖ ፡ መጥቶ ፡ ሰንብቶ ፡ በጧት ፡ ወደ ፡ ሒንዶ ፡ ሺን ፡ ለመሔድ ፡ ሲነሣ ፡ በአንድሬ ፡ ሊቦን ፡ መርከብ ፡ መምጣትዎን ፡ ዛሬ ፡ ማለዳ ፡ ሰማሁ ። እኔም ፡ ፕሮግራሙ ፡ ሁሉ ፡ እንዳይፋለስብኝ ፡ ብዬ ፡ ሳላይዎ ፡ ወደ ፡ ሒንዶ ፡ ሺን ፡ በመሔዴ ፡ አዝኛለሁ ፡ ብሎ ፡ አንድ ፡ መላክተኛ ፡ ላከ

ብኝ ። የኮሸንሸንም ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ እንኳን ፡ ደህና ፡ መጡ ፡ የሚል ፡ መላ ክተኛ ፡ ልኮ ፡ ወዲያውም ፡ በማግሥቱ ፡ ምሳ ፡ እንድንጋበዝለት ፡ የጥሪ ፡ ወረቀት ፡ ጻፈልን ።

በሳይጎንም ፡ ያለው ፡ የጃፓን ፡ ቆንስል ፡ መጥቶ ፡ በአውቶሞቢል ፡ እያዞረ ፡ የሳይጎንን ፡ ከተማና ፡ የአንቲካውን ፡ ቤት ፡ የለማዶች ፡ አራዊ ቱን ፡ ስፍራ ፡ ሲያሳየን ፡ ውሎ ፡ ማታ ፡ በቆንስላው ፡ ቤት ፡ ራት ፡ ጋበዘን ።

በጥቅምት ፡ ፲፫ ፡ ቀን ፡ ከሌሊቱ ፡ በ፲ ሰዓት ፡ መርከባችን ፡ ወደ ፡ ሆንግኮንግ ፡ ጉዞ ፡ ጀመረና ፡ በዚያው ፡ በመጣንበት ፡ ወንዝ ፡ ተመል ሰን ፡ በኬፕ ፡ ዳ ፡ ዣክ ፡ አድርገን ፡ ወደ ፡ ትልቁ ፡ ባሕር ፡ ደረስን ።

በጥቅምት ፡ ፲፯ ቀን ፡ ወደ ፡ ማታ ፡ በ፲፩ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ሆንግ ኮንግ፡ወደ፡ሚባለው፡የእንግሊዝ ፡ የቅኝ ፡ አገር ፡ ከተማ ፡ ደረስን ። በሆ ንግኮንግ ፡ ብዙ ፡ መርከቦች ፡ ቆመው ፡ ነበር ። ከነዚሁም ፡ ትልልቁ ፡ ጃፓኖቹ ናቸው ። ከሁሉም ፡ የሚበልጠውና ፡ የሚያምረው ፡ መለሎ ፡ የሚባለ ው ፡ የአሜሪካን ፡ መርከብ ፡ ነው ። ይህንም ፡ መርከብ ፡ ማየቱ ፡ እጅ ግ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ከኮማንዳው ፡ ፈቃድ ፡ ተቀብለን ፡ ለማየት ፡ ገባን ።

ከዚህም ፡ ቀድሞ ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ትልቅና ፡ የሚያምር ፡ መርከ ብ ፡ በማንም ፡ አገር ፡ አላየሁም ። መርከብ ፡ ነው ፡ በማለት ፡ ፋንታ ፡ አንድ ፡ ቤት ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ለመናገር ፡ ይቻላል ።

በዚህም ፡ መርከብ ፡ ውስጥ ፡ ያየነው ፡ እጅግ ፡ የሚያስደንቀው ፡ ሁ ለት ፡ ዓይነት ፡ አዲስ ፡ የጥበብ ፡ ሥራ ፡ ነው ። ፩ኛው ፡ ዓይነት ፡ ማን ም ፡ ሠራተኛ ፡ ሳይነካው ፡ የሚሔድበትን ፡ አገር ፡ ብቻ ፡ አመልክቶ ፡ መርከቡ ፡ በኦቶማቲክ ፡(በገዛ ፡ ራሱ ፡)እየተጓዘ ፡ ለመድረስ ፡ ከታሰበት ፡ አ ገር ፡ ደርሶ ፡ መገኘቱ ፡ ነው ።

ምሳሌ ። ከአዲስ ፡ አበባ ፡ ወደ ፡ ትግሬ ፡ አውራጃ ፡ ወደ ፡ አደዋ ፡ ለመሔድ ፡ ያሰበ ፡ ሰው ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ላይ ፡ መኪናውን ፡ ዘውሮ ፡ ቢተወው ፡ መኪናው ፡ በገዛ ፡ ራሱ ፡ መንገዱን ፡ እየፈለገ ፡ ይደርሳል ፡ ማለት ፡ ነው ።

፪ኛው ፡ ዓይነት ፤ መርከቡ ፡ ባንድ ፡ ምክንያት ፡ ተበላሽቶ ፡ ውሀ ፡ የገባበት ፡ እንደሆነ ፡ ውሀው ፡ መግባቱን ፡ የሚያመለክት ፡ የኤሌክት ሪክ ፡ ኃይል ፡ ሠርተው ፡ ምልክቱን ፡ ተጠባባቂ ፡ ሰው ፡ በየተራ ፡ ያስ

ቀምጣሉ ። ውሀው ፡ መግባቱ ፡ እርግጥ ፡ ሲሆን ፡ አንድ ፡ ጠብታ ፡ ውሀ ፡ እንኳ ፡ የማያስገባ ፡ የብረት ፡ ሣንቃ ፡ ያለው ፡ አምስት ፡ ክፍል ፡ ቤት ፡ አለና ፡ መንገደኛውን ፡ ሁሉ ፡ ወደዚያ ፡ አስገብተው ፡ ይዘጉበትና ፡ የመርከቡን ፡ መበላሸት ፡ በራዲዮ ፡ ያስታውቃሉ ። በዚያም ፡ መርከቡና ፡ መንገደኞቹ ፡ ምንም ፡ አደጋ ፡ ሳያገኛቸው ፡ አንድ ፡ ወርም ፡ ቢሆን ፡ ባንድ ፡ ሥፍራ ፡ ቆይተው ፡ ሌላ ፡ መርከብ ፡ ይደርስላቸውና ፡ በደህና ፡ ይዛወራሉ ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

በማግሥቱም ፡ የጃፓን ፡ ቆንስል ፡ መጥቶ ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ ስለሚደረግላችሁ ፡ አቀባበል ፡ ከመንግሥቴ ፡ የመጣልኝን ፡ ፕሮግራም ፡ እንድሰጣችሁ ፡ ታዝዣለሁ ፡ ብሎ ፡ ከአስረከበን ፡ በኋላ ፡ የሆንግኮንግን ፡ ከተማ ፡ ለማሳየት ፡ በአውቶሞቢል ፡ ይዞን ፡ ሔደ ።

ሆንግኮንግ ፡ በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ በካንቶን ፡ ወንዝ ፡ መውጫ ፡ የተሠራች ፡ ደሴት ፡ መሳይ ፡ ከተማ ፡ ናት ። የሺን ፡ አገር ፡ ዓሣ ፡ አጥማጆች ፡ ሰፈር ፡ ነበረች ። በኋላ ፡ ግን ፡ በ፲፰፻፴፫ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡ እንግሊዞች ፡ ከሺኖች ፡ ላይ ፡ በውል ፡ ወስደው ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ለሚተላለፈው ፡ የንግድ ፡ መርከብና ፡ የጦር ፡ መርከብ ፡ መቋሚያ ፡ አድርገዋታል ። ስፍራውም፡ዙሪያውን ፡ ተራራማ ፡ ስለሆነ ፡ ለምሽግ ፡ የተመቸ ፡ በመሆኑ ፡ ብዙ ፡ ካዘርን ፡ (የወታደር ፡ መኖሪያ ፡ ቤት ፡) ሠርተው ፡ ብዙ ፡ ወታደሮች ፡ አኑረውበታል ።

እኛም ፡ በተራራው ፡ ዙሪያ ፡ በተሠራው ፡ መንገድ ፡ በአውቶሞቢል ፡ እየተዛወርን ፡ የወታደሩን ፡ ካዘርን፡ለመናፈሻም ፡ የተሠራውን ፡ ጥሩ ፡ ጥሩ ፡ ቤትና ፡ ሆቴል ፡ አይተን ፡ በ፯ ፡ ሰዓት ፡ ከአገረ ፡ ገዥው ፡ ቤት ፡ ምሳችንን ፡ ተጋብዘን ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ተመለስን ።

በጥቅምት ፡ ፲፯ ፡ ቀን ፡ ከሌሊቱ ፡ በ፲ሰዓት ፡ መርከባችን ፡ ወደ ፡ ሸንጋሂ ፡ ጉዞ ፡ ጀመረና ፡ በጥቅምት ፡ ፳ቀን ፡ በ፯ ሰዓት ፡ ሸንጋሂ ፡ ከተማ ፡ ደረስን ።

---

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

የሸንጋሂ ፡ ከተማ ፡ ከተመሠረተ ፡ ፬ሺ፰፻፶፫ ፡ ዓመት ፡ ይሆናል ። የተመሠረተውም ፡ ዋንግፑ ፡ በሚባል ፡ መርከብ ፡ በሚያስሔድ ፡ በትልቅ ፡ ወንዝ ፡ ዳር ፡ በስተ ፡ ግራ ፡ በኩል ፡ ነው ። የፊተኛ ፡ ስሙ ፡ ሁነበር ፡ ይባል ፡ ነበር ። በኋላ ፡ ግን ፡ በ፲፱፻፳ ዓ ፡ ም ፡ ሸንጋሂ ፡ ተባለ ። ት

ርጓሚውም ፡ ላይኛ ፡ ባሕር ፡ ማለት ፡ ነው ። እንደ ፡ ሥፍራው ፡ አኳ ኋን ፡ እያዩ ፡ ዝቅ ፡ ያለውን ፡ ታችኛ ፡ ባሕር ፤ ከፍ ፡ ያለውን ፡ ላይኛ ፡ ባሕር ፡ ይሉታል ። በሀገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ በንዳንድ ፡ አገር ፡ ላይ ፡ አምባ ፤ ታች ፡ አምባ ፡ እንደሚባለው ፡ ነው ።

እስከ ፡ ፲፰፻፴፪ ፡ ዓ ፡ ም ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰው ፡ አይኖርበትም ፡ ነበር ። በኋላ ፡ ግን ፡ የምሥራቅ ፡ ህንድ ፡ ኩምፓኒያ ፡ የሚባለው ፡ የእ ንግሊዝ ፡ የንግድ ፡ ማኅበር ፡ የንግድ ፡ መርከብ ፡ ይዞ ፡ ቢሔድ ፡ ሺኖች ፡ አናስገባም ፡ ስላሉት ፤ የእንግሊዝ ፡ መንግሥት ፡ የጦር ፡ መርከብ ፡ ልኮ ፡ በጦርነት ፡ ከያዘው ፡ በኋላ ፡ የንግድ ፡ ውል ፡ ተዋውሎ ፡ ለቀቀላቸው ።

ቀጥሎም ፡ የአሜሪካ ፡ ዩናይትድ ፡ እስቴት ፡ መላክተኛ ፡ ልኮ ፡ የ ንግድ ፡ ውል ፡ ተዋዋላቸው ። ቀጥሎም ፡ የፈረንሳዊ ፡ ሬፑብሊክ ፡ መን ግሥት ፡ መላክተኛ ፡ ልኮ ፡ የንግድ ፡ ውል ፡ ተዋዋላቸው ። በዚህም ፡ ምክንያት ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ እየበዙ ፡ ስለ ፡ ሔዱ ፡ በተለየ ፡ ባ ንድ ፡ ወገን ፡ በታ ፡ ተቀብለው ፡ ሰፈራቸውን ፡ ለይተው ፡ የሚኖሩ ፡ ሆነዋል ።

ሻንጋሂ ፡ ለምሥራቅ ፡ አገሮች ፡ ሁሉ ፡ ዋና ፡ በርና ፡ መገናኛ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ከተማው ፡ እየሰፋ ፤ ንግዱ ፡ እየበዛ ፡ ሔድዋል ። ነገር ፡ ግን ፡ የሺን ፡ መንግሥት ፡ ሕዝብ ፡ ያልተማሩና ፡ ያልሠለጠኑ ፡ በመሆናቸው ፡ በውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ በየጊዜው ፡ አደጋ ፡ እየጣሉ ፤ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡ እየተዋጉ ፡ ስለ ፡ አስቸገሩ ፡ ትልቆች ፡ መንግሥቶች ፡ ሁሉ ፡ በሻንጋሂ ፡ የሚኖሩትን ፡ ቆንስሎቻቸውንና ፡ ሕዝባቸውን ፡ ለመጠበቅ ፡ ሲሉ ፡ ብዙ ፡ የጦር ፡ መርከብ ፡ በሻንጋሂ ፡ ባሕር ፡ ላይ ፡ ያስቀምጡ ፡ ጀመር ።

እኛም ፡ ወደ ፡ ሻንጋሂ ፡ በገባንበት ፡ ቀን ፡ የእንግሊዝም ፡ የአሜሪ ካም ፡ የኢጣልያም ፤ የጃፓንም ፡ የሌሎችም ፡ መንግሥቶች ፡ ትልቁም ፡ ትንሹም ፡ ባንድነት ፡ ፳ ፡ ያህል ፡ የጦር ፡ መርከቦች ፡ አይተናል ።

በዚህም ፡ ሁሉ ፡ ምክንያት ፡ የሻንጋሂ ፡ ከተማ ፡ ምንም ፡ ስሙ ፡ የሺን ፡ ቢሆን ፡ ኢንተርናሺዮናል ፡ አድርገውታል ። ኢንተርናሺዮናል ፡ ማለት ፡ በሺን ፡ መንግሥት ፡ ሕግ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ የዓለም ፡ መንግሥቶች ፡ ሁሉ ፡ ተስማምተው ፡ ባቆሙት ፡ ሕግ ፡ የሚገዛ ፡ አገር ፡ ማለት ፡ ነው ።

አሁን ፡ በሻንጋሂ ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ቍጥራቸው ፡ ፩ሚሊዮን ፡ ፪ ፩ሺ ፡ ፱፻፫ ፡ ነው ። ከዚሁም ፡ ፵፰ሺ ፡ ፰፻፺ቱ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ናቸው ። በሻንጋሂ ፡ ከሁሉም ፡ ይልቅ ፡ ሰፊ ፡ በታ ፡ የያዙ ፡ ፈረንሳ ዎች ፡ ናቸው ።

እስከ ፡ ፲፱፻፳፫ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡ በሻንጋሂ ፡ የሚኖሩ ፡ ሺኖች ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ የተካሰሱ ፡ እንደሆነ ፡ በሺን ፡ ዳኛ ፡ ላይ ፡ ይነጋገሩ ፡ ነበር ። አንድ ፡ ሺናዊና ፡ አንድ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰው ፡ የተካሰሱ ፡ እን ደሆነ ፡ ግን ፡ በውጭ ፡ አገር ፡ ቆንስል ፡ ላይ ፡ ይነጋገሩ ፡ ነበር ። አሁን ፡ ግን ፡ የሺን ፡ መንግሥት ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ ስለ ፡ ተቃወመ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰው ፡ ከሳሽም ፡ ተከሳሽም ፡ ቢሆን ፡ በሺን ፡ ዳኛ ፡ ላይ ፡ እየተነጋገረ ፡ ከሳሽ ፡ ሲሆን ፡ እንደ ፡ ሺን ፡ መንግሥት ፡ ሕግ ፤ ተከሳሽ ፡ ሲሆን ፡ እን ደ ፡ መንግሥቱ ፡ ሕግ ፡ እንዲፈረድ ፡ ስምምነት ፡ ተደርጓል ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

መርከባችንም ፡ በቆመ ፡ ጊዜ ፡ የእንግሊዝና የጃፖን ፡ ቆንስ ል ፡ ጄነራሎች ፡ መጥተው ፡ ከተገናኘን ፡ በኋላ ፡ የእንግሊዝ ፡ ቆንስል ፡ ጄኔራል ፡ ለምሳ ፤ የጃፖን ፡ ቆንስል ፡ ጄኔራል ፡ ለራት ፤ ግብዣ ፡ ፈቃድ ፡ ጠየቁንና ፡ ፈቃዳችን ፡ መሆኑን ፡ ለሁለቱም ፡ አስታወቅናቸው ።

ቀጥሎም ፡ የፈረንሳዊ ፡ ቆንስል ፡ ጄኔራል ፡ መጥቶ ፡ እኛ ፡ ለራት ፡ ስለ ፡ ተቀመጥን ፡ ካርታውን ፡ ለመርከቡ ፡ ሹም ፡ ሰጥቶ ፡ ተመለሰ ።

በጥቅምት ፡ ፳፩ቀን ፡ ከጧቱ ፡ በ፬ሰዓት ፡ የጃፖን ፡ ቆንስል ፡ የሻ ንጋሂን ፡ ከተማ ፡ በሙሉ ፡ እያዞረ ፡ አሳየን ። በ፮ሰዓት ፡ ወደ ፡ እንግ ሊዝ ፡ መንግሥት ፡ ቆንስል ፡ ጄኔራል ፡ ሔደን ፡ ምሳ ፡ ተጋበዝን ። ከ ማታውም ፡ በ፱ሰዓት ፡ ወደ ፡ ጃፖን ፡ ቆንስል ፡ ጄኔራል ፡ ቤት ፡ ሔደ ን ፡ ራት ፡ ተጋበዝን ። በማግሥቱም ፡ ከቀኑ ፡ በ፳ሰዓት ፡ መርከባችን ፡ ጉዞ ፡ ጀመረና ፡ በጥቅምት ፡ ፳፫ቀን ፡ የሺን ፡ ባሕር ፡ የሚባለውን ፡ ጨ ርሰን ፡ ፔሲፊክ ፡ ወደሚባለው ፡ ውቅያኖስ ፡ ደረስን ። በቀኝና ፡ በግራ ም ፡ ትንንሽ ፡ የጃፖን ፡ ደሴቶች ፡ መታየት ፡ ጀመሩ ። ወዲያውም ፡ የ መርከቡ ፡ ኮማንዳ ፡(አለቃ)ወደ ፡ እኛ ፡ መጥቶ ፡ የጃፖን ፡ መንግሥት ፡ በሌላ ፡ በትንሽ ፡ መርከብ ፡ ተቀባይ ፡ ልኮላችኋልና ፡ ነገ ፡ ከ፮ ሰዓት ፡ በፊት ፡ ይደርሳል ። ወደዚህም ፡ መርከብ ፡ በመሰላል ፡ ገብቶ ፡ ይገና ኛችኋል ። እርሱም ፡ እዚሁ ፡ አድሮ ፡ ነገ ፡ ጧት ፡ ከናንተ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ኮቤ ፡ ይሔዳል ። ይህም ፡ ቃል ፡ የመጣልኝ ፡ በቴሌግራም ፡ ነውና ፡ ነገሩ ን ፡ እንድታውቁት ፡ ብዬ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ነገረን ። በማግሥቱም ፡ በ፬ሰዓ ት ፡ ተኩል ፡ ሙሴ ፡ ኩሮኪ ፡ የሚባለው ፡ ካንድ ፡ ደሴት ፡ በጢስ ፡ በ ሚሔድ ፡ ጃልባ ፡ መጥቶ ፡ መሰላል ፡ ተዘረጋለትና ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ገብ ቶ ፡ ከተገናኘን ፡ በኋላ ፡ በጃፖን ፡ አገር ፡ የሚደረግልንን ፡ አቀባበል ፡ የሚያስታውቅ ፡ ፕሮግራም ፡ ሰጠን ።



ክቡር ፡ ብላቴን ፡ ጌታ ፡ ኅሩይ ፡ በጃፓን ፡ የባሕር ፡ ወደብ ፡
ከተማ ፡ በኮቤ ፡ ደርሰው ፡ ከመርከብ ፡ ሲወርዱ ።

ሙሴ ፡ ኵሮኪም ፡ ለዚህ ፡ ጉዳይ ፡ የተመረጠበት ፡ ምክንያቱ ፡ ከዚህ ፡ ቀድሞ ፡ ከጃፓን ፡ መንግሥት ፡ እየተላከ ፡ ሶስት ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ መጥቶ ፡ ነበርና ፡ ልማዳቸውን ፡ ያውቀዋል ፡ ተብሎ ፡ እኛን ፡ ደስ ፡ ለማሰኘት ፡ ነው ።

ሙሴ ፡ ኵሮኪም ፡ በመርከቡ ፡ ላይ ፡ አንድ ፡ ክፍል ፡ ቤት ፡ ተቀብሎ ፡ እስተ ፡ ኮቤ ፡ ከእኛው ፡ ጋራ ፡ ተጓዘ ።

በጥቅምት ፡ ፳፫ ፡ ቀን ፡ መርከባችን ፡ ከጃፓን ፡ የወደብ ፡ ከተማ ፡ ኮቤ ፡ ከሚባለው ፡ ለመድረስ ፡ ሁለት ፡ ሰዓት ፡ ሲቀረው ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ሊጋባ ፡ ባልደረቦች ፡ ሙሴ ፡ ማኮቶ ፡ ዋታናቤና ፡ ባሮን ፡ ሮኩሮ ፡ ናቢሺማ ፡ እኛን ፡ ለመቀበል ፡ ስለ ፡ ታዘዙ ፡ በትንሽ ፡ የጢስ ፡ ጀልባ ፡ መጥተው ፡ መሰላል ፡ እየተዘረጋላቸው ፡ ገብተው ፡ በመርከቡ ፡ አዳራሽ ፡ ላይ ፡ ተገናኘን ። ሁለት ፡ ሰዓትም ፡ ባንድነት ፡ ከተጓዝን ፡ በኋላ ፡ ኮቤ ፡ ከሚባለው ፡ የወደብ ፡ ከተማ ፡ በደረስን፡ ጊዜ ፡ መልሕቁ ፡ ተጣለና ፡ መርከቡ ፡ ቆመ ።

---

## ሁለተኛ ፡ ትልቅ ፡ ክፍል ።

### ከኮቤ ፡ እስከ ፡ ዋናው ፡ ከተማ ፡ እስከ ፡ ቶኪዮና ፡ በቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ ስለ ፡ ሆነው ፡ ነገር ።

የኮቤ ፡ ከተማ ፡ አቀባበል ። የኮቤ ፡ ተራሮች ። ወደ ፡ ቶኪዮ ፡ መሔድ ። በባቡር ፡ መቋሚያ ፡ አቀባበል ። ወደ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት፡መሔድ ።የንጉሠ ፡ነገሥታችንን፡ ደብዳቤ፡ለጃፓን፡ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ማስረከብ ።የምሳ ፡ ግብዣ ።ቢዚት ፡ መመለስ።የንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂን ፡ ሽራይንና ፡ የቡዳሃን ፡ መቅደስ ፡ ማየት ።

---

### ምዕራፍ ፡ ፯ ።

በኮቤ ፡ ከተማ ፡ በባሕሩ ፡ ዳር ፡ ባለው ፡ በትልቁ ፡ በር ፡ ላይ ፡ በስተቀኝ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ባንዲራ ፤ በስተግራ ፡ የጃፓን ፡ ባንዲራ ፡ በሰፋፊው ፡ ሆኖ ፡ ተሰቅሎ ፡ ይታይ ፡ ነበር ።

በባንዲራው ፡ ቀኝ ፡ ፴፱ ፡ የሚሆኑ ፡ በወታደር ፡ ትምሕርት ፡ ቤት ፡ የሚማሩ ፡ ጎበዛዝት ፡ በቀኝ ፡ እጃቸው ፡ የኢትዮጵያን ፤ በግራ ፡ እጃቸው ፡ የጃፓንን ፤ ትንንሽ ፡ ባንዲራዎች ፡ እየያዙ ፡ ተሰልፈው ፡

ቆመው ፡ ነበር ። በስተግራም ፡ የከተማው ፡ ሰው ፡ ወንዱም ፡ ሴቱም፡ ሕፃናቱም ፡ ተሰብስበው ፡ ቆመው ፡ ነበር ።

በመርከቡም ፡ ወለል ፡ ላይ ፡ ቆመን ፡ ባዩን ፡ ጊዜ ፡ ሁሉም ፡ ባንዲራቸውን ፡ እያወዛወዙ ፡ የደስታ ፡ ድምጣቸውን ፡ እያሰሙ ፡ ሰላምታ ፡ ሰጡን ።

እኛም ፡ በመርከቡ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ቆምን ፡ ባርኔጣችንን ፡ እያወዛወዝን ፡ የደስታ ፡ ሰላምታ ፡ ሰጠናቸው ። ለጊዜውም ፡ ዝናም ፡ ይዘንም ፡ ነበርና ፡ ከመርከቡ ፡ በቶሎ ፡ አልወረድንም ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የኮቤ ፡ አውራጃ ፡ አገረ ፡ ገዥና ፡ የኮቤ ፡ ከተማ ፡ ከንቲባ ፡ የኮቤ ፡ ጉምሩክ ፡ ሹም ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ገብተው ፡ ከተገናኘን ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ መሬት ፡ ስንወርድ ፡ እንደ ፡ ደንቡ ፡ የመርከቡ ፡ ኰማንዳ ፡ (አዛዥ ፡)እስከ ፡ መርከቡ ፡ በር ፡ ሸኝቶን ፡ ተመለሰ ።

እንደ ፡ ደንቡ ፡ ማለት ፡ መርከቡ ፡ የፈረንሳዊ ፡ ሰለ ፡ ሆነ ፡ ከመርከቡ ፡ እስትንወጣ ፡ ድረስ ፡ አዛዡና ፡ ባለ ፡ ሥልጣኑ ፡ ኰማንዳው ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ ማለት ፡ ነው ።

ከመርከቡ ፡ መሰላል ፡ ወርደን ፡ የጃፓንን ፡ መሬት ፡ ስንረግጥ ፡ በባሕሩ ፡ ዳር ፡ የተሰበሰው ፡ ሕዝብ ፡ እንደገና ፡ ባንዲራውን ፡ እያወዛወዘ ፡ በደስታ ፡ ይጮህ ፡ ጀመር ። እኛም ፡ በጣም ፡ ቀረብ ፡ ብለን ፡ የደስታ ፡ ሰላምታ ፡ ከሰጠናቸው ፡ በኋላ ፡ በሁለቱ ፡ መንግሥቶች ፡ ባንዲራዎች ፡ በተቀሰተው ፡ በዋናው ፡ በር ፡ አልፈን ፡ በወጣን ፡ ጊዜ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ የሚሆኑ ፡ በኮቤ ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ የሚማሩ ፡ ወንዶች ፡ ልጆች ፡ ባንድ ፡ ወገን ፤ ሴቶቹ ፡ ልጆች ፡ ባንድ ፡ ወገን ፡ ተሰልፈው ፡ በየእጃቸው ፡ ትንንሽ ፡ የኢትዮጵያና ፡ የጃፓን ፡ ባንዲራ ፡ ይዘው ፡ በደስታ ፡ እየጮሁ ፡ ሰላምታ ፡ ይሰጡ ፡ ጀመር ።

ከዚያም ፡ ጀምሮ ፡ ኦሪዬንታል ፡ ሆቴል ፡ እስከ ፡ ሚባለው ፡ ድረስ ፡ ለማየት ፡ በየመንገዱ ፡ ዳር ፡ የቆመው ፡ ሕዝብ ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ነበር ።

ከስድስት ፡ ሰዓት ፡ በኋላም ፡ በ፰ ፡ ሰዓት ፡ የኮቤን ፡ ተራሮች ፡ ለማየት ፡ ከሆቴል ፡ ተነሣን ። የኮቤ ፡ ተራሮች ፡ እጅግ ፡ የተዋቡ ፡ ሲዳር ፡ (ቄድሮስ)በሚባል ፡ በለመለመ ፡ ዛፍና ፡ በቀርከሃ ፡ ዛፍ ፡ ያጌጡ ፡ ናቸው ። ተራራውን ፡ ስንወጣ ፡ በተራራው ፡ መካከል ፡ ባለው ፡ መንደር ፡ የሚማሩ ፡ ብዙ ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ የኢትዮጵያን ፡ ባንዲራ ፡ እየያዙ ፡ በመንገድ ፡ ዳር ፡ ተሰልፈው ፡ ቆመው ፡ አገኘናቸው ። ደግሞ ፡ ወታደሮች ፡ ለይላማ ፡ ተኩስና ፡ ለሽርሽር ፡ መድፋቸውን ፡ ጠመንጃቸ

ውን ፡ መትረየሳቸውን ፡ እየጫኑ ፡ ሔደው ፣ ሲመለሱ ፡ በተራራው ፡ መንገድ ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ አገኘናቸው ፡ መንገዱ ፡ ለአውቶሞቢልና ፡ እየተጫነ ፡ ለሚጓዘው ፡ መድፍና ፡ መትረየስ ፡ መተላለፊያ ፡ የማይበቃ ፡ ሆኖ ፡ በብዙ ፡ ችግር ፡ በአውቶሞቢል ፡ ነጂዎች ፡ ጥንቃቄ ፡ አለፍን ። በተራራውም ፡ ጫፍ ፡ ስንደርስ ፡ ወደ ፡ አንድ ፡ ባላገር ፡ ቤት ፡ አግብተው ፡ አሳረፉን ፤ ለጊዜው ፡ ባለቤቱ ፡ አልነበረምና ፡ ልጁና ፡ ቤት ፡ ጠባቂዎቹ ፡ ብቻ ፡ ነበሩ ። የቤቱ ፡ ጥዳት ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ። ሴዳር ፡ የሚባለው ፡ እንጨት ፡ እንደ ፡ ሸራ ፡ እየሆነ ፡ በስሱ ፡ እየተሰነጠቀ ፡ ተሠርቷል፤ ከበረንዳውም፡ጀምሮ ፡ ቤቱ ፡ ሁሉ ፡ የተነጠፈው ፡ እንደ ፡ ክር ፡ የቀጠነ ፡ የሣር ፡ ኬሻ ፡ ነው ። እንደ ፡ ልማዳቸው ፡ በጃፓኖች ፡ ቤት ፡ ማንም ፡ ቢሆን ፡ ጫማውን ፡ ሳያወልቅ ፡ የሚገባ ፡ የለም ። ይኸውም ፡ ስለ ፡ ቤቱ ፡ ንጹሕነት ፡ እንዳያድፍ ፡ ተብሎ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሌላ ፡ ምክንያት ፡ የለበትም ። እኛም ፡ እንደ ፡ ልማዱ ፡ ጫማችንን ፡ እናወልቃለን ፡ ስንል ፡ የሩቅ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ናችሁና ፡ ሳታወልቁ ፡ ግቡ ፡ ብለው ፡ ለመኑን ። ስለሆነም ፡ ለበረንዳው ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ ውስጥ ፡ ለመግባት ፡ አይደለም ። ስንገባም ፡ ወንዶቹም ፡ ሴቶቹም ፡ በደጃፉ ፡ ላይ ፡ በጉልበታቸው ፡ ተንበርክከው ፡ ነበርና ፡ እግራችን ፡ ደጃፉን ፡ ሲረግጥ ፡ ሁሉም ፡ እንደ ፡ ልማዳቸው ፡ ግንባራቸውን ፡ ምድር ፡ እያስነኩ ፡ እጅ ፡ ነሡ ።

ከሁሉም ፡ ይልቅ ፣ በዚህ ፡ ቤት ፡ አጠገብ ፡ ያየነው ፡ ሞሚጂ ፡ (ሜፒል ፡)የሚባለው ፡ ዛፍ ፡ እጅግ ፡ ያስደንቃል ። ይህ ፡ ዛፍ ፡ ቅጠሉ ፡ ለመርገፍ ፡ አቅራቢያ ፡ ሲጠወልግ ፡ ቅላቱ ፡ የባሕር ፡ አረብ ፡ መስሎ ፡ ፲፰ ፡ ቀን ፡ ያህል ፡ ይቆያል ። እንደዚህም ፣ የሚሆንበት ፡ ከጥቅምት ፡ ወር ፡ እስከ ፡ ኅዳር ፡ ወር ፡ እኩሌታ ፡ ስለሆነ ፡ ጊዜ ፡ አጋጥሞን ፡ በማየታችን ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አለን ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ ይህ ፡ ዛፍ ፡ እንደ ፡ አንድ ፡ ትልቅ ፡ ብርቅ ፡ ነገር ፡ ይታያል ።

የኮቤን ፡ ተራሮች ፡ አይተን፡ ከተመለስን ፡ በኋላ ፡ ራታችንን ፡ በኦሪዬንታል ፡ ሆቴል ፡ ተጋብዘን ፡ ከማታው ፡ በ፫ሰዓት ፡ በልዩ ፡ ባቡር ፡ ወደ ፡ ዋናው ፡ ከተማ ፡ ወደ ፡ ቶኪዮ ፡ ተጓዝን ። የኮቤ ፡ ከንቲባና ፡ ያውራጃው ፡ ገዥ ፡ እስከ ፡ ባቡር ፡ መቋሚያ ፡ ሸኝተውን ፡ ተመለሱ ። አንድ ፡ ሰዓትም ፡ ያህል ፡ እንደ ፡ ተጓዝን ፡ በኦስካ ፡ ከተማ ፡ ስለ ፡ ደረስን ፡ የኦስካ ፡ አገረ ፡ ገዥና ፡ ከንቲባው ፡ ከብዙ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ የኢትዮጵ

ያን ፡ ባንዲራ ፡ እየያዙ ፡ ቆመው ፡ አገኘናቸው ። ባቡሩም ፡ የሚቆመው ፡ አስር ፡ ደቂቃ ፡ ብቻ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ከባቡር ፡ ሳንወርድ ፡ ሰላምታ ፡ ሰጥተን ፡ ተሰነባበትናቸው ፤ ሌሊቱንም ፡ ሁሉ ፡ ስንጓዝ ፡ አድረን ፡ በማግሥቱ ፡ ጧት ፡ በ፫ሰዓት ፡ በቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ ዳር ፡ ደረስን ።

ባቡራችንም ፡ ቶኪዮ ፡ ለመግባት ፡ አንድ ፡ ሰዓት ፡ ሲቀረው ፡ የማዕርግ ፤ ልብሳችንን ፡ እንድንለብስ ፡ ባልደረባችን ፡ ሙሴ ፡ ዋታናቤ ፡ ስለ ፡ አስታወቀን ፡ ለብሰን ፡ ተዘጋጅተን ፡ እንጠብቅ ፡ ነበርና ፡ በቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ ዳር ፡ ደርሰን ፡ ፴ ፡ ደቂቃ ፡ ያህል ፡ ከተጓዝን ፡ በኋላ ፡ ከባቡር ፡ መቆሚያው ፡ ደረስን ።

በባቡር ፡ መቋሚያም ፡ የውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስትር ፡ ክቡር ፡ ባሮን ፡ ሺዴሐራ ፤ የግቢ ፡ ሚኒስትር ፡ ክቡር ፡ ዶክቶር ፡ ኢኪ ። የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ሊጋባ ፡ ክቡር ፡ አድሚራል ፡ ሲዚኪ ፡ የቶኪዮ ፡ አውራጃ ፡ ገዥና ፡ የቶኪዮ ፡ ከንቲባ ፡ ከተከታዮቻቸው ፡ መኳንንቶች ፡ ጋራ ፡ የማዕርግ ፡ ልብሳቸውን ፡ እየለበሱ ፡ በባቡሩ ፡ በስተቀኝ ፡ ቆመው ፡ ነበር ። ከነርሱም ፡ ቀጥሎ ፡ የክብር ፡ ዘበኞች ፡ አለቃ ፡ የክብር ፡ ዘበኞቹን ፡ በተራ ፡ አሰልፎ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ። ቶኪዮም ፡ የገባነው ፡ በልዩ ፡ ባቡር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ለመቀበልና ፡ ለማየት ፡ ከተሰበሰበው ፡ ሰው ፡ በቀር ፡ በባቡሩ ፡ ውስጥ ፡ ሌላ ፡ መንገደኛ ፡ አልነበረምና ፡ ፍጹም ፡ ፀጥታ ፡ ሆኖ ፡ ነበር ። ጋዜጠኞችና ፡ ፎቶግራፍ ፡ አንሽዎች ፡ ብቻ ፡ የሚመቻቸውን ፡ ስፍራ ፡ ለመምረጥ ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ ይዛወሩ ፡ ነበር ።

ከባቡርም ፡ ስንወርድ ፡ የውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስትር ፡ ክቡር ፡ ባሮን ፡ ሺዴሐራ ፡ ቀርቦ ፡ ከተገናኘን ፡ በኋላ ፡ ሚኒስትሮችንና ፡ መኳንንቶቹን ፡ በየተራ ፡ እያቀረበ ፡ አስተዋወቀኝ ። እኔም ፡ ልጅ ፡ ተፈራ ፡ ገብረ ፡ ማርያምን ፡ አቅርቤ ፡ ከሁሉም ፡ ጋራ ፡ አስተዋወቅሁት ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ የክብር ፡ ዘበኞች ፡ አለቃ ፡ በጐራዴው ፡ ሰላምታ ፡ በሰጠ ፡ ጊዜ ፡ ሙዚቃና ፡ ጥሩምባ ፡ ይነፉ ፡ ጀመር ። እኔም ፡ በሰልፉ ፡ መካከል ፡ ሰላምታ ፡ እየሰጠሁ ፡ አለፍሁ ።

ከባቡሩ ፡ መቋሚያ ፡ እስከ ፡ አውቶሞቢሉ ፡ ስፍራ ፡ የመንገዱ ፡ ርዝመት ፡ ሶስት ፡ መቶ ፡ ሜትር ፡ ይሆናል ። በዚህም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ቀይ ፡ ግምጃ ፡ ተነጥፎ ፡ ነበርና ፡ ሊጋባው ፡ በፊት ፡ በፊታችን ፡ እየሔደ ፡ ወደ ፡ አውቶሞቢል ፡ ስፍራ ፡ አደረሰን ። ከዚያም ፡ ለማረፊያ ፡ ወደ ፡ ተዘጋጀልን ፡ ወደ ፡ ኢምፔርያል ፡ ሆቴል ፡ ወስደው ፡ አሳረፉን ።



ቶኪዮ፡ ደርሰን፡ በባቡር፡ መቋሚያ፡ የጃፓን፡ ሚኒስትሮች፡ ሲቀበሉን።

የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ እንግዶች ፡ ሆነን ፡ የገ
ባንበት ፡ ኢምፓርያል ፡ ሆቴል ፡ የሚባለው ።

በኢምፔርያል ፡ ሆቴልም ፡ ፳፰ ፡ ደቂቃ ፡ ያህል ፡ ካረፍን ፡ በኋላ ፡ በቀይ ፡ ከፈይና፡በወርቅ ፡ ያጌጡ ፡ እጅግ ፡ ያማሩ ፡ ሁሉት ፡ ሠረገሎች፡ከን ጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ መጡልን ። ነጅዎቹም ፡ ቀይ ፡ በለዲ፡ የለበሱ ፤ ረጅም ፡ ጥቁር ፡ ባርኔጣ ፡ ያደረጉ ፡ ነበሩ ። በመጀመሪያው ፡ ሠ ረገላ ፡ እኔና ፡ባልደረባችን፡ ማስተር ፡ አፍ ፡ ሲርሞኒ፡የሚባለው፡ሙሴ ፡ ዋ ታናቢ ፡ ተቀመጥን ። በሁለተኛውም ፡ ሠረገላ ፡ ልጅ ፡ ተፈራ ፡ ጉብረ ፡ ማ ርያምና ፡ ሁለተኛው፡ማስተር ፡ አፍ ፡ ሲርሞኒ ፡ ባሮን ፡ናቢሺማ ፡ ተቀመጡ ።

የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ የክብር ፡ ዘበኞች ፡ በፈረስ ፡ እየተቀመጡ ፡ በሠረ ገላው ፡ ፊትና ፡ ኋላ ፡ ባንዲራ ፡ እየያዙ ፡ ሶምሶማ ፡ ይጋልቡ ፡ ነበር ። በሠ ረገላውም ፡ ቀኝና ፡ ግራ ፡ የማዕርግ ፡ ልብስ ፡ የለበሱ ፡ ዘበኞች ፡ የሠረገ ላውን ፡ አካሔድ ፡ እየጠበቁ ፡ በሞተር ፡ ቢስኪሊት ፡ ይሔዱ ፡ ነበር ።

ከኢምፔርያል ፡ ሆቴል ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ድረስ ፡ ባለው ፡ መንገድ ፡ እግረኛም ፤ አውቶሞቢልም ፤ ትራ ምይም ፤ ሠረገላችንን፡ አቋርጦ ፡ እንዳይሔድ ፡ በዘበኛ ፡ እየተከለከለ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ።

በየቤቱ ፡ ደርብና ፡ በየመንገዱም፡ዳር ፡ ቆመው ፡ የሚያዩት ፡ የከተ ማው ፡ ሕዝብ ፡ ቊጥራቸው ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ ነበር ፡ ለማለት ፡ እጅግ ፡ ይቸግራል ።

ይህንም ፡ በመሰለ ፡ ደስታና ፡ ክብር ፡ ከቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ቅጥር ፡ ውጭ ፡ ያለውን ፡ሰፊውን፡አደባባይ ፡ ካለፍን ፡ በኋላ ፡ ሁለት ፡ ድልድይ ፡ ከሚባለው ፡ በር ፡ ደረስን ። ሁለት ፡ ድልድይ ፡ የተባለበትን ፡ ምክንያት ፡ በኋላ ፡ እንጽፈዋለን ። ሁለቱንም ፡ ድልድይ ፡ አልፈን ፡ ከውስጠኛው ፡ ቅጥር ፡ ውጭ ፡ ስንደርስ ፡ ሌሎች ፡ የክብር ፡ ዘበኞችና ፡ ሙዚቃ ፡ ነፊ ዎች ፡ ተሰልፈው ፡ ይጠብቁ ፡ ነበርና ፡ የክብር ፡ ዘበኞች ፡ አለቃ ፡ በጐራ ዴው ፡ ሰላምታ ፡ በሰጠ ፡ ጊዜ ፡ ሙዚቃው ፡ ይነፋ ፡ ጀመር ። ሁለተኛው ንም ፡ ቅጥር ፡ ስንገባ ፡ የማዕርግ ፡ ልብስ ፡ የለበሱ ፡ ሁለት ፡ ፈረሰኞች ፡ በመንገዱ ፡ ቀኝና ፡ ግራ ፡ ቆመው ፡ ነበርና ፡ ሠረገላችን ፡ በመካከላቸው ፡ አልፎ፡ ከቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ በር ፡ ደረሰና ፡ ከሠረገላ ፡ ስንወርድ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ሊጋባ ፡ ተቀበለን ። ከበሩ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ማረፊያው ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ለውስጥ ፡ መንገዱ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሜትር ፡ ይሆናል ። በየመተ ላለፊያውም ፡ ላይ ፡ የማዕርግ ፡ ልብስ ፡ የለበሱ ፡ አራት ፡ አራት ፡ መኳን ንቶች ፡ እየቆሙ ፡ ሰላምታ ፡ ይሰጡ ፡ ነበር ።

በማረፊያውም ፡ ቤት ፡ በደረስን ፡ ጊዜ ፡ የውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስትርና ፡ የግቢ ፡ ሚኒስትር ፤ ሌሎችም ፡ መኳንንቶች ፡ ተቀብለው ፡ አሳረፉን ። ሶስት ፡ ደቂቃ ፡ ያህል ፡ እንደ ፡ ቆየን ፡ የውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስትሩና ፡ የግቢው ፡ ሚኒስትር ፡ ሌሎችም ፡ መኳንንቶች ፡ ከጠገባችን ፡ እየተጠሩ ፡ ሔዱ ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ሊጋባ ፡ መጥቶ ፡ በፊት ፡ በፊታችን ፡ እየሔደ ፤ ባልደረቦቻችን ፡ በኋላ ፡ በኋላ ፡ እየተከተሉ ፡ ወደ ፡ እንግዳ ፡ መቀበያው ፡ ቤት ፡ ወሰዱን ።

ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ በወርቅ ፡ ያጌጠ ፡ የጦር ፡ አለቆች ፡ ልብስ ፡ ለብሰው ፡ ትልቁን ፡ የጃፓንን ፡ ኒሻን ፡ ባለወርቅ ፡ ሰንሰለቱን ፡ በንገታቸው ፡ አጥልቀው ፡ ፕላኩንም ፡ በደረታቸው ፡ አድርገው ፡ ነበር ። የውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስትር ፡ በስተቀኝ ፤ የግቢ ፡ ሚኒስትር ፡ በስተግራ ፡ ሶስት ፡ ሶስት ፡ ሜትር ፡ እየራቁ ፡ የቀሩትም ፡ መኳንንቶች ፡ እንደ ፡ ማዕርጋቸው ፡ በጣም ፡ እየራቁ ፡ ቆመው ፡ ነበር ። ንጉሠ ፡ ነገሥቱም ፡ በወለሉ ፡ ላይ ፡ ቆመው ፡ ነበርና ፡ ከበሩ ፡ ላይ ፡ ስደርስ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ባንገት ፡ እጅ ፡ ነሣሁ ። ቀጥሎም ፡ ከአዳራሹ ፡ መካከል ፡ ስደርስ ፡ ሁለተኛ ፡ ባንገት ፡ እጅ ፡ ነሣሁ ። ቀጥሎም ፡ እስከ ፡ ሶስት ፡ ሜትር ፡ ቀርቤ ፡ በጣም ፡ አጎንብሼ ፡ እጅ ፡ ነሣሁ ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ከኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የተላክሁ ፡ አምባሳደር ፡ (ልዩ ፡ መላክተኛ) ፡ መሆኔን ፡ ለማስረዳት ፡ እንደ ፡ ደንቡ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ያለውን ፡ ቃል ፡ ማንበብ ፡ ጀመርሁ ።

ግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሆይ ።

ጥንታዊው ፡ የንግሥተ ፡ ሳባ ፡ ዘር ፡ ወደ ፡ ጥንታዊው ፡ የጂሙ ፡ ዘር ፡ መልክተኛ ፡ የላከው ፡ ዛሬ ፡ መጀመሪያ ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፎ ፡ ይቆያልና ፡ በዚህ ፡ በትልቁ ፡ የታሪክ ፡ ጊዜ ፡ በደስታ ፡ የማቀርበውን ፡ መልእክት ፡ እጅግ ፡ ከፍ ፡ ያለና ፡ የተለየ ፡ ክብር ፡ አድርጌ ፡ እቆጥረዋለሁ ።

እነዚህም ፡ ሁለቱ ፡ ጥንታውያን ፡ መንግሥቶች ፡ በግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥትነትዎና ፡ በታላቁ ፡ ገዥዬ ፡ በኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መሪነት ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ በደስታ ፡ የመቀራረብና ፡ ያንድነት ፡ እድል ፡ በማግኘታቸው ፤ ሌሎችም ፡ ጥንታውያን ፡ የነበሩ ፡ ነገሥታት ፡ የቀድሞ ፡ ዘራቸው ፡ እየተለወጠ ፡ አዲስ ፡ የተተኩ ፡ ትውልድ ፡ ሆነው ፡ ሳሉ ፡ እነዚህ ፡ ሁለቱ ፡ ነገሥታት ፡ ብቻ ፡ ዘራቸው ፡ ሳያቋርጥ ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ ተያይዞ ፡ የመጣ ፡ በመሆናቸው ፡ በእውነት ፡ ሊመኩ ፡ ይገባቸዋል ።




ግርማዊ ፡ ሒሮሂቶ ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ።

ደግሞ ፡ የትምሕርትና ፡ የጉልበት ፡ ኃይል ፡ የጥበብና ፡ የሥራም ፡ ፖለቲካ ፡ የቀደሙት ፡ አባቶችዎ ፡ አደላድለው ፡ ያቆዩትን ፡ የጃፓንን ፡ መንግሥት ፡ በዓለም ፡ ጉዳይ ፡ ላይ ፡ ሁሉ ፡ አሁን ፡ ወደ ፡ አለበት ፡ ደረ ጃ ፡ ስለ ፡ አደረሰው ፡ ለጃፓን ፡ ሕዝብ ፡ እንኳን ፡ ደስ ፡ አላችሁ ፡ መ ባልና ፡ መመስገን ፡ ይገባቸዋል ።

ታላቁ ፡ ገዥዬ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ካለፈው ፡ ሥልሳ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ የተደረገውንና ፡ የተመሰገነውን ፡ የጃፓንን ፡ ታሪክ ፡ ልብ ፡ አድርገው ፡ ስለ ፡ አነበቡት ፡ ይህን ፡ ባጭር ፡ ዘመን ፡ ድንቅ ፡ ሆኖ ፡ የተከናወነውን ፡ መልካም ፡ አካሔድና ፡ ምሳሌ ፡ ራሳቸውና ፡ ሕ ዝባቸው ፡ ሊከተሉት ፡ የሚገባ ፡ መሆኑን ፡ ተመልክተውታል ።

ባለፈውም ፡ ዓመት ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ዘውድ ፡ በሚጭኑበት ፡ ጊዜ ፡ የዘውድ ፡ በዓላቸውን ፡ ለማክበርና ፡ እንኳን ፡ ደስ ፡ አለዎ ፡ ለማ ለት ፡ ግርማዊነትዎ ፡ ልዩ ፡ አምባሳደሩን ፡ በደስታ ፡ ልከ ፡ ነበር ። ግር ማዊ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥትም ፡ ከፍ ፡ ያለው ፡ አሳባቸው ፡ የ ሁለቱ ፡ መንግሥቶች ፡ መቀራረቢያ ፡ በዚህ ፡ በተቀባበልነው ፡ ቃል ፡ ብቻ ፡ ተወስኖ ፡ እንዲቀር ፡ አይደለምና ፡ ከልብ ፡ የሆነ ፡ ምስጋናቸው ንና ፡ ወዲያውም ፡ ግርማዊነታቸውና ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ለ ታላቁ ፡ ሰውነትዎና ፡ ለሕዝብዎ ፡ ሁሉ ፡ የሚመኙትን ፡ መልካም ፡ ም ኞት ፡ ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ አሳባቸውንም ፡ ለግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥትነትዎ ፡ እንድገልጽ ፡ አዘውኛል ።

## ግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሆይ ።

እኔም ፡ ራሴ ፡ በኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ስም ፡ ሆኜ ፡ መጥቼ ፡ ለፀሐይ ፡ መውጫ ፡ መንግሥት ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ በዋና ፡ ከተማቸው ፡ ሰላምታ ፡ ለማቅረብ ፡ መጀመሪያ ፡ ልዩ ፡ መላክተኛ ፡ መሆኔ ፡ በዘመኔ ፡ ሁሉ ፡ ትልቅና ፡ መልካም ፡ መታሰቢያ ፡ ሆኖልኝ ፡ የሚኖር ፡ ደስታና ፡ ክብሬ ፡ ነው ።

ደግሞ ፡ ለግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥትና ፡ ለቤተ ፡ ዘመዶችዎ ፡ ደህ ንነት ፡ ከልብ ፡ የሆነ ፡ ጥልቅ ፡ ምኞቴን ፡ ለማቅረብ ፡ ይህን ፡ ትልቅ ፡ እድል ፡ በማግኘቴ ፡ ከሁሉ ፡ የበለጠ ፡ ታላቅ ፡ ደስታ ፡ ይሰማኛል ።

በኢትዮጵያና ፡ በጃፓን ፡ ሕዝብ ፡ መካከል ፡ ባንድነት ፡ አሳብና ፡ በ ደስታ ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖረው ፡ ወዳጅነት ፡ በጽኑ ፡ መሠረት ፡ ላይ ፡ ተመ

ሥርቶ ፡ እያደገ ፡ በመሔዱ ፡ ምክንያት ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሏልና ፡ ወደ ፡ ፊትም ፡ እንደዚሁ ፡ እውነተኛው ፡ የወዳጅነት ፡ መተሣሠሪያ ፡ እየጠበቀ፡ ሔዶ ፡ ለዘላለም ፡ ጸንቶ ፡ እንዲኖር ፡ ዋና ፡ ምኞቴ ፡ ነው ።

ከፍ ፡ ያሉት ፡ ገዥዬ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የወዳጅነት ፡ ደብዳቤያቸውን ፡ እንዳቀርብ ፡ ባዘዙኝ ፡ ጊዜ ፡ ሹዋ ፡ የሚባለው ፡ ዘመን ፡ መንግሥትዎ ፡ ሳያቋርጥ ፡ ለረጅም ፡ ጊዜያት ፡ እንዲኖርና ፡ ለጃፓን ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ደህንነትና ፡ ልማት ፡ እንዲሆን ፡ በብርቱ ፡ የሚያስቡትን ፡ ከልብ ፡ የሆነ ፡ ጥልቅ ፡ ምኞታቸውን ፡ ለግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥትነትዎ ፡ በቃሌም ፡ እንድገልጽ ፡ አዘውኛል ፡ ብዬ ፡ ጨረስሁ ።

ይህንም ፡ ቃል ፡ አንብቤ ፡ ስጨርስ ፡ ግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሆይ እጅግ ፡ ከፍ ፡ ካሉት ፡ ገዥዬ ፡ ከኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የተላከልዎትን ፡ ደብዳቤ ፡ ለማቅረብ ፡ ፈቃድዎን ፡ እለምናለሁ ፡ ብዬ ፡ ጠይቄ ፡ አቀረብሁላቸውና ፡ ተቀብለው ፡ ለውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስትር ፡ ሰጡት ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መላክተኛነቴንና ፡ ደብዳቤውን ፡ መቀበላቸውን ፡ ለማስረዳት ፡ እንደ ፡ ደንቡ ፡ ከዚህ ፡ የሚከተለውን ፡ ቃል ፡ በጃፓን ፡ ቋንቋ ፡ ተናገሩ ።

ከግርማዊ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ልዩ ፡ አምባሳደር ፡ (መላክተኛ ፡)ሆነው ፡ መጥተው ፡ ወደዚህ ፡ በመድረስዎና ፡ ከታላቁ ፡ ገዥዎ ፡ ዘንድ፡ በእጅ፡ የተጻፈ፡ ደብዳቤ፡ከእጆችዎ፡በመቀበሌ፡በልዩ፡ደስ ፡ ብሎኛል ።

የግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥትን ፡ የዘውድ ፡ በዓል ፡ ለማክበር ፡ እንደራሴዬን ፡ መላኬ ፡ በልቤ ፡ ውስጥ ፡ እየታደሰ ፡ እስካሁንም ፡ ደስ ፡ ይለኛል ። ግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥትም ፡ መልካም ፡ ፈቃዳቸው ፡ ሆኖ ፡ በዚያ ፡ በታላቁ ፡ በዓል ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ ላደረግሁት ፡ ውለታ ፡ ለመመለስና ፡ ምስጋናቸውን ፡ ለመግለጽ ፡ ስለ ፡ ወደዱ ፡ እርስዎን ፡ የታመኑ ፡ ልዩ ፡ መላክተኛ ፡ አድርገው ፡ በመላካቸው ፡ እንደ፡ ገና፡ ታላቅ፡ደስታ ፡ ተሰማኝ ።

እርስዎ ፡ ራስዎ ፡ አሁን ፡ እንደ ፡ ተናገሩት ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ ሳያቋርጥ ፡ እንደ ፡ ሰንሰለት ፡ ተያይዞ ፡ በመጣው ፡ በነገሥታት ፡ ትውልዳችንና ፡ በገዥና ፡ በተገዥ ፡ ዜጎቻችን ፡ መካከል ፡ ስላለው ፡ ስምምነትና ፡ አንድነት ፡ ሁለቱም ፡ መንግሥቶች ፡ ሊመኩ ፡ ይችላሉና ፡ በንድነት ፡ ደስ ፡ ይለናል ።

እንደዚሁም ፡ ደግሞ ፡ የሁለቱም ፡ አገሮች ፡ ሕዝብ ፡ የወዳጅነት ፡ መገናኛቸው ፡ ከቅርብ ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ ፡ እየተቃረበ ፡ መሔዱ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡




ግርማዊት ፡ እቴጌ ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ባለቤት ።

የሚያሰኝ ፡ ነገር ፡ ሆኗልና ፡ በስምምነትና ፡ በመተማመን ፡ ከልብ ፡ የሆነው ፡ ያንድነት ፡ ሥራችን ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ እየበረታ ፡ የወዳጅነት ፡ መገናኛችንን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እያደረገ ፡ ለሕዝባችን ፡ ልማትና ፡ ደህንነት ፡ እንዲሆን ፡ እመኛለሁ ።

ጌታው ፡ አምባሳደር ፡ ሆይ ። በግርማዊ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ስም ፡ ሆነው ፡ ስለ ፡ ገለጹልኝ ፡ መልካም ፡ አሳብ ፡ ሁሉ ፡ ለታላቁ ፡ ገዥዎ ፡ ከልብ ፡ የሆነ ፡ ምስጋናዬን ፡ እንዲያደርሱልኝ ፡ እለምንዎታለሁ ።

እኔም ፡ በዚሁ ፡ ምክንያት ፡ ለግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ደስታና ፡ ላገራቸው ፡ ልማትና ፡ እድገት ፡ የምመኘውን ፡ መልካም ፡ ምኞቴን ፡ አቀርባለሁ ።

እርስዎም ፡ ራስዎ ፡ በዚህ ፡ አገር ፡ በሚሰነብቱበት ፡ ጊዜ ፡ ሁሉ ፡ በማናቸውም ፡ ነገር ፡ ደስ ፡ እንዲልዎ ፡ ተስፋ ፡ አደርጋለሁ ፡ ብለው ፡ ጨረሱ ።

ቃሉንም ፡ ተናግረው ፡ ሲጨርሱ ፡ ወደ ፡ ግርማዊነታቸው ፡ ቀርቤ ፡ እጅ ፡ ከነሣሁ ፡ በኋላ ፡ እጃቸውን ፡ ሰጥተው ፡ ከበሬታ ፡ አደረጉልኝ ።

ከዚህም ፡ ቀጥዬ ፡ እጅግ ፡ ከፍ ፡ ያሉት ፡ ገዥዬ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የሰሎሞን ፡ ኒሻን ፡ የሚባለውን ፡ ከፍተኛውን ፡ ማዕርግ ፡ ለግርማዊነትዎ ፡ እንዳቀርብ ፡ አዘውኛልና ፡ ለማቅረብ ፡ ፈቃድዎን ፡ እለምናለሁ ፡ ብዬ ፡ ከጠየቅሁ ፡ በኋላ ፡ የኒሻኑን ፡ ሣጥን ፡ ከፍቼ ፡ አቀረብሁላቸውና ፡ ተቀብለው ፡ ለግቢው ፡ ሚኒስትር ፡ ሰጡት ። ወዲያውም ፡ ሁለተኛ ፡ መላክተኛ ፡ ሆኖ ፡ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ የመጣውን ፡ ልጅ ፡ ተፈራ ፡ ገብረ ፡ ማርያምን ፡ ለማስተዋወቅ ፡ ፈቃድ ፡ ጠይቄ ፡ አስተዋወቅሁት ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ግርማዊ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ደህና ፡ ናቸው ፡ ወይ ። አንተስ ፡ ከመንገዱ ፡ በደህና ፡ ገባህወይ ፡ እያሉ ፡ አምስት ፡ ደቂቃ ፡ ያህል ፡ ካነጋገሩኝ ፡ በኋላ ፡ ተሰናብቼ ፡ ስወጣ ፡ ሊጋባው ፡ ወደ ፡ ማረፊያው ፡ ቤት ፡ መልሶ ፡ ወሰደኝ ። በዚያም ፡ ሶስት ፡ ደቂቃ ፡ ያህል ፡ እንደ ፡ ቆየሁ ፡ የግርማዊት ፡ እቴጌ ፡ የእልፍኝ ፡ አስከልካይ ፡ መጥቶ ፡ ወደ እንግዳ ፡ መቀበያቸው ፡ ቤት ፡ ወሰደኝ ።

እቴጌይቱ ፡ በፍጹም ፡ እንደ ፡ አዲሱ ፡ ዘመን ፡ የተሰፋ ፡ ከነጭነት ፡ ጥቂት ፡ ወደ ፡ ብጫነት ፡ የተለወጠ ፡ ረጅም ፡ ቀሚስ ፡ ለብሰው ፡ ነበር ። በስተ ፡ ቀኝ ፡ ሁለት ፡ ወይዛዝር ፤ በስተ ፡ ግራ ፡ ሁለት ፡ ወይዛዝር ፡ ቆመው ፡ ግርማዊነታቸው ፡ በወለሉ ፡ መካከል ፡ ቆመው ፡ ነበር ። ከነዚህም ፡ በቀር ፡

በእንግሊዝ ፡ ቋንቋ ፡ የምታስተረጕም ፡ አንዲት ፡ ወይዘሮ ፡ ባጠገባቸው ፡ ቆማ ፡ ነበረች ።

እኔም ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ እንዳደረግሁት ፡ ሶስት ፡ ጊዜ ፡ እጅ ፡ ነሥቼ ፡ በቀረብሁ ፡ ጊዜ ፡ እጃቸውን ፡ ሰጥተው ፡ ከበሬታ ፡ አደረጉልኝ ።

ቀጥዬም ፡ ግርማዊ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የላኩላቸውን፡ የንግሥተ ፡ ሳባን ፡ ኒሻን ፡ ለማቅረብ፡ ፈቃድ ፡ ጠይቄ ፡ አቀረብሁላቸውና፡ተቀብለው፡ ለክብር፡ እመቤቲቱ(ሌዲ ፡ አፍ ፡ አነር)ሰጧት ። ወዲያውም ፡ ልጅ ፡ ተፈራ ፡ ገብረ ፡ ማርያምን ፡ ለማስተዋወቅ ፡ ፈቃድ ፡ ጠይቄ ፡ አስተዋወቅሁት።

ከዚህም ፡ ቀጥሎ፡ የግርማዊ፡ የኢትዮጵያን፡ ንጉሠ፡ ነገሥትና ፡ የእቴጌይቱን ፡ ደህንነት ፡ እየጠየቁኝ ፡ ሶስት ፡ ደቂቃ ፡ ያህል ፡ ከቆየሁ ፡ በኋላ ፡ ስለ ፡ ኒሻኑ ፡ ደስታዬንና ፡ ምስጋናዬን ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ እንድትነግርልኝ ፡ ብለው ፡ አሰናበቱኝና ፡ ወጣሁ ።

ሊጋባውም ፡ በበሩ ፡ ላይ ፡ ቆሞ ፡ ይጠብቀኝ ፡ ነበርና ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ወደ ፡ ማረፊያው ፡ ቤት ፡ ወስዶ ፡ አሳረፈኝ ። ወዲያውም ፡ የኒሻኑ ፡ ሹም ፡ የፀሐይ ፡ መውጫ ፡ የሚባለውን ፡ ትልቁን ፡ ባለኮርዶን ፡ ኒሻን ፡ አምጥቶ ፡ ግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሸልመውሃል ፡ ብሎ፡ በትከሻዬ ፡ አነገተልኝ ። ለልጅ ፡ ተፈራም ፡ የዚህኑ ፡ ደረጃ ፡ ኒሻን ፡ ባለአምበሉን ፡ በደረቱ ፡ አደረገለት ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ከውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስትርና ፡ ከግቢ ፡ ሚኒስትር ፡ ተሰናብተን፡ ሊጋባው ፡ በፊት ፡ በፊታችን ፡ እየሔደ ፡ ከደጃፉ ፡ ስንደርስ ፡ ወደ ፡ ሠረገላ ፡ ገብተን ፡ እንደ ፡ ፊተኛው ፡ በክብር ፡ ዘበኞች ፡ ታጅበን፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ተመለስን ።

በዚሁም ፡ ቀን ፡ በንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ግቢ ፡ ምሳ ፡ ተጋብዘን ፡ ነበርና፡ የማዕርግ ፡ ልብሳችንን ፡ እያወለቅን ፡ ሞርኒንግ ፡ ኮት ፡ የሚባለውን ፡ ልብስ፡ እየለበስን ፡ በ፯ ሰዓት ፡ ተኩል፡እንደ፡ገና፡ ሔድን። በዚሁም፡ቀን፡ከእኛ፡ጋራ ፡ ለምሳ ፡ የተጋበዙት ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ቤተ ፡ ዘመዶችና ፡ የጃፓን ፡ መኳንንቶች ፡ ነበሩ ፡ እንጂ ፡ ሌላ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰው ፡ አንድም ፡ አልነበረም ። ቍጥራቸውም ፡ ፴፪ ፡ ነበር ።

ወይዛዝሩ ፡ የለበሱት ፡ እንደ ፡ ጥንቱ ፡ እንደ ፡ ጃፓን ፡ ወይዛዝር ፡ ነበር ። እቴጌይቱ ፡ ብቻ ፡ የአዲሱን ፡ ዘመን ፡ ልብስ ፡ ለብሰው ፡ ነበር ።

ንጉሠ ፡ ነገሥቱም ፡ በትከሻቸው ፡ ላይ ፡ ወርቅ ፡ ያለበት ፡ የጦር ፡ አለቆች ፡ ልብስ ፡ ለብሰው ፡ ከኢትዮጵያ ፡ የመጣላቸውን ፡ የሰሎሞንንና ፡

ያገራቸውን ፡ ኒሻን ፡ ፐላኩን ፡ ብቻ ፡ አድርገው ፡ ነበር ። ወንድማቸው ፡ ልዑል ፡ ታከማትዝም ፡ የጃፓንን ፡ ኒሻን ፡ ፐላኩን ፡ ብቻ ፡ አድርጎ ፡ ነበር ።

ከንጉሠ ፡ ነገሥቱና ፡ ከእቴጌይቱ ፡ በቀር ፡ ለምሳ ፡ የተጠራነው ፡ ሁላችንም ፡ አስቀድመን ፡ ወደ ፡ አዳራሹ ፡ ውስጥ ፡ ገብተን ፡ ቆይተን ፡ ነበርና ፤ ሊጋበው ፡ መጥቶ ፡ ግርማዊነታቸው ፡ የሚመጡበት ፡ ጊዜ ፡ መድረሱን ፡ አስታወቀን ።

ወዲያውም ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ፡ ቀደም ፡ ብለው ፡ እቴጌይቱ ፡ ተከትለው ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ ሁላችንም ፡ አንገታችንን ፡ እየደፋን ፡ እጅ ፡ ነሣን ።

በወለሉም ፡ ላይ ፡ ሁለት ፡ ደቂቃ ፡ ያህል ፡ እንደ ፡ ቆሙ ፡ አዛዡ ፡ ቀርበ ፡ ግብር ፡ ቀርቧል ፡ ብሎ ፡ ተናገረና ፡ ወደ ፡ ሙብል ፡ ቤት ፡ ገባን ።

የገበታው ፡ ስፋት ፡ ሁለት ፡ ሜትር ፡ ይሆናል ። በመካከሉም ፡ እጅግ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ የሆነ ፡ ሎቱስ ፡ የሚባለው ፡ የጃፓን ፡ አበባ ፡ አጠር ፡ ሰፋ ፡ ባለ ፡ በብር ፡ ዕቃ ፡ ሆኖ፡ በገበታው ፡ መካከል ፡ ተቀምጦ ፡ ይታይ፡ ነበር ። እኔም ፡ በኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት፡መላክተኛነቴ፡በእቴጌይቱ፡አጠገብ ፡ ተቀምጬ ፡ በጃፓን ፡ ቋንቋ ፡ ሲያነጋግሩኝ ፡ የውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስትር ፡ ባለቤት፡ባሮኒት፡ሺዲሐራ፡በእንግሊዝ፡ቋንቋ፡እየተረጐሙ፡ይነግሩኝ፡ነበር።

መጀመሪያ ፡ ጥያቄ። የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ለእኛ ፡ ንጉሠ፡ ነገሥት ፡ የላኳቸው ፡ አንበሶች ፡ ትልልቆች ፡ ናቸው ፡ ወይ ፡ አሉኝ ። ትልልቅ ፡ የሆኑ ፡ እንደሆነ ፡ አገር ፡ አይለምዱም ፡ ይባላልና ፡ አነስ ፡ አነስ ፡ ያሉ ፡ መጠነኖኞች ፡ ናቸው ፡ ብዬ ፡ መለስሁ ።

ሁለተኛ ፡ ጥያቄ ። ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ አንበሳ ፡ ይወዳሉ ፡ ወይ ፡ አሉኝ ።

አዎን ፡ ይወዳሉ ። በኢትዮጵያ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ በቅጥር ፡ ግቢ ፡ አንበሳ ፡ እንዲቀመጥ ፡ የነገሥታቱ ፡ ክብር ፡ ነው ፡ ብዬ ፡ መለስሁ ።

ሶስተኛ ፡ ጥያቄ ። እቴጌይቱ ፡ አንበሳ ፡ ያያሉ ፡ ወይ ፡ አሉኝ ። አንበሳው ፡ የሚኖረው ፡ በቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ቅጥር ፡ ግቢ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ሲወጡና ፡ ሲገቡ ፡ ያዩታል ፡ ብዬ ፡ መለስሁ ።

አራተኛ ፡ ጥያቄ ። በገበታው ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ ሎቱስ ፡ የሚባለውን ፡ አበባ ፡ እያሳዩ ፡ ባገራችሁ ፡ ይህን ፡ የሚመስል ፡ አበባ ፡ አለ ፡ ወይ ፡ አሉኝ ። ይህን ፡ የሚመስል ፡ የለም ። ነገር ፡ ግን ፡ ከዚህም ፡ የሚያማምሩ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ አበቦች ፡ ይገኛሉ ፡ ብዬ ፡ መለስሁ ።

አምስተኛ ፡ ጥያቄ ። ሞሚጂ (ሜፕል) የሚባል ፡ ዛፍ ፡ ባገራችሁ ፡ አለ ፡ ወይ ፡ አሉኝ ።

ምናልባት ፡ ባንዳንድ ፡ አውራጃ ፡ በየዱሩ ፡ ውስጥ ፡ ሳይገኝ ፡ አይቀ ርም ። በዋና ፡ ከተማችን ፡ በአዲስ ፡ አበባ ፡ ዙሪያ ፡ ግን ፡ የለም ። እኔ ም ፡ ኑሮዬ ፡ በከተማ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ይህ ፡ ዛፍ ፡ በያውራጃው ፡ መኖሩንና ፡ አለመኖሩን ፡ አስረግጨ ፡ ለመናገር ፡ አልችልም ፡ ብዬ ፡ መለስሁ ።

ይህም ፡ ሞሚጂ ፡ የሚባለው ፡ ዛፍ ፡ ውፍረትና ፡ ርዝመት ፡ የለ ውም ። ነገር ፡ ግን ፡ ቅርንጫፉ (ዓጽቁ)ወደ ፡ ላይም ፡ ወደ ፡ ቀኝም ፡ ወደ ፡ ግራም ፡ እየተዘረጋ ፡ ያድግና ፡ ቅጠሉ ፡ በሚረግፈበት ፡ ወራት ፡ የ ቅጠሉ ፡ መልክ ፡ እንደ ፡ ሌላው ፡ ዛፍ ፡ ቅጠል ፡ ወደ ፡ ብጫነት ፡ በመ ለወጥ ፡ ፋንታ ፡ የባሕር ፡ አረብ ፡ መስሎ ፡ ይታያል ። ስለዚህ ፡ ከጥቅምት፡ እኩሌታ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ኅዳር ፡ መጨረሻ ፡ የጃፓን ፡ አገር ፡ ዱሮች ሲታዩ ፡ የእሳት ፡ ነበልባል ፡ የሚነድባቸው ፡ መስለው ፡ ይታያሉ ።

እኛም ፡ መጀመሪያ ፡ የጃፓንን ፡ መሬት ፡ ስንረግጥ ፡ በኮቤ ፡ ተራ ራ ፡ ላይ ፡ ይህንኑ ፡ ዛፍ ፡ አይተን ፡ ማድነቃችንን፡ ለግርማዊነታቸው ፡ ብነግራቸው ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ አላቸው ።

ስድስተኛ ፡ ጥያቄ ። ልጆች ፡ አሉህ ፡ ወይ ፡ አሉኝ ። ግርማዊት ፡ ሆይ ። በእግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ ስድስት ፡ ልጆችና ፡ የልጅ ፡ ልጆችም ፡ አሉኝ ፡ ብዬ ፡ መለስሁ ። ይህንም ፡ ሁሉ ፡ ሲጠይቁኝ ፡ በዝግታና ፡ በለዘ ብታ ፡ ቃል ፡ በብሩህ ፡ ገጽ ፡ ነበር ።

አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ በቀኛቸው ፡ ወደ ፡ ተቀመጠው ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወንድም ፡ ወደ ፡ ልዑል ፡ ታካማትዝ ፡ ፊታቸውን ፡ እያዞሩ ፡ ይነጋገሩ ፡ ነ በር ። ንጉሠ ፡ ነገሥቱም ፡ ሌሎችም ፡ ሚኒስትሮችና ፡ መኳንንቶች ፤ ወይ ዛዝሮችም ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ በደስታ ፡ እየተነጋገሩ ፡ ይጫወቱ ፡ ነበር ። ደግሞ ፡ የመብሉ ፡ ሰሐን ፡ በተለወጠ ፡ ቍጥር ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ የሙዚቃ፡ ድምፅ ፡ ይሰማ ፡ ነበርና ፡ ደስታችን ፡ ከልክ ፡ ያለፈ ፡ ሆኖ ፡ ነበር ።

ይህንም ፡ በመሰለ ፡ ደስታ ፡ ምሳ ፡ ተበልቶ ፡ ሸምፓኝ ፡ ተጠጥቶ ፡ ሲጨረስ ፡ ከመብል ፡ ቤቱ ፡ ወጥተን ፡ ቡን ፡ ወደ ፡ ሚጠጣበት ፡ ወደ ፡ ሌላው ፡ አዳራሽ ፡ ገባን ።

ንጉሠ ፡ ነገሥቱም ፡ በወንበር ፡ ላይ ፡ በተቀመጡ ፡ ጊዜ ፡ ሊጋባው ፡ ጠርቶ ፡ ወስዶ ፡ በስተቀኛቸው ፡ ባለው ፡ ወንበር ፡ ላይ ፡ አስቀመጠኝ ።

እቴጌይቱም ፡ በንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ግራ ፡ ጥቂት ፡ እልፍ ፡ ብሎ ፡ በተዘ ረጋው ፡ ወንበር ፡ ላይ ፡ ተቀምጠው ፡ ነበርና ፡ የልዑል ፡ ታካማትዝ፡ ባለ ቤት ፡ ልዕልት ፡ ታካማትዝ ፡ ባጠገባቸው ፡ ተቀምጣ ፡ ነበር ። በንጉሠ ፡ ነ

ገሥቱ ፡ ግንባር ፡ ልውል ፡ ታካማትዝና ፡ ጠቅላይ ፡ ሚኒስትሩ ፡ ባሮን ፡ ዋካትሱኪ ፡ በወንበር ፡ ተቀምጠው ፡ ነበር። የቀሩት ፡ መኳንንቱና ፡ ወ ይዛዝሩ ፡ ግን ፡ አምስት ፡ ሜትር ፡ ያህል ፡ እርቀው ፡ ቆመው ፡ ቡን ፡ ይጠጡ ፡ ነበር ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ፊታቸውን ፡ ወደ፡ እኔ ፡ አዙረው ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ያሉትን ፡ ቃሎች ፡ ተናገሩ ።

መጀመሪያ ። ግርማዊ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ዘውድ ፡ በጫኑ ፡ ጊዜ ፡ በዓሉ ፡ እጅግ ፡ አምሮ ፡ ነበር ፡ ሲሉ ፡ ሰማሁ ፡ አሉኝ ።

አዎን ፡ እርግጥ ፡ ነው ። ይህን ፡ የመሰለ ፡ በዓልና ፡ ሥርዓት ፡ ን ግሥ ፡ በኢትዮጵያ ፡ ለእገሌ ፡ ንጉሥ ፡ ተደርጎለት ፡ ነበር ፡ ተብሎ ፡ በ ታሪክም ፡ ተጽፎ ፡ አላገኘንም ። መሳፍንቱና ፡ መኳንንቱ ፡ ሕዝቡም ፡ በዚሁ ፡ በጃንሆይ ፡ የዘውድ ፡ በዓል ፡ በጣም ፡ ተደንቀዋል ። ግርማዊ ነትዎ ፡ በሲኒማ ፡ ባያዩት ፡ ይሆናል ፡ እንጂ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝና ፡ የሚያ ስደንቅ ፡ ነው ፡ አልኋቸው ።

ሁለተኛ ። ግርማዊ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ አገራቸውን ፡ ወደ ፡ ትልቅ ፡ ደረጃ ፡ ለማድረስና ፡ ሕዝባቸውን ፡ ለማሰልጠን ፡ በብዙ ፡ ይደክማሉ ፡ ሲሉ ፡ ሰምቻለሁ ፡ አሉኝ ።

ግርማዊ ፡ ሆይ ፤ አዎን ፡ እርግጥ ፡ ነው ። ባገርም ፡ ውስጥ ፡ የትም ሕርት ፡ ቤትና ፡ ሆፒታል ፡ በማቆም ፤ ወደ ፡ ውጭ ፡ አገርም ፡ ልጆች ፡ እየሰደዱ ፡ በማስተማር ፤ የመንግሥቱም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ በደንብና ፡ በ ሕግ ፡ እንዲሆን ፡ ለማድረግ ፡ ከጧት ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ይሠራሉ ።

አሁን ፡ በቅርቡ ፡ ጊዜ ፡ በ፲፱፻፳፮ ዓ ፡ ም ፡ አውሮጳን ፡ ጎብኝተው ፡ ተመልሰው ፡ ነበርና ፡ በዚሁ ፡ በጭሩ ፡ ዘመን ፡ በዋናው ፡ ከተማ ፡ በ አዲስ ፡ አበባ ፡ ብዙ ፡ ነገር ፡ ተለውጦና ፡ ታድሶ ፡ ይታያል ፡ አልኋቸው ።

ሶስተኛ ። ከሁሉም ፡ የሚበልጥ ፡ ነገር ፡ ሕገ ፡ መንግሥት ፡ በፈቃዳቸ ው ፡ ማቆማቸውን ፡ የሚያስታውቅ ፡ ቴሌግራም ፡ በመጣልኝ ፡ ጊዜ ፡ በቅ ርቡ ፡ ጊዜ ፡ ይህን ፡ በማድረጋቸው ፡ በጣም ፡ አደነቅሁ ። ይህም ፡ የጀመሩ ት ፡ መልካም ፡ ሥራ ፡ እንዲቀናላቸው ፡ እመኝላቸዋለሁ ፡ አሉኝ ።

ግርማዊ ፡ ሆይ ፤ በዚህ ፡ ነገር ፡ ያልተደነቀ ፡ ሰው ፡ የለም ። በፈቃዳቸ ው ፡ ሕገ ፡ መንግሥት ፡ ያቆሙ ፡ የግርማዊነትዎ ፡ አያት ፡ ሚቺ ፡ ንጉሠ ነገሥት ፡ ሚጂ ፡ ብቻ ፡ መሆናቸውን ፡ እንሰማ ፡ ነበር ። አሁን ፡ ግን ፡ የኢ

ትዮጵያ ፣ ንጉሠ ፣ ነገሥት ፣ ቀዳማዊ ፣ ኃይለ ፣ ሥላሴ ፣ ለዚህ ፣ ነገር ፣ ሁለ ተኛ ፣ መሆናቸው ፣ ነው ። ይልቁንም ፣ ግርማዊነትዎ ፣ ሕገ ፣ መንግሥቱን ፣ ሲያነቡት ፣ ከጃፓን ፣ ሕገ ፣ መንግሥት ፣ ጋራ ፣ የተያያዘና ፣ የተመሳሰለ ፣ ሆኖ ፣ ሳያገኙት ፣ አይቀሩም ፣ አልኋቸው ።

አራተኛ ። በጃፓን ፣ አገር ፣ በምትሰነብትበት ፣ ጊዜ ፣ የምታያቸውን ፣ አገሮች ፣ ሹሞቹ ፣ ያስታውቁሃልና ፣ በምታየው ፣ ነገር ፣ ሁሉ ፣ ደስ ፣ ሳይ ልህ ፣ አይቀርም ። በማናቸውም ፣ ነገር ፣ ቢሆን ፣ የሁለቱ ፣ መንግሥቶ ች ፣ ሕዝቦች ፣ በጣም ፣ እንዲቃረቡ ፣ ፈቃዳችን ፣ ነው ፣ አሉኝ ።

ከዚህም ፣ በኋላ ፣ ልጅ ፣ አርአያ ፣ አበበ ፣ ምንም ፣ በኦፊሲል ፣ ባይ ሆን ፣ አገር ፣ ለማየት ፣ ከእኔ ፣ ጋራ ፣ ወደ ፣ ጃፓን ፣ መምጣቱንና ፣ የግ ርማዊ ፣ ንጉሠ ፣ ነገሥት ፣ ዘመድ ፣ መሆኑን ፣ አስታውቄ ፣ መጥቶ ፣ እጅ ፣ እንዲነሣና ፣ እንዲተዋወቅ ፣ አመልክቼ ፣ ከምሳ ፣ በኋላ ፣ መጥቶ ፣ እንዲገ ናኝ ፣ ፈቀደውለት ፣ ነበርና ፣ ሊጋባው ፣ መጥቶ ፣ መምጣቱን ፣ ባስታወቀ ፣ ጊዜ ፣ ይግባ ፣ ተብሎ ፣ ከንጉሠ ፣ ነገሥቱና ፣ ከእቴጌይቱ ፣ ጋራ ፣ አስተ ቀወቅሁት ።

ከዚህም ፣ በኋላ ፣ ሊጋባው ፣ ወደ ፣ ንጉሠ ፣ ነገሥቱ ፣ ቀርቦ ፣ እጅ ፣ ሲነሣ ፣ ንጉሠ ፣ ነገሥቱና ፣ እቴጌይቱ ፣ ወደ ፣ እልፍኛቸው ፣ ለመሔድ ፣ ተነሡ ። እኔም ፣ እየቀረብሁ ፣ ተሰናብቼ ፣ ከመኳንንቱ ፣ ጋራ ፣ ቆምሁ ።

ከደራሹም ፣ እስቲወጡና ፣ ላይን ፣ እስቲሰወሩ ፣ ድረስ ፣ ሁላችንም ፣ አንገታችንን ፣ ደፍተን ፣ እጅ ፣ እንነሣ ፣ ነበርና ፣ በኋላ ፣ እርስ ፣ በርሳችን ፣ ተሰነባብተን ፣ እየወጣን ፣ ሔድን ።

የቤተ ፣ መንግሥቱ ፣ ሥርዓት ፣ እንግዶቹን ፣ ውጡና ፣ ሒዱ ፣ ከማለ ት ፣ ንጉሠ ፣ ነገሥቱ ፣ መጀመሪያ ፣ ተነሥተው ፣ ወደ፣እልፍኝ ፣ መሔድ ፣ መልካም ፣ ሥርዓት ፣ ነው ።

ስምንት ፣ ሰዓትም ፣ በሆነ ፣ ጊዜ ፣ ወደ ፣ ሆቴል ፣ ተመለስን ።

አንድ ፣ ሰዓትም ፣ ያህል ፣ እንደ ፣ ቆየን ፣ የግቢው ፣ ሚኒስትር ፣ ክቡር ፣ ዶክቶር ፣ ኢኪ ፣ መጥቶ ፣ በንጉሠ ፣ ነገሥቱ ፣ ስም ፣ ቢዚት ፣ ለመመለስ ፣ ተልኮ ፣ መምጣቱን ፣ አስታውቆን ፣ ተመለሰ ።

ቢዚት ፣ መመለስ ፣ ማለት ። አንድ ፣ የውጭ ፣ አገር ፣ እንግዳ ፣ ወዳን ዱ ፣ መንግሥት ፣ አገር ፣ ሔዶ ፣ ከንጉሡ ፣ ጋራ ፣ ከተገናኘ ፣ በኋላ ፣ ወዲ ያው ፣ ዕለቱን ፣ እንደ ፣ እንግዳው ፣ ትልቅነት ፣ እንግዳው ፣ ንጉሥ ፣ የሆነ ፣ እንደሆነ ፣ ንጉሡ ፣ ራሱ ፣ ወደ ፣ ማረፊያው ፣ ሔዶ ፣ ይጠይቀዋል ። የነጋ

ሚ ፡ ዘር ፡ የሆነ ፡ እንደሆነ ፡ የነጋሚው ፡ ዘር ፡ በንጉሡ ፡ ስም ፡ ሆኖ ፡ ሔዶ ፡ ይጠይቀዋል ። የነጋሚ ፡ ዘር ፡ ያልሆነ ፡ ልዩ ፡ መላክተኛ ፡ የሆነ ፡ እንደ ሆነ ፡ ግን ፡ የግቢው ፡ ሚኒስትር ፡ በንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ስም ፡ ሆኖ ፡ ይጠይ ቀዋልና ፡ ቢዚት ፡ መመለስ ፡ ማለት ፡ ይህ ፡ ነው ።

---

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

### በጥቅምት ፡ ፳፯ ፡ ቀን ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂን ፡ ሽራይን ፡ ለማየት ፡ ሔድን ።

---

ሚጂ ፡ ከ፲፰፻፶፱ ፡ ዓመ ፡ ምሕ ፡ እስከ ፡ ፲፱፻፬ ፡ ዓመ ፡ ምሕ ፡ ፵፭ ፡ ዓመት ፡ ሙሉ ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የነበረው ፡ ነው ።እስቲነግሥ ፡ ድረስ ፡ ስሙ ፡ ሙትሱሒቶ ፡ ይባል ፡ ነበር ። በነገሠ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ሚጂ ፡ ተብሎ ፡ ተሰየመ ። ይህም ፡ ልማድ ፡ በሀገራችን ፡ በኢትዮጵያም ፡ ከቀድሞ ፡ ጀምሮ ፡ እስካሁን ፡ ድረስ ፡ ሲደረግ ፡ ይኖራል ። አጼ ፡ ልብነ ፡ ድንግል ፡ ወናግ ፡ ሰገድ ። አጼ ፡ ሚናስ ፡ አጥናፍ ፡ ሰገድ ። አጼ ፡ ሠርፀ ፡ ድንግል ፡ መለክ ፡ ሰገድ ። አጼ ፡ ሱስንዮስ ፡ ሥልጣን ፡ ሰገድ ። አጼ ፡ ኢያሱ ፡ አድያም ፡ ሰገድ ። ደጃች ፡ ካሣ ፡ ቴዎድሮስ ። ደጃች ፡ ጎበዜ ፡ ተክለ ፡ ጊዮርጊስ ። ሁለተኛው ፡ ደጃች ፡ ካሣ ፡ ዮሐንስ ፤ ራስ ፡ ተፈሪ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ተብለዋል ።

ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂ ፡ ለጃፓን ፡ የሠራውን ፡ መልካሙን ፡ ሥራ ውን ፡ ሁሉ ፡ በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ ለመጻፍ ፡ ጊዜ ፡ የለኝምና ፡ አገራቸ ውን ፡ ለሚወዱ ፡ ሰዎች ፡ ደስ ፡ እንዲላቸው ፡ አሳቡ ፡ ወደ ፡ መልካም ፡ ሥራ ፡ የተመራበትን ፡ ምክንያቱን ፡ ብቻ ፤ ባጭሩ ፡ እጽፋለሁ ።

ጃፓን ፡ እስከ ፡ ፲፰፻፵፮ ፡ ዓመ ፡ ምሕ ፡ ለውጭ ፡ አገር ፡ መንግሥ ቶች ፡ አልታወቀችም ፡ ነበር ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ የፖርቱጊዝ ፡ ነጋ ዲዎችና ፡ ሚሲዮኖች ፡ ስለ ፡ መጡ ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ መታወቅ ፡ ጀመረች ።

እነዚህንም ፡ የውጭ ፡ አገሮችን ፡ ሰዎች ፡ ካገርዋ ፡ ውስጥ ፡ ለማጥ ፋት ፡ ስትከላከል ፡ የብዙ ፡ ሰዎች ፡ ደም ፡ እስከማፍሰስ ፡ ደርሳ ፡ ነበር ።

ነገር ፡ ግን ፡ ከፖርቱጊዞችም ፡ በኋላ ፡ የእንግሊዝም ፤ የአሜሪካም ፤ የጀርመንም ፤ የፈረንሳዊም ፤ ነጋዴዎችና ፡ ሠራተኞች ፡ በብዙ ፡ መጥተ ው ፡ ነበርና ፡ ከሁሉም ፡ ጋራ ፡ ለመጣላት ፡ የሚያሠጋት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የመንግሥቷን ፡ ነጻነት ፡ ብቻ ፡ እየጠበቀች ፡ የአገርዋን ፡ በር ፡ ለውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ከፈተች ።

ይልቁንም ፡ የሚጂ ፡ አባት ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ኮሚይ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎችን ፡ እንዳይወድ ፡ የመንግሥቱ ፡ እንደራሴ ፡ ተኩጋዋ ፡ ይመክረው ፡ ነበርና ፡ በዘመኑ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡ ችግር ፡ ስለ ፡ አገኛቸው ፡ በጃፓን ፡ ላይ ፡ ባንድነት ፡ ለመነሣት ፡ ያስቡ ፡ ነበር ።

ነገር ፡ ግን ፡ ጃፓንን ፡ እግዚአብሔር ፡ ጠብቋታልና ፡ ኮሚይ ፡ ሞቶ ፡ ልጁ ፡ ሚጂ ፡ ሲነግሥ ፡ ደህና ፡ ደህና ፡ አማካሪዎችና ፡ ረዳቶች ፡ ስለ ፡ አገኘ ፡ እንደ ፡ አባቶቹ ፡ በስም ፡ ብቻ ፡ ነግሦ ፡ ሥራውን ፡ ለእንደራሴው ፡ እንዳይለቅ ፡ ስለ ፡ መከሩት ፡ የመንግሥቱን ፡ እንደራሴ ፡ በግድ ፡ አስለቅቆ ፡ አገር ፡ በእጄ ፡ ብሎ ፡ የመንግሥቱን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ራሱ ፡ ለመሥራት ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የጃፓን ፡ ልጆች ፡ ከእንቅልፋቸው ፡ ቢነሡ ፡ ሌሊቱ ፡ አልፎ ፡ ቀኑ ፡ በርቶ ፡ አገኙት ።

በጃፓንም ፡ አገር ፡ ብዙ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎችና ፡ ቆንስሎች ፡ ነበሩና ፡ የመንግሥቱ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ባንድ ፡ በንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ በመጠቅለሉ ፡ ደስ ፡ አላቸው ። ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂም ፡ ከውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ ወዳጅነቱን ፡ በማጽናቱ ፡ ባገሩ ፡ ውስጥ ፡ የትምሕርት ፡ ቤት ፡ እየሠራ ፡ የጃፓንን ፡ ልጆች ፡ እንዲያስተምር ፡ መከሩት ። እርሱም ፡ ለሀገር ፡ ነጻነትና ፡ ለሕዝብ ፡ ሥልጣኔ ፡ የትምሕርት ፡ ቤት ፡ ከማቆም ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ የሚሻል ፡ ነገር ፡ እንደሌለ ፡ ስለ ፡ ተረዳው ፡ ከዋናው ፡ ከተማ ፡ ጀምሮ ፡ በያውራጃው ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ የትምሕርት ፡ ቤት ፡ እንዲቆምና ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ልጁን ፡ በግድ ፡ እንዲያስተምር ፡ አዋጅ ፡ ነገረ ።

በዚህም ፡ ላይ ፡ ደግሞ ፡ ገንዘብ ፡ ያለው ፡ በገንዘቡ ፡ ገንዙብ ፡ የሌላውግን ፡ በመንግሥት ፡ ገንዘብ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አገር ፡ እየሔዱ ፡ የሚማሩ ፡ ልጆች ፡ እንዲመረጡ ፡ አደረገ ።

ደግሞ ፡ ካንድ ፡ መንግሥት ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ ከየመንግሥቱ ፡ አስተማሪዎችና ፡ ሠራተኞች ፡ እየቀጠረ ፡ እያመጣ ፡ የጃፓን ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ ንብ ፡ ከሁሉም ፡ እንዲቀስሙ ፡ አደረገ ።

የጦር ፡ መርከብን ፤ የባቡርን ፤ የላይት ፡ ሐውስን ፤ የቴሌግራፍን ፤ ሥራ ፡ ከእንግሊዝ ፡ መንግሥት ።

የወታደርን ፤ የሕግን ፤ የፍርድን ፡ ሥራ ፡ ከፈረንሳዊ ፡ መንግሥት ።

የወታደርንና ፡ የወታደር ፡ አለቆችን ፡ መመልመል ፡ ሥራ ፡ ከጀርመን ፡ መንግሥት ።

የእጅ ፡ ብልሃትንና ፡ የጥበብን ፤ የሥዕልን ፡ ሥራ ፡ ከኢጣልያ ፡ መንግሥት ።

የፖስታን ፤ የርሻን ፤ የትምሕርትን ፤ የንግድን ፡ ሥራ ፡ ከአሜሪካ ፡ መንግሥት ፡ እንዲማሩ ፡ አደረገ ።

ለጃፓንም ፡ ሥልጣኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ የፈቀደበት፡ ጊዜ ፡ ደርስዋልና፡ ባገርም ፡ ውስጥ ፡ ያሉት ፤ ወደ ፡ ውጭ ፡ አገርም ፡ የሔዱት ፡ የጃፓን ፡ ልጆች ፡ ትምሕርታቸው ፡ እየቀናቸው ፡ በመሔዱ ፡ ዓለም ፡ ሁሉ ፡ ይደነቅ ፡ ጀመር ።

ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂም ፡ ለሥራው ፡ ሁሉ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሠራተኞች ፡ በደመወዝ ፡ እየቀጠረ ፤ ለባለ ፡ ውልም ፡ እየሰጠ ፡ የመንግሥቱ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ በፍጥነት ፡ እንዲጀመር ፡ አደረገ ፡ እንጂ ፡ ያገሩ ፡ ልጆች ፡ እስቲማሩ ፡ አልጠበቀም ።

የቀንና ፡ የወርን ፤ ያመትንም ፡ ቍጥር (ካላንድር )የእሁድንም ፡ ማክበር ፡ እንደ ፡ አውሮጳ ፡ እንዲሆንና ፡ ሥራው ፡ ሁሉ ፡ ከአውሮጶች ፡ ጋራ ፡ እንዲተካከል ፡ አደረገ ።

ቀጥሎም ፡ የፖስታና ፡ የቴሌፎን ፡ የቴሌግራም ፡ ሥራ ፡ ተጀመረ ። የምድር ፡ ባቡርም ፡ ከቶኪዮ ፡ እስከ ፡ ዮክሃማ ፡ ተሠራ ። ሆስፒታልና ፡ ፋርማሲም ፡( የመድኃኒት ፡ መቀመሚያ)እንዲቆም፡ ፈቀደ ። ቀጥሎም ፡ ላይት ፡ ሐውስ ፡ በየወደቡ ፡ ሁሉ ፡ እንዲቆም ፡ አዘዘ ። ላይት ፡ ሐውስ ፡ ማለት ፡ መርከብ ፡ ሲመጣ፡ የመቋሚያውን ፡ ስፍራ፡የሚያመለክት፤ወይም ለመርከብ ፡ መቋሚያ ፡ የማይመች ፡ ስፍራ ፡ እንደሆነ ፡ መርከቡ ፡ እንዳይሰበር ፡ ብርሃን ፡ እያሳየ ፡ የሚያስጠነቅቅ ፡ ነው ።

የጋዜጣ ፡ ሥራና ፡ በየቋንቋው ፡ የታተሙ ፡ መጻሕፍቶች ፡ የሚሸጡበት ፡ ሱቅ ፡ ተሠራ ። ልዩ ፡ ልዩ ፡ ሱቆችም ፡ ስለ ፡ ተከፈቱ ፡ ያገሩ ፡ ሕዝብ ፡ ከትልቁ ፡ እስከ ፡ ትንሹ ፡ ባርኔጣና ፡ ጫማ ፡ ማድረግ ፤ ሰዓትና ፡ ጃንጥላ ፡ መያዝ ፡ ለመደ ።

በፈንጣጣም ፡ በያመቱ ፡ ብዙ ፡ ሰው ፡ ያልቅ ፡ ነበርና ፡ እንዲከተቡ ፡ አዋጅ ፡ ተደረገ ።

ፎቶግራፍ፡ማንሣትና፡ሥዕል፡መሣል፡ ሁሉ፡ተለመደ። በዳኝነትም፡ነገር፡ የመጀመሪያ ፡ ነገር ፡ የሚሰማበት፤ይግባኝም ፡ የሚባልበት ፡ ተለይቶ፡ቆመ ።

የጃፓን ፡ ሕዝብ ፡ የጥንቱ ፡ ሃይማኖት ፡ ሽንቶ ፡ የሚባለው ፡ ነበር ። በኋላ ፡ ግን ፡ የቡዳሃ ፡ ሃይማኖት ፡ ስለ ፡ ገባ ፡ ሥጋ ፡ መብላት ፡ ተነቅፎ ፡ ነበርና ፡

አሁን ፡ የመንግሥት ፡ ኃይማኖት ፡ እንደ ፡ ጥንቱ ፡ ሽንቶ ፡ ይሁን ፡ ብሎ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ሥጋ ፡ እንዲበላ ፡ አደረገ ።

ይህንም ፡ ሁሉ ፡ ከሠራና ፡ ካደላደለ ፡ በኋላ ፡ እርሱ ፡ ሲያልፍ ፡ ጃፓን ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ወደ ፡ ፊዮዳል ፡ መንግሥት ፡ ተመልሳ ፡ ጥፋት ፡ እንዳያገኛት ፡ ስለ ፡ አሰበላት ፡ መንግሥቱና ፡ ሕዝቡ ፡ ተጠባብቀውና ፡ ተከባብረው ፤ እንድነታቸውን ፡ አጽንተው ፡ የሚኖሩበት ፡ ሕገ ፡ መንግሥት ፡ በፈቃዱ ፡ አቆመላቸው ።

ይህንም ፡ የመሰለ ፡ ለዘላለም ፡ ስም ፡ የሚያስጠራውን ፡ መልካም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ከሠራ ፡ በኋላ ፡ በነገሠ ፡ በ፵፭ ፡ ዓመቱ ፡ በተወለደ ፡ በ፷ ዓመቱ ፡ አረፈና ፡ ከቶኪዮ ፡ ወደ ፡ ተወለደበትና ፡ መጀመሪያ ፡ ሥርዓተ ፡ ንግሥ ፡ ወደ ፡ አደረሰበት ፡ ወደ ፡ ኪዮቶ ፡ ከተማ ፡ ወስደው ፡ ቀበሩት ። ነገር ፡ ግን ፡ የመንግሥቱ ፡ ዋና ፡ ከተማና ፡ የዓለም ፡ ሕዝብ ፡ መሰብሰቢያ ፡ ቶኪዮ ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡ በቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ ውስጥ ፡ ለመናፈሻ ፡ ይሆናል ፡ ተብሎ ፡ እንዲያው ፡ የተቀመጠ ፡ እጅግ ፡ ሰፊ ፡ የሆነ ፡ ዱር ፡ ነበርና ፡ በዚያ ፡ ውስጥ ፡ እጅግ ፡ የተዋበ ፡ ሽራይን ፡ ሠርተውለት ፡ የከተማው ፡ ሕዝብ ፡ በየበዓሉ ፡ ቀን ፡ እየሄደ ፡ እጅ ፡ ሲነሣውና ፡ ሲያመሰግነው ፡ ይውላል ። የሚጂ ፡ ሥጋው ፡ ብቻ ፡ ሞቷል ፡ እንጂ ፡ ስሙ ፡ እስካሁን ፡ በሕይወቱ ፡ እንደ ፡ ነበረበት ፡ ዘመን ፡ ይከበራል ፡ ይመስገናል ።

በጃፓንም ፡ አገር ፡ ሽራይን ፡ የሚሠራላቸው ፡ ነገሥታቱ ፡ ብቻ ፡ አይደሉም ። ነገር ፡ ግን ፡ በጦርነትም ፡ ሆነ ፡ በሌላም ፡ ነገር ፡ ሆነ ፡ መንግሥታቸውና ፡ ሕዝባቸው ፡ የሚጠቀምበትንና ፡ የሚከበርበትን ፡ ሥራ ፡ ለሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ሽራይን ፡ ይሠራላቸዋል ። በእኛ ፡ አገር ፡ መንፈሳዊ ፡ ሥራ ፡ ለሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ጽላት ፡ ተቀረጸላቸው ፤ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ተሠራላቸው ፡ እንደሚባል ፡ በጃፓንም ፡ አገር ፡ ሰው ፡ የሚጠቀምበትና ፡ አገር ፡ የሚከበርበት ፡ ሥራ ፡ ከሠራ ፡ ሽራይን ፡ እንዲሠራለት ፡ ይገባዋል ፡ ይላሉ ።

ምሳሌ ። በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ አንዲት ፡ የጃፓን ፡ ልጃገረድ ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ዳር ፡ ሔዳ ፡ ሳለች ፡ የአሜሪካ ፡ መርከብ ፡ በድንገት ፡ ደርሶ ፡ መርከበኞቹ ፡ ማርከው ፡ ወሰድዋት ። እርስዋም ፡ እኔን ፡ ጃፓኒቱን ፡ ይህ ፡ አሜሪካዊ ፡ ሊያረክሰኝና ፡ ሊያዋርደኝ ፡ አይደለምን ፤ እንደምን ፡ አድርጌ ፡ ላምልጥ ፡ ብላ ፡ አስባ ፡ የምታመልጥበት ፡ ሌላ ፡ መንገድ ፡ እንዳታገኝ ፡ ባወቀች ፡ ጊዜ ፡ ራስዋን ፡ ለመግደል ፡ ቍርጥ ፡

አሳብ ፡ ካደረገች ፡ በኋላ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ያለውን ፡ ግጥም ፡ ጽፋ ሰውነቷን ፡ በገዛ ፡ እጅዋ ፡ ገደለች ።

ትሱዮ ፡ ዎ ፡ ዳኒ ፡ ኢቶ ፡ አ ፡ ያማቶ ፡ ኖ ፡ አሚናሜሺኢ ።

ፋሩ ፡ አሜሪካ ፡ ኢን ፡ ሶዴ ፡ ዋ ፡ ኑራ ፡ ሰጂኢ ፡

ትርጓሜ ።

በጃፓን ፡ ሜዳ ፡ የበቀለች ፡ አበባ ፡ አንድ ፡ ጠብታ ፡ ጤዛ ፡ ለማግኘት ፡ ምንም ፡ ብትቸገር ፡ እንኳ ። በአሜሪካ ፡ ዝናብ ፡ የልብሷን ፡ እጅጌ ፡ ለማራስ ፡ አትፈልግም ፡ ማለት ፡ ነው ።

ይህም ፡ ወሬ ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ በተሰማ ፡ ጊዜ ፡ ይህች ፡ ልጅ ፡ የጃፓንን ፡ ክብር ፡ ጭምር ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የራስዋን ፡ ክብር ፡ ብቻ ፡ አልጠበቀችምና ፡ ሸራይን ፡ ሊሠራላትና ፡ ልትከበር ፡ ይገባታል ፡ ብለው ፡ ሸራይን ፡ ተሠርቶላት ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ወደዚያ ፡ እየሔደ ፡ ሲያመሰግናትና ፡ ሲያከብራት ፡ ይኖራል ።

በአውሮጳም ፡ ቢሆን ፡ ሐውልት ፡ የሚቆመው ፡ ለመንግሥቱና ፡ ለሕዝቡ ፡ ጥቅም ፡ የሚሆን ፡ ሥራ ፡ ለሠራና ፡ ያገሩን፡ ክብር ፡ ለጠበቀም፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ለነገሥታት ፡ ብቻ ፡ አይደለም ።

ሸራይን ፡ ማለት ፡ ባማረኛ ፡ ቋንቋ ፡ መታሰቢያ ፡ ከማለት ፡ በቀር ፡ ሌላ፡ ትርጓሜ ፡ አይገኝለትም ።

ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ ነገሥታቱ ፡ በአክሱም ፡ በነበሩበት ፡ ጊዜ ፡ አንዳንድ ፡ ነገሥታት ፡ ስማቸውና ፡ ሥራቸው ፡ በደንጊያ ፡ ሐውልት ፡ እየተጻፈ ፡ ተገኝቶላቸዋል ፡ እንጂ ፡ ከሞቱ ፡ በኋላ ፡ የመታሰቢያ ፡ ቤት ፡ የተሠራላቸውና ፡ ሐውልት ፡ የቆመላቸው ፡ ነገሥታት ፡ መኖራቸውን ፡ በታሪክ ፡ ተጽፎ ፡ አላገኘንም ። ቃል ፡ ለቃልም ፡ ሲነገር ፡ አልሰማንም ። አሁን ፡ ግን ፡ ጃንሆይ ፡ አፄ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ገና ፡ አልጋ ፡ ወራሽና ፡ ባለ ፡ ሙሉ ፡ ሥልጣን ፡ እንደራሴ ፡ ሆነው ፡ ሳሉ ፡ ለሀገሩና ፡ ለሕዝቡ ፡ መልካም፡ ሥራ ፡ የሠራ ፡ ንጉሥ ፡ የመታሰቢያ ፡ ቤት ፡ እንዲሠራለትና ፡ ሐውልት ፡ እንዲቆምለት ፡ የሚገባ ፡ መሆኑን ፡ ለግርማዊት ፡ ንግሥተ ፡ ነገሥታት ፡ ዘውዲቱ ፡ አስረድተው ፡ ለኢትዮጵያ ፡ መልካም ፡ ሥራ ፡ ለጀመሩ ፡ ለዳግማዊ ፡ ምኒልክ ፡ የመታሰቢያ ፡ ቤት ፡ እንዲሠራላቸውና ፡ ሀውልት ፡ እንዲቆምላቸው ፡ አደረጉ ።

ወደ ፡ ፊትም ፡ ለኢትዮጵያና ፡ ለሕዝባቸው ፡ መልካም ፡ ሥራ ፡ የሚሠሩ ፡ ነገሥታትና ፡ አርበኞች ፡ እንደዚሁ ፡ የመታሰቢያ ፡ ቤት ፡ እንዲሠራላቸው ፡ ሀውልትም ፡ እንዲቆምላቸው ፡ የተገባ ፡ ነው ።

የሚጂንም ፡ ሸራይን ፡ ለማየት ፡ በሔድን ፡ ጊዜ ፡ ገና ፡ አንድ ፡ ኪሎ፡ ሜትር ፡ ሲቀረን ፡ ከአቶሞቢል ፡ ወርደን ፡ በእግራችን ፡ እንድንሔድ ፡ እ ስታወቁንና ፡ በእግራችን ፡ ሔድን ። የሸራይኑ ፡ አለቃ ፡ አድሚራል ፡ አሪማ ፡ የሚባለው ፡ ነው ። ግን ፡ በበታቹ ፡ አንድ ፡ ሊቀ ፡ ካህናት ፡ ሹም ፡ አለና ፡ የበታቹ ፡ ሹም ፡ እስከ ፡ ቅጥሩ ፡ በር ፡ ድረስ ፡ መጥቶ ፡ ተቀበለን ። አንደኛውንም ፡ ቅጥር ፡ ከገባን ፡ በኋላ ፡ ውሀ ፡ በመዘውር ፡ ወደ ፡ ተ ጠራቀመበት ፡ ስፍራ ፡ ወስደው ፡ እጃችሁን ፡ ታጥባችሁ ፡ ንጽሐን ፡ ሆ ናችሁ ፡ ወደ ፡ ሸራይኑ ፡ ትገባላችሁ ፡ ስላሉን ፡ ወደ ፡ መታጠቢው ፡ ስ ፍራ ፡ ሔደን ፡ እጃችንን ፡ ታጠብን ።

ወእነዝኅከሙ ፡ በማይ ፡ ንጽሕ ፡ ወትነጽሑ ፡ እምርኩስክሙ ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ባገራችን ፡ ቀሳውስቱ ፡ ጠበል ፡ እያሉ ፡ ሕዝቡን ፡ እንደሚ ረጩት ፡ ነው ።

ከዚያም ፡ ጥቂት ፡ እንዳለፍን ፡ ሁለት ፡ ካህናት ፡ የክህነት ፡ ልብስ ፡ ለብሰው ፡ በቀኝና ፡ በግራ ፡ ሆነው ፡ ወደ ፡ ሸራይኑ ፡ ወሰዱን ። በሸራይ ኑም ፡ ደጃፍ ፡ ሲደርሱ ፡ ለሚጂ ፡ እጅ ፡ መንሣት ፡ ይገባል ፡ ስላሉን ፡ እጅ ፡ ነሣን ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በመጣንበት ፡ መንገድ ፡ ተመልሰን ፡ ስንወጣ ፡ ሊቀ ፡ ካህናቱ ፡ ከኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ተልካችሁ ፡ ለመምጣ ታችሁ ፡ መታሰቢያ ፡ እንዲሆነን ፡ ፎቶግራፍ ፡ ተነሡልኝ ፡ ብሎ ፡ ስለ ፡ ለመነን ፡ ፎቶግራፍ ፡ ተነሥተን ፡ ወጣን ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ የሸንቶ ፡ ሸራይን ፡ የሚባለው ፡ እጅግ ፡ የከበረ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ አለቆቹ ፡ የነገሥታቱ ፡ ልጆችና ፡ ተወላጆች ፡ ነበሩ ። አሁን ፡ ግን ፡ በጦርነትም ፡ በሌላም ፡ ነገር ፡ መንግሥታቸውን፡እ ያገለገሉ ፡ ያረጁ ፡ ሰዎች ፡ ይሾሙታል ። የሚሾማቸውም ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ፡ ነው ። በጃፓን ፡ አገር ፡ የሸንቶንም ፡ የቡዳሃንም ፡ መቅደስ ፡ ቢሆን ፡ በላይ ፡ የሚቆጣጠራቸውና ፡ በልደረባቸው ፡ ያገር ፡ ግዛት ፡ ሚኒስትር ፡ ነው ።

የሚጂንም ፡ ሸራይን ፡ አይተን ፡ ስንወጣ ፡ በቶኪዮ ፡ ያለውን ፡ ትል ቁን ፡ የቡዳሃ ፡ መቅደስ ፡ እዩ ፡ ብለው ፡ ወሰዱን ። ገና ፡ ከበሩ ፡ ስንደርስ ፡ ሊቀ ፡ ካህናቱ ፡ መጥቶ ፡ ተቀበለን ። ከበሩ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ መቅደሱ ፡ ር ቀቱ ፡ ፳፻ ፡ ሜትር ፡ ይሆናል ።

አውቶሞቢል ፡ ከቅጥር ፡ ግቢ ፡ የማይገባ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ሊቀ ፡ ካህናቱ ፡ በፊት ፡ በፊታችን ፡ እየሔደ ፡ እስከ ፡ መቅደሱ ፡ በር፡ በእግራችን፡ ሔድን ፤ በበሩም ፡ ላይ ፡ ጫማችንን ፡ እንድናወልቅ ፡ ታዘዝን ። በጃፓን ፡ አገር ፡



# Déjeuner

du 6 Novembre 1931

Consommé Ambassadeur

Amadaï au Vin de Champagne

Mousse de Foie-gras à la Gelée

Cailles rôties à la Polonaise

Petits Pois à la Française

Parfait au Moka

Dessert

ከጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ምሳ ፡
ተጋብዘን ፡ የቀረበው ፡ ምግብ ፡ ዓይነትና ፡ ቍጥር ።



በንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂ ፡ መታሰቢያ ፡ በር ፡ ስንደርስ ።



በቶኪዮ ፡ ከትያትር ፡ ሊቃውንቶች ፡ ጋራ ፡ ስንገናኝ ።

ወደ ፡ ሽንቶ ፡ ሽራይንና ፡ ወደ ፡ ቡዳሃ ፡ መቅደስ ፡ የሚገባ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ጫማ ፡ ማውለቅ ፡ የግድ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ የመቅደሱ ፡ ውስጥ ፡ እጅግ ፡ ባማረ ፡ በነጭ ፡ ኬሻ ፡ ምንጣፍ ፡ የተነጠፈ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ምንጣፉ ፡ እንዳያ ድፍና ፡ እንዳይበላሽ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ስለ ፡ መቅደሱ ፡ ክብር ፡ ተብሎ ፡ አይ ደለም ።

ወዲያውም ፡ ካህናቱ ፡ እንዲሰበሰቡ ፡ ደወል ፡ ተደወለና ፡ በፍጥነት ፡ ከየበአታቸው ፡ እየወጡ ፡ ባንድነት ፡ ሆነው ፡ መጡ ።

መቅደሱ ፡ እንደ ፡ እኛ ፡ አገር ፡ መቅደስ ፡ በግንብ ፡ አይደለም ፡ እንጂ ፡ በትልልቅ ፡ ዓምድ ፡ ከሶስት ፡ የተከፈለ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ ቅኔ ፡ ማኅሌት ፤ ቅድስት ፤ መቅደስ ፡ እንደምንለው ፡ ነው ።

መጀመሪያው ፡ ክፍል ፡ ሕዝቡ ፡ እየቆሙ ፡ የሚጸልዩበት ፡ ነው ። ሁለተኛው ፡ ክፍል ፡ ካህናቱ ፡ የሚጸልዩበት ፡ ነው ። ካህናቱ ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ እየሆኑ ፡ በእጃቸው ፡ ትንንሽ ፡ መጽሐፍ ፡ እየያዙ ፡ በሶስቱ ፡ ማዕዘን ፡ ይንበረከካሉ ።

ሊቀ ፡ ካህናቱ ፡ ጥቂት ፡ ወደ ፡ ውስጥ ፡ ገባ ፡ ብሎ ፡ በተለየ ፡ ትንሽ ፡ ከፍታ ፡ ባለው ፡ ጣንቃ ፡ ላይ ፡ ይቆማል ። ዲያቆኑም ፡ በስተኋላው ፡ ይቆማል ።

ሊቀ ፡ ካህናቱ ፡ የለበሰው ፡ በስተ ፡ ውስጥ ፡ ጥቂት ፡ ረዘም ፡ ያለ ፡ ነጭ ፡ ቀሚስ ፤ በላይ ፡ አጠር ፡ ያለ ፡ ጥቁር ፡ ቀሚስ ፤ በዚያ ፡ ላይ ፡ የወ ይን ፡ ጠጅ ፡ ሐር ፡ የሚመስል ፡ ግልድም ፤ በዚያ ፡ ላይ ፡ የወይባ ፡ ቀለ ም ፡ የገባ ፡ ልብስ ፡ ነው ።

ካህናቱም ፡ በውስጥ ፡ አጠር ፡ ያለ ፡ ጥቁር ፡ ቀሚስ ፡ ለብሰው ፡ ቀኝ ፡ እጃቸውን ፡ እያወጡ ፡ በላይ ፡ የወይባ ፡ ልብስ ፡ ደርበዋል ።

ጸሎቱ ፡ ሲጀመርና ፡ ሲጨረስ ፡ የእንጨት ፡ ደወል ፡ ይደውላሉ ። አደዋወሉም ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ በየገጠሩ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እ ንደሚደወለው ፡ ቍጥር ፤ ግዕዝ ፡ ንባብ ፡ አለው ፤ ዕጣንም ፡ ያጥናሉ ።

ሶስተኛው ፡ ክፍል ፡ የቡዳሃ ፡ ምስል ፡ የቆመበት ፡ ነው ። ይኸው ም ፡ መሬቱ ፡ ሁለት ፡ ሜትር ፡ ያህል ፡ ተደልድሎ ፡ ደግሞ ፡ ከዚያው ፡ ከመካከሉ ፡ አንድ ፡ ሜትር ፡ ያህል ፡ ለብቻው ፡ ተደልድሎ ፡ ወጥቶ ፡ በዚያ ፡ ላይ ፡ የቡዳሃ ፡ ምስል ፡ ትልቅ ፡ የጉብስ ፡ ክምር ፡ መ ስሎ ፡ ይታያል ።

ሊቀ ፡ ካህናቱ ፡ በተለየለት ፡ ስፍራ ፡ ላይ ፡ ቆሞ ፡ ጸሎቱን ፡ ሲጀ ምር ፡ ዙሪያውን ፡ የተንበረከኩት ፡ ካህናት ፡ መጽሐፋቸውን ፡ እየገለጡ ፡

እየተቀባበሉ ፣ ያዜማሉ ። ከካህናቱም ፣ ጋራ ፣ የራስ፣ ጠጕራቸውን ፣ የተ ላጩ ፣ ደናግሎች ፣ ሴቶች ፣ ነበሩ ።

በጃፓን ፣ አገር ፣ ሴት ፣ ምንም ፣ ቢሆን ፣ የራሷን ፣ ጠጕር ፣ አትላጭም ። ነገር ፣ ግን ፣ አንዲት ፣ ሴት ፣ የራሷን ፣ ጠጕር ፣ የተላጨች ፣ እንደሆነ ፣ መ ነኩሲት ፣ መሆኗ ፣ በዚህ ፣ ይታወቃል ።

በጸሎታቸውም ፣ መጨረሻ ፣ በቡዳሃ ፣ ምስልና ፣ በሊቀ ፣ ካህናቱ ፣ መ ካከል ፣ ፫ ፣ ጊዜ ፣ ዑደት ፣ አደረጉና ፣ የእንጨቱ ፣ ደወል ፣ ተደውሎ ፣ ጸሎ ታቸውን ፣ ጨረሱ ።

ከዚህም ፣ በኋላ ፣ ሊቀ ፣ ካህናቱ ፣ ወደ ፣ እኛ ፣ ቀርቦ ፣ መቅደሱን ፣ ስላ የንለት ፣ ምስጋና ፣ አቀረበልን ።

ከዚህ ፣ በኋላ ፣ ጥቂቶች ፣ ጥያቄዎች ፣ እንድጠይቀው ፣ ፈቃድ ፣ ለመ ንሁና ፣ ከዚህ ፣ ቀጥሎ ፣ ያሉትን ፣ ጥያቄዎች ፣ ጠየቅሁት ።

ጥያቄ ። ይህ ፣ መቅደስ ፣ ከተሠራ ፣ ስንት ፣ ዓመቱ ፣ ነው ።

ምላሽ ። ፫፻ ፣ ዓመቱ ፣ ነው ።

ጥ ። በቀን ፣ ስንት ፣ ጊዜ ፣ ጸሎተ ፣ ማኅበር ፣ ታደርጋላችሁ ።

ም ። በቀን ፣ አራት ፣ ጊዜ ፣ ነው ። ይኸውም ፣ ጧት ፤ በ፫ ፣ ሰዓት ፤ በ፮ ፣ ሰዓት ፤ በ፱ ፣ ሰዓት ፤ በ፲፪ ፣ ሰዓት ፣ ነው ። ከዚህም ፣ በቀር ፣ ማ ታ ፣ በመኝታ ፣ ጊዜ ፤ ሌሊት ፣ በ፮ ፣ ሰዓት ፣ ጸሎተ ፣ ማኅበር ፣ እና ደርጋለን ።

ጥ ። ላንድ ፣ ጊዜ ፣ ጸሎት ፣ ስንት ፣ ስንት ፣ እየሆናችሁ ፣ ነው ።

ም ። እንደ ፣ ተገኘ ፣ ነው ። ነገር ፣ ግን ፣ ከ፴፫ ፣ ያነሱ ፣ ሊሆኑ ፣ አይ ገባም ። ከነዚሁም ፣ ሰባቱ ፣ ደናግል ፣ ሴቶች ፣ (መነኩሲቶች ፣) ናቸው ።

ጥ ። በጃፓን ፣ አገር ፣ ላለው ፣ የቡዳሃ ፣ መቅደስ ፣ ሁሉ ፣ ጠቅላይ ፣ አለቃ ፣ አላችሁን ።

ም ። መምሕሩ ፣ እያስተማረ ፣ ብዙ ፣ ማኅበር ፣ እንደ ፣ ማግኘቱ ፣ መቅደስ ፣ እየተከለ ፣ ለዚያው ፣ ለተከለው ፣ መቅደስ ፣ አለቃ ፣ ይሆናል ፣ እንጂ ፣ ጠቅላይ ፣ አለቃ ፣ የለንም ። ሥራችንን ፣ የሚጠባበቅና ፣ የሚ ቆጣጠር ፣ ግን ፣ ከመንግሥት ፣ ያገር ፣ ግዛት ፣ ሚኒስቴር ፣ ነው ።

ጥ ። በጸሎታችሁ ፣ ጊዜ ፣ ይህን ፣ አድርግልን ፣ ብላችሁ ፣ ወደ ፣ እግዚ አብሔር ፣ የምትለምኑትና ፣ አሳባችሁን ፣ የምትገልጹት ፣ ነገር ፣ አላችሁን ።

ም ። በጸሎታችን ፣ ወደ ፣ እግዚአብሔር ፣ የምናቀርበውና ፣ የምን ለምነው ፣ ነገር ፣ የለንም ። ነገር ፣ ግን ፣ ቡዳሃ ፣ በትምሕርቱ ፣ ሕዝቡን ፣

ሁሉ ፡ ከጭንቀትና ፡ ከመከራ ፡ ስለ ፡ አዳነ ፡ በዚህ ፡ በምስሉ ፡ ወይም ፡ በ ሥዕሉ ፡ ፊት ፡ እየቆምን ፡ እናመሰግነዋለን ። በምስጋናችንም ፡ ደስ ፡ እናሰኘዋለን ። በሥራችንም ፡ እንዲረዳን ፡ እንለምንዋለን ፡ አለኝ ።

ይኸውም ፡ በሀገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ ለጻድቁ ፡ ለአቡነ ፡ ተክለ ፡ ሃይ ማኖት ፡ እንደሚደረግላቸው ፡ ምስጋናና ፡ ክብር ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሌላ ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ ሌለበት ፡ ያስረዳል ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ከአለቃውም ፡ ከማኅበሩም ፡ ተሰነባብተን ፡ ወደ ፡ ሆቴላችን ፡ ተመለስን ።

## ሶስተኛ ፡ ትልቅ ፡ ክፍል ።

በቶኪዮና ፡ በቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ ዙሪያ ፡ ባሉት ፡ አገሮች ፡ ስለ ፡ ሆነው ፡ ነገር ።

ኒኮ ። በባቡር ፡ መቋሚያ ። ፏፏቴ ፡ ውሀ ። ባሕር ። የአሣ ፡ መርባት ። ቤተ ፡ መቅደስና ፡ ሽራይን ። የአንቲካና ፡ የዕቃ ፡ ቤት ። ወደ ፡ ቶኪዮ ። በውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስቴር ፡ ራት ፡ ግብዣ ። ዳክዮች ፡ ማደን ። (መያዝ ።) ዩንቢርስቲ ። የምድር ፡ መናወጥ ፡ መመርመሪያ ፡ ቤት ። የካሳካ ፡ የጦር ፡ መር ከብና ፡ የጦር ፡ አይሮፕላን ። የአድሚራል ፡ ቶጎ ፡ መርከብ ። የወታደር ፡ ሰል ፍና ፡ ጦርነት ፡ ማየት ። በሚሊታሪ ፡ ክለብ ፡ ራት ፡ ግብዣ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

በጥቅምት ፡ ፳፱ ፡ ቀን ፡ ከጧቱ ፡ በ፪ ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ከቶኪዮ ፡ ተነሥተን ፡ በ፯ሰዓት ፡ ኒኮ ፡ ገባን ። ኒኮ ፡ ሲዳር ፡ (ቄድሮስ ፡) በሚባል ፡ ዛፍ ፡ የተሸፈነችና ፡ የተከበበች ፡ በተራራ ፡ ጥግ ፡ ያለች ፡ ከተማ ፡ ናት ። የስፍራዋም ፡ አቀማመጥ ፡ ልዩ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በዛፍ ፡ መሸፈኗ ፡ አዲስ ፡ አበባን ፡ ትመስላለች ።

በባቡር ፡ መቋሚያም ፡ አገረ ፡ ገዥውና ፡ የከተማው ፡ ከንቲባ ፡ ከ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ መጥተው ፡ ተቀበሉን ። የባቡሩንም ፡ መቋሚያ ፡ ባለፍን ፡ ጊዜ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ የሚሆኑ ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ተማሪዎች ፡ በመንገዱ ፡ ቀኝና ፡ ግራ ፡ ተሰልፈው ፡ ከዳር ፡ እስከ ፡ ዳር ፡ ትንንሽ ፡ የ ኢትዮጵያ ፡ ባንዲራ ፡ ይዘው ፡ በደስታ ፡ ተቀበሉን ። ከዚያም ፡ አልፈን ፡ ኒኮ ፡ ካናያ ፡ ወደሚባለው ፡ ሆቴል ፡ ገባን ። በከተማው ፡ ውስጥና ፡ በ ከተማው ፡ ዙሪያ ፡ ካንድ ፡ ሚሊዮን ፡ የሚበልጥ ፡ የሲዳር ፡ ዛፍ ፡ ይገኛል ። ከዚሁም ፡ አርባው ፡ ሺ ፡ በ፲፮፻፳፬ ፡ ዓመት ፡ ሊሚትሱ ፡ የሚባለው ፡ የ መስፍኑ ፡ የቶኩጋዋ ፡ ሶስተኛ ፡ ትውልድ ፡ የነበረው ፡ የሽንቶን ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ለማሠራት ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ ያስተከለው ፡ ነው ፡ ይባላል ።

ነገር ፡ ግን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂ ፡ ሕገ ፡ መንግሥት ፡ ባቆመ ፡ ጊዜ ፡ ይህ ፡ በ ኒኮ ፡ ያለው ፡ የሲዳር ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ቤተ ፡ ዘመዶች ፡ ስለ ፡ ደ መወዛቸው ፡ መጨመሪያ ፡ እንዲሆን ፡ በሕግ ፡ ተወስኖላቸዋል ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

ይህንም ፡ ነገር ፡ ለግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ የዘውድ ፡ በዓል ፡ ከጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ተልኮ ፡ መጥቶ ፡ የነበረው ፤ አምባሳደር ፡ ዮሺዳ ፡ በቃል ፡ ነግሮኝ ፡ ነበርና ፡ አሁን ፡ በ ዓይኔ ፡ በማየቴ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አለኝ ።

ቀድሞ ፡ የተተከለው ፡ አርባው ፡ ሺ ፡ ዛፍ ፡ እያንዳንዱ ፡ ፳፻ዬን ፡ ያወጣል ፡ አሉን ። በድምሩ ፡ ፰ ፡ ሚሊዮን ፡ ዬን ፡ መሆኑ ፡ ነው ፡

አንዱ ፡ ዬን ፡ በዛሬው ፡ ምንዛሪ ፡ ፪ ብር ፡ ተኩል ፡ ሲሆን ፡ ፰ው ፡ ሚሊዮን ፡ ዬን ፡ ፳ ሚሊዮን ፡ ብር ፡ ይሆናል ።

ከምሳም ፡ በኋላ ፡ በተራራው ፡ ጫፍ ፡ ያለውን ፡ ኬጎን ፡ የሚባለውን ፡ ፏፏቴ ፡ ውሀ ፡ ለማየት ፡ ወጣን ። አገረ ፡ ገዥውና ፡ ሌሎችም ፡ ትልል ቆች ፡ ሰዎች ፡ የተቀመጡባቸው ፡ ሰባት ፡ አውቶሞቢሎች ፤ በጃፓንና ፡ በኢትዮጵያ ፡ ባንዲራ ፡ አጊጠው ፡ ተከትለውን ፡ ነበር ። በየመንገዱም ፡ ዳርና ፡ በየቤቱ ፡ ደጃፍ ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ ክብር ፡ የጃፓን ፡ ባንዲራ ፡ ተሰቅ ሎና ፡ አምሮ ፡ ይታይ ፡ ነበር ።

የተራራው ፡ ርዝመት ፡ ፬ሺ ፡ ፫፻፩ ፡ ጫማ ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ መ ንገዱን ፡ እያዘዋወሩ ፡ ስለ ፡ ሠሩት ፡ እስከ ፡ ጫፉ ፡ ድረስ ፡ በአውቶ ሞቢል ፡ ያስወጣልና ፡ ድካም ፡ የለበትም ።

ወደ ፡ ጫፉም ፡ በደርስን ፡ ጊዜ ፡ ፏፏቴው ፡ ወደ ፡ ግራ ፡ ባለው ፡ ገደ ል ፡ በኩል ፡ ነበርና ፡ ወደ ፡ መውረጃው ፡ ስፍራ ፡ ስንደርስ ፡ ፪፻የሚሆኑ ፡ ተማሪዎች ፡ የኢትዮጵያን ፡ ባንዲራ ፡ ይዘው ፡ ቆይተው ፡ ሰላምታ ፡ ሰጡን ።

ከዚያም ፡ በኤሌክትሪክ ፡ በሚወጣና ፡ በሚወርድ ፡ ቤት ፡ ውስጥ፤ ገብተን ፡ ወደ ፡ ታች ፡ መቶ ፡ ሜትር ፡ ወረድን ።

በጥጉም ፡ ቆመን ፡ ፏፏቴውን ፡ ካየን ፡ በኋላ ፡ ፏፏቴው ፡ የሚወ ጣበትን ፡ ቹዜንጂ ፡ የሚባለውን ፡ ባሕርና ፡ በባሕሩ ፡ ዙሪያ ፡ ለመናፈሻ ፡ የተሠራውን ፡ ከተማ ፡ ለማየት ፡ ወጣን ።

ባሕሩ ፡ እጅግ ፡ ሰፊ ፡ አይደለም ። ነገር ፡ ግን ፡ ዓባይ ፡ በጣና ፡ ላይ ፡ አልፎ ፡ እንዲወርድ ፡ የላይኞቹ ፡ ወንዞች ፡ ውሀ ፡ በባሕሩ ፡ ላይ ፡ አልፎ ፡ መጥቶ ፡ ከገደሉ ፡ ላይ ፡ ሲደርስ ፡ ፏፏቴ ፡ ሆኖ ፡ ይወረወራል ። ይህንም ፡ ፏፏቴ ፤ ለማየት ፡ የሚመጡ ፡ እንግዶች ፡ ብዙ ፡ ናቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ አወራረዱ ፡ ያምራል ፡ እንጂ ፡ በርዝመት ፡ ቢሆን ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵ ያ ፡ ከዚህ ፡ የሚበላልጡ ፡ ብዙ ፡ ፏፏቴዎች ፡ ይገኛሉ ። በባሕሩ ፡ ዳር ፡ እ ጅግ ፡ የሚያምሩ ፡ ሆቴሎችና ፡ ዕቃ ፡ የሚሸጥባቸው ፡ ቤቶች ፡ ተሠርተዋል ።

ስፍራው ፡ ከፍተኛ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ የሚኖሩ ፡ ትልልቅ ፡ ሰዎች ፡ በበጋ ፡ ወራት ፡ በሙቀት ፡ ጊዜ ፡ ወደዚያ ፡ እየወጡ ፡ ይናፈሳሉ ፡ ብለው ፡ ነገሩን ። ከውጭ ፡ አገር ፡ አምባሳደሮችም ፡ አንዳንዱ ፡ በዚሁ ፡ ባሕር ፡ ዳር ፡ ቦታ ፡ እየተከራዩ ፡ የበጋ ፡ መናፈሻ ፡ ቤት ፡ ሠርተዋል ።

ወደ ፡ ተራራው ፡ ለመውጣትና ፡ ከተራራው ፡ ለመውረድ ፡ መንገዱ ፡ ጠባብ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ አውቶሞቢሎቹ ፡ እንዳይጋጩ ፡ ተብሎ ፡ አንደኛው ፡ አውቶሞቢል ፡ ከመቆሚያው ፡ መድረሱ ፡ በስልክ ፡ ሳይጠየቅ ፡ ሌላው ፡ አውቶሞቢል ፡ አይነሣም ።

ይህንም ፡ ካየን ፡ በኋላ ፡ ከከተማው ፡ በስተግራ ፡ ያለውን ፡ ሪዩዙ ፡ የሚባለውን ፡ ሁለተኛውን ፡ የኒኮ ፡ ፏፏቴ ፡ አይተን ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ተመለስን ። ኒኮ ፡ የሚባለው ፡ አገር ፡ በፍጥረቱም ፡ በሰውም ፡ እጅ ፡ ሥራ ፡ እጅግ ፡ የተዋበ ፡ ሥፍራ ፡ ነው ።

ይህም ፡ ይታወቅ ፡ ዘንድ ፤ ዱ ፡ ኖት ፡ ሴይ ፡ ዚ ፡ ወርድ ፡ ኪክ ። ኡንቲል ፡ ዩ ፡ ሂብ ፡ ሲን ፡ ኒኮ ። ይባላል ።

ትርጓሜ ። እየዞርህ ፡ አገር ፡ ስታይ ፡ ኒኮን ፡ እስትታይ ፤ ድረስ ፡ እጅግ ፡ መልካም ፡ አገር ፡ ነው ፡ ብለህ ፡ አትናገር ። ኒኮ ፡ በደረስህ ፡ ጊዜ ፡ ከሁሉ ፡ በልጦ ፡ ታገኘዋለህና ፡ አስቀድሞ ፡ ያየኸውን ፡ ሌላውን ፡ አገር ፡ እጅግ ፡ መልካም ፡ ነው ፡ ብለህ ፡ ከተናገርህ ፡ በኋላ ፡ ለኒኮ ፡ መልካምነት ፡ ሌላ ፡ ቃል ፡ አታገኝም ፡ ማለት ፡ ነው ።

በጥቅምት ፡ ፴ ፡ ቀን ፡ ከጧቱ ፡ በ፫ ፡ ሰዓት ፡ ወጥተን ፡ ባለ ፡ ሆቴሉ ፡ ሙሴ ፡ ካናያ ፡ የሚያረባውን ፡ ዓሣ ፡ አየን ። ከላይ ፡ የወንዙ ፡ ውሀ ፡ ሲወርድ ፡ የሚጠራቀምበት ፡ ኩሬ ፡ አብጅቶ ፡ ዓሣዎቹ ፡ በኩሬ ፡ ውስጥ ፡ ይረባሉ ።

ውሀውንም ፡ እየተከተሉ ፡ ወደ ፡ ታች ፡ እንዳይወርዱ ፡ በብረት ፡ ሽቦ ፡ ታጥረዋል ። ዓሦቹ ፡ በጣም ፡ ትልልቅ ፡ ሆነዋል ። ቁጥራቸውንም ፡ ብን ጠይቀው ፡ በጣም ፡ ትልልቆቹ ፡ ፫፻ ፡ ይሆናሉ ፡ አለ ። እድሜያቸውንም ፡ ያንዳንዱን ፡ ያውቀዋልና ፡ ይህ ፡ ዓሣ ፡ ፩ ፡ ዓመቱ ፡ ነው ፤ ይህ ፡ ዓሣ ፡ ፪ ፡ ዓመቱ ፡ ነው ። ይህ ፡ ሶስት ፡ ዓመቱ ፡ ነው ፡ እያለ ፡ ወንዱንና ፡ ሴቱንም ፡ እየለየ ፡ አሳየን ።

ከሁሉም ፡ የሚበልጥ ፡ ነገር ፡ ዓሣውን ፡ በብርጭቆ ፡ ውስጥ ፡ ማርባቱ ፡ ነው ። ሴቲቱን ፡ ዓሣ ፡ ይዞ ፡ እንቁላሉን ፡ አውጥቶ ፡ በብርጭቆ ፡ ቱባ ፡ ያኖረዋል ። የብርጭቆ ፡ ቱባ ፡ ማለት ፡ ውፍረቱ ፡ የሸምበቆ ፡ ያህል ፡ የሆነ ፡ ውስጠ ፡ ክፍት ፡ ማለት ፡ ነው ።

እንቁላሉንም ፡ በዚያ ፡ ሲያስቀምጠው ፡ በሳምንቱ ፡ ዓሣ ፡ ለመሆን ፡ ትንሽ ፡ ምልክት ፡ ይሰጣል ። በሁለተኛው ፡ ሳምንት ፡ በጣም ፡ የሚታይ ፡ ምልክት ፡ ይሰጣል ። በ፫ኛው ፡ ሳምንት ፡ ቀጭን ፡ ትል ፡ ሆኖ ፡ ይታያል ። በ፬ኛው ፡ ሳምንት ፡ ግን ፡ ዓሣ ፡ ሆኖ ፡ ይታያል ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ቡሹን ፡ እየከፈተ ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ ወተትና ፤ የእንቁላል ፡ አስኳል ፡ እየሰጠ ፡ ይመግበዋል ።

ብርጭቆውም ፡ እንዳይጠበው ፡ እየጠበቀና ፡ እያዛወረ ፡ በቤት ፡ ውስጥ ፡ በየክፍሉ ፡ እየደረደረ ፡ ያሳድገዋል ።

ያደገውን ፡ ዓሣ ፡ ይህ ፡ የ፩ ፡ ዓመት ፡ ነው ፤ የ፪ ፡ ዓመት ፡ ነው ፤ የ፫ ፡ ዓመት ፡ ነው ፤ የ፬ ፡ ዓመት ፡ ነው ፡ እያለ ፡ በብርጭቆ ፡ ውስጥ ፡ እንደሆነ ፡ አሳየን ።

የ፬ ፡ ዓመት ፡ ነው ፡ ያለው ፡ ቁመቱ ፡ ፺ ፡ ሳንቲም ፡ ውፍረቱ ፡ ፴ ፡ ሳንቲም ፡ ይሆናል ።

ከዚያም ፡ ወጥተን ፡ የኒኮን ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ለማየት ፡ ቅዱስ ፡ ድልድይ ፡ በሚባለው ፡ አጠገብ ፡ አለፍን ።

ቅዱስ ፡ ድልድይ ፡ የሚባለው ፡ ከከተማው ፡ ወደ ፡ መቅደሱ ፡ በሚወስደው ፡ መንገድ ፡ አጠገብ ፡ በሚወርደው ፡ ወንዝ ፡ ላይ ፡ የተሠራ ፡ ከዳር ፡ እስከ ፡ ዳሩ ፡ ቀይ ፡ ቀለም ፡ የተቀባ ፡ ድልድይ ፡ ነው ።

ይህም ፡ ድልድይ ፡ ተዘግቶ ፡ የሚኖር ፡ ስለሆነ ፡ ባመት ፡ የሽንቶ ፡ በዓል ፡ ቀን ፡ በዓሉን ፡ ለማክበር ፡ ከየአገሩ ፡ የሚመጡ ፡ እንግዶችና ፡ የከተማው ፡ ሰዎች ፡ እንዲሻገሩበት ፡ ይከፈታል ፡ እንጂ ፡ በሌላ ፡ ጊዜ ፡ አይከፈትም ። የሽንቶን ፡ (ሽራይን ፡) ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ሥራ ፡ ማማር ፡ እንደዚህ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ለመናገር ፡ ያስቸግራል ። በወርቅና ፡ በብር ፤ በነሐስ ፤ በክቡር ፡ ድንጋይ ፤ በብረት ፤ በተፈለፈለ ፡ እንጨት ፡ ያጌጠና ፡ የተሠራ ፡ ነው ።

የቤተ ፡ መቅደሱም ፡ ክፍል ፡ በያይነቱ ፡ ብዙ ፡ ነው ። በያንዳንዱም ፡ ክፍል ፡ ካህናቱ ፡ የጸሎት ፡ መጽሐፍ ፡ እየያዙ ፡ ይታያሉ ። የካህናቱም ፡ ልብስ ፡ ከሊቀ ፡ ካህናቱ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዲያቆኑ ፡ ድረስ ፡ መለዮ ፡ አለው ፡ እንጂ ፡ አንድ ፡ ዓይነት ፡ አይደለም ።

ይህንም ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ የሠራው ፡ የቶኩጋዋ ፡ ሁለተኛው ፡ ትውልድ ፡ ሂዴታዳ ፡ ቶኩጋዋ ፡ የሚባለው ፡ ነው ። ሥራውም ፡ በ፲፮፻፳፭ ፡ ዓ ፡ ም ፡ ተጀምሮ ፡ በ፲፮፻፴፮ ፡ ዓ ፡ ም ፡ ተጨረሰ ፤ በ፲፪ ፡ ዓመት ፡ መጨረሱ ፡ ነው ።



በኒኮ ፡ አጠጉብ ፡ ካለው ፡ ተራራ ፡ የሚወርደ
ውን ፡ ኪጎን ፡ የሚባለውን ፡ ፏፏቴ ፡ ስናይ ።



ቶኪዮ ፡ ደርሰን ፡ በባቡር ፡ መቋሚያ ፡ የጃፓን ፡ ሚኒስትሮች ፡ ሲቀበሉን ።



ወደ ፡ ጃፓን ፡ ስንሔድ ፡ የኮሎምቦን ፡ ከተማ ፡ ለማየት ፡ ከመርከብ ፡ እንደ ፡ ወረድን ፡፡



ከጂቡቲ ፡ እስከ ፡ ጃፓን ፡ የባሕር ፡ ወደብ ፡ ከተማ ፡ እስከ ፡ ኮቤ ፡ የሔድ
ንበት ፡ አንድሬ ፡ ሊቦን ፡ የሚባለው ፡ የማሳጂሪ ፡ ማረቲም ፡ መርከብ ።

ይህም ፡ ትልቅ ፡ አሳብ ፡ በታሰበበት ፡ ወራት ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ አልጋ ፡ ወራሽ ፡ ልዑል ፡ መርድ ፡ አዝማች ፡ አስፋ ፡ ወሰን ፡ አውሮጳን ፡ ለመጎብኘት ፡ እንዲሔዱ ፡ ስለ ፡ ታሰበ ፡ እኔ ፡ ልዑልነታቸውን ፡ ተከትዬ ፡ ለመሔድ ፡ ነገሩ ፡ ተቆርጦ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ በሁለቱ ፡ መንግሥቶች ፡ መካከል ፡ የተደረገውን ፡ የወዳጅነትና ፡ የንግድ ፡ ውል ፡ በግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ፈቃድና ፡ በውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስቴርነቴ ፡ ከጃፓን ፡ ልዩ ፡ መላክተኛ ፡ ጋራ ፡ ተነጋግሬ ፡ የተጻጻፍሁትና ፡ የተፈራረምሁት ፡ እኔ ፡ ስለ ፡ ሆንሁ ፡ በልዩ ፡ አምባሳደርነቴ ፡ ላይ ፡ ወዲያውም ፡ የውሉን ፡ አሳብና ፡ አፈጻጸም ፡ በቃል ፡ ለማስረዳት ፡ የእኔ ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ መሔድ ፡ የጃንሆይ ፡ አፄ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ፈቃድ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የአውሮጳ ፡ መንገዴ ፡ ቀርቶ ፡ ለጃፓን ፡ መንገዴ እንድሰናዳ ፡ ታዘዝሁ ።

ከዚህም ፡ ቀድሞ ፡ በግርማዊነታቸው ፡ ቸርነት ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ መላክተኛ ፡ እየሆንሁ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ እየተመላለስሁ ፡ አውሮጳንና ፡ አሜሪካን ፡ በማየቴ ፡ ደስ ፡ ሲለኝ ፡ እኖር ፡ ነበርና ፡ አሁን ፡ ደግሞ ፡ ከዚህ ፡ ቀደም ፡ ማንም ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ መላክተኛ ፡ ያልሔደበትን ፡ እሩቁን ፡ የፀሐይ ፡ መውጫ ፡ የሚባለውን ፡ የጃፓንን ፡ አገር ፡ በማዕርግና ፡ በክብር ፡ ለማየት ፡ በመታዘዜ ፡ ከታዘዝሁበት ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ በልቤ ፡ ውስጥ ፡ የደስታ ፡ ጐርፍ ፡ ሲጐርፍ ፡ ይሰማኝ ፡ ነበር ።

ለዚህም ፡ ለትልቁ ፡ መልእክቴ ፡ ጂቡቲ ፡ ላይ ፡ ያለው ፡ የኢትዮጵያ ፡ ቆንስል ፡ ልጅ ፡ ተፈራ ፡ ገብረ ፡ ማርያም ፡ ዋና ፡ ጸሐፊ ፡ ሆኖ ፡ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ እንዲሔድ ፡ ታዘዘልኝ ።

ደግሞ ፡ ከግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ዝምድና ፡ ያለው ፡ ልጅ ፡ አርአያ ፡ አበበ ፡ በኦፊሴል ፡ ሳይሆን ፡ አገር ፡ ለማየት ፡ ብቻ ፡ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ እንዲሔድ ፡ ከግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ተፈቀደለት ።

ለአስተርጓሚነትም ፡ በውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስቴር ፡ የአስተርጓሚነት ፡ ሥራ ፡ የሚሠራ ፡ አቶ ፡ ዳባ ፡ ብሩ ፡ ታዘዘልኝ ።

ስለዚህ ፡ መንገዳችን ፡ ሁሉ ፡ የደስታና ፡ የፍቅር ፡ መንገድ ፡ ሆኖ ፡ ነበር ።

ለማናቸውም ፡ ቢሆን ፡ ከአዲስ ፡ አበባ ፡ ተነሥቼ ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ ደርሼ ፡ መልእክቴን ፡ ፈጽሜ ፡ ወደ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ እስከ ፡ ተመለስሁበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ በየለቱ ፡ ከሠራሁትና ፡ ካየሁት ፡ ሁሉ ፡ ፍሬ ፡ ነገሩን ፡ እየለየሁ ፡ ጽፌዋለሁና ፡ ለአንባቢዎቼ ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ትምሕርት ፡ እንዲሆናቸው ፡ እርግጥ ፡ ነው ።

ዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ ወደ ፡ መንግሥታት ፡ ማኅበር ፡ በገባች ፡ ጊዜ ፡ የ ኢትዮጵያና ፡ የጃፓን ፡ መንግሥት ፡ መላክተኞች ፡ በጄኔብ ፡ ላይ ፡ ተ ገናኝተው ፡ ከመተዋወቅ ፡ ደረሱ ።

በዚያም ፡ ዘመን ፡ ከኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ መላክተኞች ፡ አንደ ኛው ፡ እኔ ፡ ራሴ ፡ ነበርሁ ።

ከዚያም ፡ ወዲህ ፡ ዛሬ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የሆኑት ፡ ልዑል ፡ ተፈሪ ፡ ገና ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ አልጋ ፡ ወራሽና ፡ ባለ ፡ ሙሉ ፡ ሥልጣን ፡ እንደራሴ ፡ ሆነው ፡ ሳሉ ፡ ከውጭ ፡ አገር ፡ መንግሥቶች ፡ ጋራ ፡ ወዳጅ ነት ፡ ለማጽናት ፡ ንግድ ፡ ለማስፋት ፡ ሙሉ ፡ ፈቃድ ፡ እንዳላቸው ፡ በተ ሰማ ፡ ጊዜ ፡ የምሥራቅ ፡ አገር ፡ መጨረሻ ፡ የሚሆን ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ በ፲፱፻፲፯ ዓ ፡ ም ፡ ፖርት ፡ ሳይድ ፡ ላይ ፡ የጃፓን ፡ ቆንስል ፡ ሆኖ ፡ የሚኖረውን ፡ ሙሴ ፡ ክሮኪ ፡ የሚባለውን ፡ ወደ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ልከው ፡ ነገሩን ፡ ሁሉ ፡ አስመረመሩ ።

ልዑል ፡ አልጋ ፡ ወራሽም ፡ ሙሴ ፡ ክሮኪን ፡ በመልካም ፡ አቀባበል ፡ ተቀብለው ፡ ኢትዮጵያን ፡ ወደ ፡ ትልቅ ፡ የሥልጣኔ ፡ ደረጃ ፡ ለማድረስና ፡ ሕዝባቸውን ፡ ለማሠልጠን ፡ ፈቃዳቸው ፡ መሆኑን ፡ ገልጠው ፡ ስለ ፡ ነ ገሩትና ፡ ስለ ፡ አሳዩት ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ ተመልሶ ፡ በአዲስ ፡ አበባ ። ያየውንና ፡ የሰማውን ፡ ሁሉ ፡ ለመንግሥቱ ፡ ባስታወቀ ፡ ጊዜ ፡ በ፲፱፻፳ ዓ ፡ ም ፡ ሌላ ፡ ባለ ፡ ሙሉ ፡ ሥልጣን ፡ መላክተኛ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ተልከ ፡ መጥቶ ፡ የወዳጅነትና ፡ የንግድ ፡ ውል ፡ ተዋውሎና ፡ ተፈራርሞ ፡ ተመለሰ ።

ደግሞ ፡ በ፲፱፻፳፫ ዓ ፡ ም ፡ ግርማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ የንጉሠ ፡ ነገ ሥት ፡ ዘውድ ፡ በሚጭኑበት ፡ ጊዜ ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ስለ ፡ ሁለቱ ፡ መንግሥቶች ፡ ወዳጅነት ፡ የዘውዱን ፡ በዓል ፡ ለማክበር ፡ ምስተ ር ፡ ዮሺዳ ፡ የሚባል ፡ ልዩ ፡ አምባሳደር ፡ ልከው ፡ ነበርና ፡ የዘውዱ ፡ በዓ ል ፡ ሲጨረስ ፡ የወዳጅነቱንና ፡ የንግዱን ፡ ውል ፡ አሳድሶ ፡ ተመልሶ ፡ ነበር ።

የሁለቱም ፡ መንግሥቶች ፡ ወዳጅነት ፡ ይህን ፡ በመሰለ ፡ በጠንካራ ፡ መሠረት ፡ መመሥረቱ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ሆነ ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ጃንሆይ ፡ አፄ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ይህን ፡ መሠረት ፡ ለማጽናትና ፡ በመሠረቱ ፡ ላይ ፡ ሥራ ፡ ለመሥራት ፡ ስለ ፡ ፈቀዱ ፡ እንደ ፡ ዓለም ፡ ነገሥታት ፡ ደንብ ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ለዘውድ ፡ በዓ ላቸው ፡ ልዩ ፡ አምባሳደር ፡ ስለ ፡ መላካቸው ፡ የወዳጅነት ፡ ብድር ፡ ለመ መለስ ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ ልዩ ፡ አምባሳደር ፡ ለመላክ ፡ አሰቡ ።

ፋሲልም ፡ የጎንደርን ፡ ግንብና ፡ የዓባይን ድልድይ ፡ እንደ ፡ ሠሩለት ፡ በሙሉ ፡ ኢትዮጵያ ፡ የታወቀ ፡ ነገር ፡ ነው ።

ቀጥሎም፡ በአጼ ፡ ኢያሱ፡ አድያም ፡ ሰገድ ፡ ዘመን ፡ የፈረንሣዊ፡ መንግሥት ፡ ሙሴ ፡ ፔንዝ ፡ የሚባል ፡ ቆንስል ፡ ልኮ ፡ ነበር ።

ከዚያ ፡ ወዲህ ፡ ግን ፡ አገር ፡ እየዞሩ ፡ የሚያዩና ፡ ታሪክ ፡ የሚጽፉ ፡ እንደነ ፡ ጀምስ ፡ ብሩስ ፤ እንደነ ፡ እንጦንዮስ ፡ ዳባዲ ፤ እንደ ፡ ሌሎችም፡ እነዜህን ፡ እንደ ፡ መሰሉ ፡ አንዳንድ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ይመጡ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ በመንግሥት ፡ መላክተኛነት ፡ የመጡ ፡ አልነበሩም ።

በኋላ ፡ ግን ፡ በ፲፰፻፵፯ ፡ ም ፡ አጼ ፡ ቴዎድሮስ ፡ በነገሡ ፡ ጊዜ ፡ የውጭ ፡ አገር፡ ሚሲዮኖች ፡ ወደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ስለ ፡ መጡ ፡ በዜህ፡ምክንያት፡ የእንግሊዝና ፡ የፈረንሣዊ ፡ መንግሥቶች ፡ ቆንስሎች ፡ ልከው ፡ ነበር ።

በአጼ ፡ ዮሐንስም ፡ ዘመን ፡ ከእንግሊዝና ፡ ከኢጣልያ ፡ ከፈረንሣዊም ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ መላክተኞች ፡ እየተላኩና ፡ እየመጡ ፡ ይመለሱ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ በኢትዮጵያ ፡ ነዋሪ ፡ የሆነ ፡ ቆንስል ፡ አልመጣም ፡ ነበር ።

በጃንሆይ ፡ በዳግማዊ ፡ ምኒልክ ፡ ዘመን ፡ ግን ፡ የፈረንሳዊና ፡ የእንግሊዝ ፤ የኢጣልያና ፡ የጀርመን ፤ የአሜሪካና ፡ የመስኮብ ፡ መንግሥቶች ፡ የወዳጅነትና ፡ የንግድ ፡ ውል ፡ እየተዋዋሉ ፡ የቆንስል ፤ ቤትና ፡ ሌጋሲዮን ፡ እስከ ፡ ማቆም ፡ ደረሱ ።

አጼ ፡ ምኒልክም ፡ የወዳጅነትና ፡ የንግድ ፡ ውል ፡ ተዋውለው ፡ ሕዝባቸውን ፡ እስከ ፡ ማቃረብ ፡ ያደረሱት ፡ ከምዕራብ ፡ አውሮጳ ፡ መንግሥቶች ፡ ጋራ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከምሥራቅ ፡ እስያ ፡ መንግሥቶች ፡ ከጃፓን ፤ ከሺን ፤ ከሲያም ፤ ከአናም ፤ ከሌሎቹም ፡ እነዜህን ፡ ከመሰሉት ፡ ካንዳቸውም ፡ ጋራ ፡ የመገናኛ ፡ ውል ፡ አልተዋዋሉም ፡ ነበር ። መዋዋላቸውም ፡ ይቅርና ፡ እስከ ፡ ፲፰፻፺፯ ፡ ም ፡ ከዜህ ፡ በላይ ፡ የተቆጠሩት ፡ የምሥራቅ ፡ መንግሥት ፡ አገሮች ፡ መኖራቸው ፡ እንኳ ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ አልታወቀም ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ በ፲፰፻፺፯ ፡ ም ፡ ጃፓንና ፡ መስኮብ ፡ ተዋግተው ፡ ጃፓን ፡ ድል ፡ ባደረገ ፡ ጊዜ ፡ በዚያ ፡ ዘመን ፡ ብዙ ፡ መስኮቦች ፡ በአዲስ ፡ አበባ ፡ ነበሩና ፡ ጃፓን ፡ የሚባል፡ መንግሥት ፡ መኖሩ ፡ ከመስኮቦች ፡ አፍ ፡ ተሰምቶ፡ነበር ።

ከዚያም ፡ ወዲህ ፡ ግርማዊት ፡ ንግሥተ ፡ ነገሥታት ፡ ዘውዲቱ ፡ በነገሡ ፡ ልዑል ፡ ተፈሪ ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ አልጋ ፡ ወራሽና፡ ባለ ፡ ሙሉ ፡ ሥልጣን ፡ እንደራሴ ፡ በሆኑ ፡ በ፮ኛው ፡ ዓመት ፡ የኢት

## መቅድም ።

ኢትዮጵያ ፡ ከቀድሞ ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ ከውጭ ፡ አገር ፡ መንግሥ ቶች ፡ ጋራ ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ እየተገናኘች ፡ ስትኖር ፤ እስካሁን ፡ ከጃ ፓን ፡ መንግሥት ፡ ጋራ ፡ ሳትገናኝ ፡ የቆየችበትንና ፡ አሁን ፡ ከመቃረብና ፡ ከመገናኘት ፡ የደረሰችበትን ፡ ለዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ አንባቢዎች ፡ አጭር ፡ ማ ስረጃ ፡ እጽፋለሁ ።

ይህንም ፡ ስጽፍ ፡ ከንግሥተ ፡ ሳባ ፡ ወዲህ ፡ ባለው ፡ ዘመን ፡ ውስጥ ፡ የሆነውን ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከዚያ ፡ አስቀድሞ ፡ የነበረውን ፡ በጭራሽ ፡ አላነሣሁትም ።

ማክዳ ፡ የተባለችው ፡ ንግሥተ ፡ ሳባ ፡ የነገሠችው ፡ ክክርስቶስ ፡ ልደት ፡ አስቀድሞ ፡ በሺ ፡ ዓመት ፡ ነው ። እርስዋ ፡ በነገሠች ፡ በ፳ኛው ፡ ዓመ ት ፡ የሰሎሞንን ፡ ጥበብ ፡ ለመስማት ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወርዳ ፡ ነ በርና ፡ ከሰሎሞን ፡ ፀንሳ ፡ ተመልሳ ፡ ቀዳማዊ ፡ ምኒልክን ፡ ወለደች ።

ቀዳማዊ ፡ ምኒልክም ፡ ካደገ ፡ በኋላ ፡ አባቱን ፡ ሰሎሞንን ፡ ለማየት ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወርዶ ፡ ሲመለስ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ተከትለውት ፡ ወደ ፡ ኢት ዮጵያ ፡ መጥተው ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ ክብረ ፡ ነገሥት ፡ የሚባለው ፡ የታሪክ ፡ መጽሐፋችን ፡ ያስረዳናል ።

ከዚያም ፡ ወዲህ ፡ ከአረብ ፡ አገርና ፡ ከህንድ ፡ አገር ፡ በንግድም ፡ በሌላም ፡ ሥራ ፡ ምክንያት ፡ አንዳንድ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ወ ደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ መምጣታቸው ፡ አልቀረም ።

ደግሞ ፡ በ፲፬፻፳ ፡ ዓ ፡ ም ፡ በአጼ ፡ ዘርአ ፡ ያዕቆብና ፡ በልጁ ፡ በ አጼ ፡ በእደ ፡ ማርያም ፡ ዘመን ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ መጥተው ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ የአጼ ፡ ዘርአ ፡ ያዕቆብና ፡ የበእደ ፡ ማርያም ፡ ታሪክና ፡ መጽሐፈ ፡ ምስጢር ፡ የሚባለው ፡ ያባ ፡ ጊዮርጊስ ፡ መጽሐፍ ፡ ያስረዳናል ።

ቀጥሎም ፡ በ፲፭፻፲፭ ፡ ዓ ፡ ም ፡ መሐመድ ፡ ግራኝ ፡ የሚባል ፡ እ ስላም ፡ ከዘይላ ፡ ተነሥቶ ፡ በአዳል ፡ አገር ፡ መጥቶ ፡ ኢትዮጵያን ፡ ባ ጠፋ ፡ ጊዜ ፡ በአጼ ፡ ልብነ ፡ ድንግል ፡ ልመና ፡ ብዙ ፡ ፖርቱጊዞች ፡ መጥተው ፡ ግራኝን ፡ ወግተው ፡ በዚሁ ፡ በኢትዮጵያ ፡ እየተራቡ ፡ መ ኖራቸውን ፡ ታሪከ ፡ ነገሥት ፡ ይመሰክራል ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ከአጼ ፡ ሱስንዮስ ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ አጼ ፡ ፋሲል ፡ ዘመን ፡ ብዙ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ እንደመጡ ፤ ለአጼ

በየቀኑም ፡ የሚሠሩት ፡ ሠራተኞች ፡ ፲፫ሺ ፡ ነበሩ ። ለሥራውም ፡ የወጣው ፡ ገንዘብ ፡ ፭ ፡ ሚሊዮን ፡ ዬን ፡ ነው ። የዚያን ፡ ዘመን ፡ ፭ ፡ ሚሊዮን ፡ በዛሬው ፡ ግምት ፡ ፪፻ ፡ ሚሊዮን ፡ ይሆናል ።

የቤተ ፡ መቅደሱም ፡ በሩና ፡ ደጀሰላሙ ፡ ብቻ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ይመስላል ። ደግሞ ፡ የቀድሞ ፡ የጃፓን ፡ ሰዎች ፡ በአሳባቸው ፡ እንደሚ መስላቸው ፡ ለነፍስ ፡ አንድ ፡ አምላክ ፤ ለእሳት ፡ አንድ ፡ አምላክ ፤ ለመ ብረቅ ፡ አንድ ፡ አምላክ ፤ አለ ፡ ይሉ ፡ ነበርና ፡ ምንም ፡ ዛሬ ፡ እው ነትነው ፡ ብለው ፡ ባይቀበሉት ፡ የዚያ ፡ ሁሉ ፡ ምስል ፡ በየበሩና ፡ በየደ ጀሰላሙ ፡ እንደ ፡ አንቲካ ፡ ቆሞ ፡ ይታያል ።

የነፍስ ፡ አምላክ ፡ የተነፋ ፡ ቀረጢት ፡ በጫንቃው ፡ ተሸክሞ ፡ የቀረጢ ቱን ፡ አፍ ፡ አንቆ ፡ ይዞ ፡ ነፋሱን ፡ በትንሽ ፡ በትንሹ ፡ የሚለቅ ፡ ይመስላል ።

የእሳት ፡ አምላክ ፡ በነበልባለ ፡ እሳት ፡ መካከል ፡ ተቀምጦ ፡ ይታያል ።

የመብረቅም ፡ አምላክ ፡ የእሳት ፡ አሎሎ ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ መሬት ፡ ይመለከታል ።

ይህም ፡ አደራረግ ፡ አምላክ ፤ መልአክ ፡ በማለት ፡ ይለያይ ፡ እንጂ ባገራችንም ፡ ሊቃውንቱ ፡ መዝገበ ፡ ነፋስ ፤ መዝገበ ፡ መብረቅ ፤ መዝ ገበ ፡ ብርሃን ፤ አለ ። ለነዚህም ፡ ሁሉ ፡ አንዳንድ ፡ ጠባቂ ፡ መልአክ ፡ አላቸው ፡ ይላሉ ። ቅ ፡ ራጉኤል ፡ መጋቤ ፡ ፀሐይ ፡ ወወርሕ ፡ ወከዋ ክብት ። ቅ ፡ ኡራኤል ፡ መጋቤ ፡ ነፋሳት ፡ ይባላሉ ። ስለዚህ ፡ አሳቡ ፡ እጅግ ፡ የተራራቀ ፡ አይደለም ።

በቤተ ፡ መቅደሱም ፡ ጣራ ፡ ላይ ፡ በየክፍሉ ፡ ሁሉ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ዓይነት ፡ ሆኖ ፡ የተሣለ ፡ መቶ ፡ ደራጎን ፡ ይታያል ። ይኸውም ፡ ጃፓ ኖች ፡ ከሽኖች ፡ የተቀበሉት ፡ የቀድሞ ፡ ዘመን ፡ ልማድ ፡ ነው ።

በሽን ፡ አገር ፡ አሳባቸው ፡ ሁሉ ፡ በደራጎን ፡ ነበር ። ልጅ ፡ ወል ደው ፡ የሞተባቸው ፡ እንደሆነ ፡ አዝመራቸውም ፡ የጠፋ ፡ እንደሆነ ፤ ከብትም ፡ ሳይረባላቸው ፡ የቀረ ፡ እንደሆነ ፤ ቤታቸውም ፡ የተቃጠለ ፡ እንደሆነ ፤ ደራጎን ፡ ቢቆጣ ፡ ነው ፡ ይሉ ፡ ነበር ።

መልካም ፡ ነገርም ፡ የተደረገላቸው ፡ እንደሆነ ፡ ደራጎን ፡ ይቅርታ ፡ ቢያደርግልን ፡ ነው ፤ በደራጎን ፡ ቸርነት ፡ ነው ፡ ይሉ ፡ ነበር ።

ይህም ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ ባንዳንድ ፡ አገር ፡ ይልቁንም ፡ በ ቆላ ፡ አገር ፡ የዛር ፡ ውላጅ ፡ እየተባለ ፡ እንደሚፈራ ፤ ዛሩንም ፡ ለመለማ መጥ ፡ እየተባለ ፡ በግ ፤ ዶሮ ፡ ሲታረድለት ፡ እንደሚኖረው ፡ ነው ።

ይኸውም ፡ የሕዝቡ ፡ አሳብ ፡ በዚህ ፡ ተስቦ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ዛር ፡ የ ሚሉ ፡ ፍጥረት ፡ ባይኔ ፡ አየሁ ፡ የሚል ፡ የለም ። በጐጃምም ፡ የሕዝቡ ፡ አሳብ ፡ ሰውን ፡ ሰው ፡ ይበላዋል ፡ በማለት ፡ ተስቦ ፡ ሰውን ፡ ባይኑ ፡ የሚ በላ ፡ ቡዳ ፡ አለ ፡ እያለ ፡ ብዙ ፡ ሰው ፡ ሲፈራና ፡ ሲንቀጠቀጥ ፡ ይኖራል ።

ይኸውም ፡ በአሳቡ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሰው ፡ ባይኑ ፡ ሰውን ፡ ሲበላው ፡ አየሁ ፡ የሚል ፡ አይገኝም ።

በመንፈሳዊም ፡ ቢሆን ፡ የብዙ ፡ ሰው ፡ አሳብ ፡ እንደዚሁ ፡ ባንዳንድ ፡ መልክ ፡ ይሳባል ። ወንጌላዊ ፡ ዮሐንስ ፡ ክፉውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በደ ራጎን ፡ እየመሰለ ፡ በራእዩ ፡ ተናግሯል ።

ዮሐንስ ፡ መጥምቅም ፡ አሳቡ ፡ በበግ ፡ ተስቦ ፡ ጌታችንን ፡ በበግ ፡ መስሎታል ። መንፈስ ፡ ቅዱስንም ፡ በርግብ ፡ አምሳል ፡ አይቶታል ።

ደግሞ ፡ ከዋናው ፡ በር ፡ ጀምሮ ፡ በውስጡ ፡ በየወለሉ ፡ የተነጠፈ ው ፡ ጥርብ ፡ ድንጋይ ፡ የተገጠመው ፡ በእርሳስ ፡ ነው ።

በእርሳስም ፡ መገጠሙ ፡ በዚያ ፡ ዘመን ፡ የሲሚንቶ ፡ ነገር ፡ ስላል ታወቀ ፡ ይመስላል ።

ቤተ ፡ መቅደሱና ፡ ወለሉም ፡ የተሠራው ፡ ገደሉ ፡ እየተቆፈረ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ አፈሩ ፡ እንዳይናድ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ አስር ፡ ሜትር ፡ ያህል ፡ በጥርብ ፡ ድንጋይ ፡ ተገንብቷል ። በግምቡም ፡ ዙሪያ ፡ ሊያሹ ፡ ቶኩጋ ዋ ፡ በእጁ ፡ የተከላቸው ፡ የሴድሮ ፡(ቄድሮስ ፡)ዛፎች ፡ ይታያሉ ።

በሀገራችን ፡ በኢትዮጵያም ፡ አንዳንድ ፡ ትልልቅ ፡ ሰዎች ፡ ለስማ ችን ፡ መጠሪያ ፡ እያሉ ፡ ወይራ ፡ ወይም ፡ ጥድ ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ገረገራ ፡ ግቢ ፡ እየተከሉ ፡ እገሌ ፡ የተከለው ፡ ዓፀድ ፡ እየተባለ ፡ ሲነገ ርለት ፡ ይኖራል ።

ከዚያም ፡ በቤተ ፡ መቅደሱ ፡ በስተ ፡ ግራ ፡ ባለው ፡ በር ፡ አልፈ ን ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ፳፱ ደረጃ ፡ ወጥተን ፡ ሊያሹ ፡ የተባለውን ፡ የመጀመ ሪያውን ፡ ቶኩጋዋ ፡ መቃብር ፡ አየን ።

እርሱ ፡ የሞተው ፡ በሌላ ፡ አገር ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ በሚሞትበ ት ፡ ጊዜ ፡ በኒኮ ፡ ቅበሩኝ ፡ ብሎ ፡ ስለ ፡ ተናዘዘ ፡ አጽሙን ፡ አፍልሰ ው ፡ አምጥተው ፡ ቀበሩት ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

በሀገራችን ፡ በኢትዮጵያም ፡ አንዳንድ ፡ ትልልቅ ፡ ሰዎች ፡ በዚህ ፡ ገዳም ፡ በዚህ ፡ አገር ፡ ቅበሩን ፡ እያሉ ፡ እየተናዘዙ ፡ እንደዚሁ ፡ ይደረግላቸዋል ።

ከዚያም ፡ ወርደን ፡ ሁለተኛውን ፡ የሸንቶን ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ለ ማየት ፡ ገባን ። በዚህም ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ምንም ፡ የበዓሉ ፡ ቀን ፡ ባ ይሆን ፡ ለእኛ ፡ ለእንግዶቹ ፡ ሲሉ ፡ የበዓሉን ፡ አከባበር ፡ አሳዩን ።

ባገራችን ፡ በኢትዮጵያም ፡ ከ፳ ፡ ዓመት ፡ በፊት ፡ እንደ ፡ ዛሬ ፡ የው ጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ባዲስ ፡ አበባ ፡ ሳይበዙና ፡ ሳይለመዱ ፡ አንድ ፡ የ ውጭ ፡ አገር ፡ መንግሥት ፡ መላከተኛ ፡ መጥቶ ፡ የየአድባራቱን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ለመጎብኘት ፡ የፈለገ ፡ እንደሆነ ፡ ቀሳውስቱና ፡ ዲያቆናቱ፡ ልብሰ፡ተክህኖ ፡ እየለበሱ፤ መስቀል ፡ ጥና፡ እየያዙ፤ ደብተሮቹ፡ወረብ፡እየወረ ቡ ፤ ጸናጽልና፡ መቋሚያ፡እየያዙ፡ከበሮ፡እየመቱ፡እንዲቀበሉ ፡ይታዘዙ፡ነበር።

በኒኮም፡በሸንቶ፡መቅደስ፡የተደረገልን ፡ አቀባበል ፡ እንደዚያው ፡ ነው ።

ንዋየ ፡ ቅድሳቱም ፡ ምንም ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ ቢለያይ ፡ በብዙ ፡ ነ ገር ፡ ከእኛ ፡ አገር ፡ ንዋየ ፡ ቅድሳት ፡ ጋራ ፡ ይመሳሰላል ።

ነጋሪትና፡ ከበሮ፤ ጸናጽልም፡ አላቸው ። ዋሽንትም፡ ይነፋሉ ። ነገር ፡ ግን ፡ የኢትዮጵያ ፡ ካህናት ፡ ዋሽንት ፡ አይነፉምና ፡ በዚህ ፡ ብቻ ፡ ል ዩነት ፡ አላቸው ።

ደግሞ ፡ በእኛ ፡ አገር ፡ ወረብ ፡ የሚወርቡትና ፡ የሚያስረግጡት ፡ ደብ ተሮች ፡ ናቸው ። በሸንቶ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ግን ፡ ደናግል ፡ ሴቶች ፡ናቸው ።

የደናግሉ ፡ ሴቶችም ፡ ልብስ ፡ በውስጥ ፡ ነጭ ፡ ሐር ፡ ቀሚስ ፡ ሆኖ፡ በላይ ፡ ቀይ ፡ በለዲ ፡ ነው ። ከበለዲው ፡ በላይ ፡ እንደ ፡ ሞጣሕት ፡ ሆኖ፡ የተሰፋ ፡ ነጭ ፡ ሐር ፡ ደርበውበታል ። እጅጌው ፡ በጣም ፡ ሰፊና ፡ ረ ጅም ፡ ነው ። ያንን ፡ ለብሰው ፡ እንደ ፡ ከበሮው ፡ አመታትና ፡ እንደ፡ ጸናጽሉ ፡ አጣጣል ፡ እንደ ፡ ዋሽንቱ ፡ ድምጥ ፡ ሲያሸበሽቡና ፡ ሲያስረ ግጡ ፡ ማማራቸው ፡ እጅግ ፡ ያስደንቃል ።

የሸንቶ ፡ መቅደስ ፡ ሊቃውንት ፡ የግዕዝ ፡ ቋንቋ ፡ ባያውቁ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ አውቀው ፡ በሆን ፡ እኛ ፡ ስንደርስ ፡ በጽሑ ፡ መላእክት ፡ ንጉሠ፡ ነገሥት ፡ ዘኢትዮጵያ ፡ ወበሙ ፡ መዘምራን ። ማዕከለ ፡ ደናግል ፡ ዘባጥያ ተ ፡ ከበሮ ፡ ሳይሉ ፡ አይቀሩም ፡ ነበር ።

ወደ ፡ ውስጥም ፡ በገባን ፡ ጊዜ ፡ ነገሥታቱ ፡ በያመቱ ፡ የተወለዱበትን ፡ ቀን ፡ ለማክበር ፡ ለቤተ ፡ መቅደስ ፡ የሰጡትን ፡ ባለ ፡ ወርቅ ፡ ሀረግ፡የሆኑ ፡ እንደ ፡ ክታብ ፡ የተጠቀለሉ ፡ ብዙ ፡ መጻሕፍት ፡ አሳዩን ። በመጀመሪያው፡ አርእስቱ፡ላይ፡የነገሥታቱን፡ ስም፡ ያነሣል ። ከዚያም ፡ ጥቂት ፡ ዝቅ ፡ ብሎ ፡ መጽሐፉን ፡ ይጀምራል ።

ይህም ፡ በሀገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ የተወለዱበትን ፡ ቀን ፡ ለማክበር ፡ አይሁን ፡ እንጂ ፡ ለመታሰቢያ ፡ እያሉ ፡ ነገሥታቱ ፡ ለየደብሩ ፡ ለየገዳሙ ፡ መጽሐፍ ፡ ይሰጡ ፡ ሉ ። በመጽሐፉም ፡ መጀመሪያ ፡ ወይም ፡ በመጨረሻው ፡ ስማቸው ፡ እየተጻፈ ፡ ይገኛል ።

ምሳሌ ። ዝንቱ ፡ ገድለ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ ዘንጉሥ ፡ ሣህለ ፡ ሥላሴ ፡ ዘወሀቦ ፡ ለደብረ ፡ ሊባኖስ ። ዘሠረቆ ፡ ወዘፈሐቆ ፡ ውጉዘ ፡ ለይኩን ፡ ይላል ። በዚህ ፡ አምሳል ፡ የኢትዮጵያ ፡ ነገሥታት ፡ ለየደብሩ ፡ ለየገዳሙ ፡ የሰጡት ፡ ብዙ ፡ መጽሐፍ ፡ ይገኛል ።

ሊቀ ፡ ካህናቱም ፡ ፎተግራፍ ፡ ባንድነት ፡ እንድንነሣ ፡ ስለ ፡ ለመነን ፡ በበሩ ፡ ላይ ፡ ቆመን ፡ ተነሣን ።

ከዚያም ፡ ስንወጣ ፡ የቀድሞ ፡ ነገሥታት ፡ ለመታሰቢያ ፡ እያሉ ፡ የሰጡት ፡ የራስ ፡ ወርቅና ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ዓይነት ፡ የጦር ፡ መሣሪያ ፤ ጎራዴና ፡ ጦር ፤ ጋሻም ፡ ልብሰ ፡ መንግሥትም ፡ ነጋሪትም ፡ ሌላም ፡ ሌላም ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ አንቲካ ፡ የሚቀመጥበትን ፡ ቅዱስ ፡ ዕቃ ፡ ቤት ፡ የሚባለውን ፡ አሳዩን ።

ባገራችን ፡ በኢትዮጵያም ፡ ነገሥታቱ ፡ ልብሰ ፡ መንግሥታቸውን ፤ ጃንጥላቸውን ፤ ዘውዳቸውን ፡ እንኳ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ የሚሰጡ ፡ ይገኛሉና ፡ የኢትዮጵያና ፡ የጃፓን ፡ ልማድ ፡ በመመሰሉ ፡ በጣም ፡ አደነቅን ።

ደግሞ ፡ በዚሁ ፡ ቅዱስ ፡ ዕቃ ፡ ቤት ፡ በሚባለው ፡ ባንደኛው ፡ ክፍል ፡ ቤት ፡ የሶስት ፡ ዝንጀሮች ፡ ሥዕል ፡ ይታያል ።

፩ኛው ፡ ዝንጀሮ ፡ ባንድ ፡ እጁ ፡ ግራ ፡ ዓይኑን ፡ ጨፍኖ ፡ ይዟል ። በስሩም ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አትይ ፡ ይላል ። ፪ተኛው ፡ ዝንጀሮ ፡ ባንድ ፡ እጁ ፡ ግራ ፡ ጆሮውን ፡ ደፍኖ ፡ ይዟል ። በስሩም ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አትስማ ፡ ይላል ።

፫ኛው ፡ ዝንጀሮ ፡ ባንድ ፡ እጁ ፡ ያፉን ፡ ግማሽ ፡ አፍኖ ፡ ይዟል ። በስሩም ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አትናገር ፡ ይላል ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ቶኪዮ ፡ የምንመለስበት ፡ ሰዓቱ ፡ ስለደረሰ ፡ ከሊቀ ፡ ካህናቱ ፡ ተሰነባብተን ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ተመለስን ።

ወደ ፡ ባቡር ፡ መቆሚያም ፡ ስንሔድ ፡ የኒኮ ፡ ተማሪዎች ፡ ወንዶችም ፡ ሴቶችም ፡ እንደ ፡ ፊተኛው ፡ ጊዜ ፡ የጃፓንና ፡ የኢትዮጵያን ፡ ትንንሽ ፡ ባንዲራ ፡ እየያዙ ፡ በየመንገዱ ፡ዳር ፡ ቆመው ፡ በደስታ ፡ ተሰናበቱን ።



# Menu

Déjeuner du 11 Novembre 1931

Potage Chantilly

Langouste à l'Américaine

Tournedos à la Chasseur

Canard sauvage grillé, Salade

Pouding aux Amandes

Dessert

በጃፓን ፡ የውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስቴር ፡ ራት ፡
ተጋብዘን ፡ የቀረበው ፡ ምግብ ፡ ዓይነትና ፡ ቍጥር ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

በጥቅምት ፡ ፴ ፡ ቀን ፡ ከማታው ፡ በ፪ ፡ ሰዓት ፡ የጃፓን ፡ የውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስትር ፡ ክቡር ፡ ባሮን ፡ ሺዴሃራ ፡ ስለ ፡ ኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ መላክተኞች ፡ ክብር ፡ ብለው ፡ ቁጥራቸው ፡ ፴ ፡ የሆነ ፡ ሚኒስትሮችና ፡ ሌሎችም ፡ ብዙ ፡ መኳንንቶች ፡ ለራት ፡ ጋብዘው ፡ ነበርና ፡ በዚሁ ፡ ሰዓት ፡ ወደ ፡ ሹመት ፡ ቤታቸው ፡ ሔድን ።

የሹመት ፡ ቤት ፡ ማለት ፡ የጃፓን ፡ ሚኒስትሮች ፡ ሶስት ፡ ሶስት ፡ ቤት ፡ አላቸው ። ፩ኛው ፡ የመኖሪያ ፡ ቤታቸው ፡ ነው ፤ በዚህም ፡ ቤት ፡ ወዳጆቻቸውንና ፡ ዘመዶቻቸውን ፡ ይቀበላሉ ። ፪ኛው ፡ የሹመት ፡ ቤታቸው ፡ ነው ። በዚህም ፡ ቤት ፡ ለራትም ፡ ሆነ ፡ ለሻይም ፡ ሆነ ፡ የመንግሥት ፡ እንግዶችና ፡ ያገር ፡ ሹሞች ፡ የሚጋብዙበት ፡ ትንንሽም ፡ ያገር ፡ ውስጥ ፡ ጉዳይ ፡ የሚነጋገሩበት ፡ ነው ። ፫ኛው ፡ ቤት ፡ ከውጭ ፡ አገር ፡ መንግሥቶች ፡ ጋራ ፡ የሚያገናኛቸውን ፡ ጉዳይ ፡ ሁሉ ፡ የሚፈጽሙበት ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ አምባሳዶሮችንና ፡ ሚኒስትሮችን ፡ ቆንስሎችንም ፡ የሚቀበሉበት ፡ ነው ። ይህም ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ይባላል ።

እኛም ፡ በዚያው ፡ በተጠራንበት ፡ ሰዓት ፡ በደረስን ፡ ጊዜ ፡ ክቡር ፡ ባሮን ፡ ሺዲሃራ ፡ እስከ ፡ ደጃፉ ፡ መጥተው ፡ ተቀበሉን ። ወደ ፡ ማረፊያውም ፡ ቤት ፡ በወሰዱን ፡ ጊዜ ፡ ለእራት ፡ የተጠሩ ፡ ሚኒስትሮችና ፡ መኳንንቶች ፡ ተሰብስበው ፡ አገኘን ። አንዳንዱንም ፡ በየተራ ፡ እያቀረቡ ፡ አስተዋወቁን ።

ሰዓቱም ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ሙብል ፡ ቤቱ ፡ ገባን ። በገበታው ፡ ላይ ፡ የቀረበው ፡ ዛፍና ፡ አበባ ፡ ባታክልት ፡ ማኖሪያ ፡ እጅግ ፡ በማረ ፡ ሸክላ ፡ ውስጥ ፡ ተተክሎ ፡ የበቀለ ፡ ነበረ ፡ እንጂ ፡ የተቆረጠ፡አልነበረም። ይኸውም ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ በየትልልቁ ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ የተለመደ ፡ ነገር ፡ ነው ። ሥራውም ፡ እጅግ ፡ ቀላል ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ማንም ፡ ሰው፡በየቤቱ፡ ሊያደርገው ፡ ይቻላል ።

አሳላፊዎቹም፡ሁሉ፡እንደ፡ቤተ፡መንግሥት፡አሳላፊዎች፡የለበሱ፡ነበሩ ። ጠቅላይ ፡ ሚኒስትሩና ፡ የውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስትሩ ፡ ግንባር ፡ ለ[illegible]ንባር ፡ ተቀምጠው ፡ እኔን ፡ በውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስትሩ ፡ ቀኝ ፡ አስቀምጠውኝ፡ ነበር ። ልጅ ፡ ተፈራንና ፡ ልጅ ፡ አርአያን ፡ አቶ ፡ ዳባንም ፡ እንደዚሁ ፡ በየሚኒስትሮቹ ፡ ጣልቃ ፡ እያገቡ ፡ አስቀምጠዋቸው ፡ ነበር ።

ለያንዳንዳቸውም ፡ ሰው ፡ የቀረበው ፡ ሚኒው ፡ (የሙብል ፡ ማስታወቂያ)በቀኝ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ባንዲራ ፤ በግራ ፡ የጃፓን ፡ ባንዲራ ፤ የተደረገበት ፡ ነበር ።

በሻምፓኝም ፡ ጊዜ ፡ ክቡር ፡ ባሮን ፡ ሺዲሃራ ፡ ተነሥተው ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ያለውን ፡ ዲስኩር ፡ ተናገሩ ።

ክቡራን ፡ ሆይ ። የዛሬው ፡ ግብዣ ፡ ስለ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ልዩ ፡ መላክተኛ ፡ ስለ ፡ ክቡር ፡ ብላቴን ፡ ጌታ ፤ ኅሩይ ፡ ክብር ፡ መሆኑን ፡ አስቀድሜ ፡ አስታውቃለሁ ።

ከጥንት ፡ ከመሠረት ፡ ጀምሮ ፡ እንደ ፡ አንቲካ ፡ ሆኖ ፡ ሳያቋርጥ ፡ ተያይዞ ፡ የመጣው ፡ የነዚህ ፡ የሁለቱ ፡ ነገሥታት ፡ መጀመሪያ ፡ መገናኘት ፡ በጣም ፡ የሚያስደንቅ ፡ መሆኑን ፡ በግልጥ ፡ መናገር ፡ የተገባ ፡ ነው ።

ባለፈው ፡ ዓመት ፡ ግርማዊ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የዘውድ ፡ በዓላቸው ፡ በሚከብርበት ፡ ጊዜ ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መንግሥት ፡ እንደራሴ ፡ እንዲልክ ፡ በመልካም ፡ ፈቃዳቸው ፡ ስለ ፡ ጠሩ ፡ ምስተር ፡ ዩሺዳ ፡ ይህን ፡ የተከበረውን ፡ መልእክት ፡ ለመፈጸም ፡ በታላቅ ፡ ደስታ ፡ ተነሥቶ ፡ ሔዶ ፡ ነበር ። አሁን ፡ ደግሞ ፡ ክፍ ፡ ያሉት ፡ ትልቁ ፡ ገዥዎ ፡ ለታላቁ ፡ ጌታዬ ፡ ለጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የሚመልሱትን ፡ የከበረውን ፡ ምስጋናቸውንና ፡ መልእክታቸውን ፡ ለማቅረብ ፡ ክቡርነትዎ ፡ ተልከው ፡ መጥተው ፡ ዛሬ ፡ በመካከላችን ፡ ስለ ፡ አየንዎ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ ብሎናል ።

ይህም ፡ ከሙሉ ፡ ልባችን ፡ ያደረግንልዎ ፡ አቀባበል ፡ ደስ ፡ እንዲያሰኝዎ ፡ ፍጹም ፡ ምኞቴ ፡ ነውና ፡ ለኢትዮጵያና ፡ ለገዥዋ ፡ ለኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ክብር ፤ የሁለቱም ፡ ሕዝቦች ፡ ለዘላለም ፡ ወዳጆች ፡ ሆነው ፡ እንዲኖሩ ፡ እየተመኘሁ ፡ ስለ ፡ ግርማዊ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ጤና ፡ ጽዋዬን ፡ አነሣለሁ ፡ ብለው ፡ ሲጨርሱ ፡ ሁላችንም ፡ ጽዋችንን ፡ እያነሣን ፡ ቆመን ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሂም ፡ ናሺዮናል ፡ ተዘመረና ፡ ተቀመጥን ።

እኔም ፡ ሚኒስትሩ ፡ ለተናገሩት ፡ ዲሲኩር ፡ ምላሽ ፡ እንደ ፡ ደንቡ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ያለውን ፡ ቃል ፡ ተናገርሁ ።

ክቡር ፡ ሚኒስትር ፡ ሆይ ። የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ልዩ ፡ መላክተኛ ፡ ሆኜ ፡ መምጣቴን ፡ አክብረው ፡ ዛሬ ፡ ስለ ፡ አደረጉት ፡ ግብዣ ፡ ደስታዬን ፡ ስገልጽልዎ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ።



ክቡር ፡ ብላቴን ፡ ጌታ ፡ ኅሩይ ፡ በጃፓን ፡ የውጭ ፡ ጉዳይ ፡
ሚኒስትር ፡ ቤት ፡ ራት ፡ ተጋብዘው ፡ ዲስኩር ፡ ሲናገሩ ።



ክቡር ፡ ብላቴን ፡ ጌታ ፡ ኅሩይ ፡ ከጠቅላይ ፡ ሚኒስትሩ ፡ ከባሮን ፡ ዋካትሱኪና ፡
ከውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስትሩ ፡ ከባሮን ፡ ሺዲሐራ ፡ ጋራ ፡ ሲነጋገሩ ።

ሁለቱ ፡ ጥንታውያን ፡ ነገሥታት ፡ ሳይገናኙና ፡ ሳይቀራረቡ ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ ረጅም ፡ ዘመን ፡ ከኖሩ ፡ በኋላ ፡ ዛሬ ፡ በተገናኙበትና ፡ በተቀራረ ቡበት ፡ ጊዜ ፡ ልዩ ፡ መላክተኛ ፡ ሆኜ ፡ መምጣቴ ፡ ታላቅ ፡ እድል ፡ መ ሆኑ ፡ ለልቤ ፡ ይሰማኛል ።

ክቡርነትዎ ፡ አሁን ፡ እንደ ፡ ተናገሩት ፡ ባለፈው ፡ ዓመት ፡ ለግር ማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የዘውድ ፡ በዓል ፡ ልዩ ፡ አምባሳደር ፡ ሆነው ፡ ወደ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ የመጡት ፡ ምስተር ፡ ዮሺዳ ፡ የጃፓንን ፡ መንግ ሥት ፡ ትልቅነት ፡ የሕዝቡን ፡ ሥልጣኔ ፡ ነግረውኝ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ አሁን ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ መጥቼ ፡ ባይኔ ፡ ያየሁት ፡ ሁሉ ፡ ምስተር ፡ ዮሺዳ ፡ በቃል ፡ ከነገሩኝ ፡ አሥር ፡ እጅ ፡ በልጦ ፡ ስለ ፡ አገኘሁት ፡ በጣም ፡ ተደነቅሁ ።

ከእንግዲህም ፡ ወዲህ ፡ የሁለቱ ፡ መንግሥቶች ፡ የወዳጅነት ፡ ማሠ ሪያ ፡ እየጠበቀና ፡ ንግድ ፡ እየሰፋ ፡ እንዲሔድ ፡ በፍጹም ፡ ልቤ ፡ እመኛለሁ ።

ክቡር ፡ ሆይ ። ዛሬ ፡ በተደረገልኝ ፡ የክብር ፡ አቀባበል ፡ ክቡርነት ዎን ፡ እያመሰገንሁ ፡ ስለ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ ልማት ፡ ስለ ፡ ጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ጤና ፡ ጽዋዬን ፡ አነሣለሁ ፡ ብዬ ፡ ስጨርስ ፡ ሁሉም ፡ ጽዋቸ ውን ፡ አንሥተው ፡ ቆመው ፡ የጃፓን ፡ ሂም ፡ ናሺዮናል ፡ ተነፋና ፡ ከ ሙብል ፡ ቤቱ ፡ ወጥተን ፡ ወደ ፡ ቡን ፡ መጠጫው ፡ አዳራሽ ፡ ገባን ።

በዚያም ፡ ከጠቅላይ ፡ ሚኒስትሩ ፡ ከባሮን ፡ ዋካትሱኪ ፡ ጀምሮ ፡ አ ንዳንዱ ፡ ሚኒስትሮችና ፡ መኳንንቶች ፡ በየተራ ፡ እየቀረቡ ፡ መጀመሪያ ፡ የቶኪዮን ፡ ከተማ ፡ መውደዴንና ፡ ጤናዬን ፤ ቀጥሎም ፡ የኢትዮጵያን ፡ አኳኋን ፡ እየጠየቁኝ ፡ እስከ ፡ ፱ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ በደስታ ፡ አምሽተን ፡ ወደ ፡ ሆቴላችን ፡ ተመለስን

---

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

በኅዳር ፡ ፬ ፡ ቀን ፡ ከጧቱ ፤ በ፰ ፡ ሰዓት ፡ በንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ዱር ፡ ው ስጥ ፡ በቦይ ፡ በገባው ፡ ባሕር ፡ ውስጥ ፡ ዳክዮች ፡ ለማደን ስለ ፡ ተፈቀደ ልን ፡ ወደዚያ ፡ ሔድን ። የንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ግራንድ ፡ ማስተር ፡ አፍ ፡ ሴሬምኒውና ፡ ( ሊጋባው) ሌሎችም ፡ ከውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስትር ፡ አሥ ር ፡ ያህል ፡ መኳንንቶች ፡ ባልደረቦቻችን ፡ እነ ፡ ሙሴ ፡ ዋታናቤም ፡ ከኛው ፡ ጋራ ፡ ሔደው ፡ ነበር ።

ሙሴ ፡ ኩሮኪም ፡ በሆቴልም ፡ በሌላም ፡ ስፍራ ፡ ቢሆን ፡ ከ እኛ ፡ አይለዩም ፡ ነበር ። በቦይ ፡ የገባው ፡ ባሕርና ፡ የዳክዬዎቹ ፡ መር ባት ፡ በጣም ፡ የሚያስደንቅ ፡ ነው ።

ባሕሩ ፡ ከትልቁ ፡ ባሕርና ፡ ከሌላም ፡ ወንዝ ፡ በቦይ ፡ የገባ ፡ ነው ። ይህንም ፡ ካደረጉ ፡ በኋላ ፡ በውስጡ ፡ ዳክዬዎቹን ፡ አርብተዋቸዋል ፤ ከባሕሩ ፡ ቀጥሎ ፡ በያቅጣጫው ፡ አምሳ ፡ አምሳ ፡ ሜትር ፡ ያህል ፡ እ የተራራቀ ፡ ቦይ ፡ እየተቆፈረ ፡ በዳሩ ፡ ግንብ ፡ ገንብተው ፡ ግንቡን ፡ ባ ፈር ፡ ደልድለው ፡ ሣር ፡ አብቅለውበታል ። ዳክዬዎቹ ፡ በሺ ፡ ይቆጠ ሩ ፡ እንደሆነ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ባሥርና ፡ በመቶ ፡ አይቆጠሩም ። እንደ ዚህ ፡ ማለት ፡ ስለ ፡ ብዛታቸው ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ ሺ ፡ ዳክዬ ፡ እየተባ ለ ፡ ወደ ፡ ሚሊዮን ፡ ይቆጠራሉ ፡ እንጂ ፡ አሥር ፡ ወይም ፡ መቶ ፡ እ የተባሉ ፡ ወደ ፡ ሺ ፡ አይቆጠሩም ፡ ማለት ፡ ነው ።

ዳክዬዎቹ ፡ ከባሕሩ ፡ ቦይ ፡ ለቦይ ፡ በወጣው ፡ ውሀ ፡ እየተንሳፈፉ ፡ ወደ ፡ ግንቡ ፡ ሲመጡ ፡ ከግንቡ ፡ ውጭ ፡ በትንሽ ፡ ቀዳዳ ፡ እህልና ፡ ሌላም ፡ ነገር ፡ እየጣሉ ፡ አስለምደዋቸዋል ። ለነዚህም ፡ ጠባቂዎችና ፡ የዳክዬ ፡ አደን ፡ አስተማሪዎች ፤ ተደርጎላቸዋል ።

ዳክዬዎቹን ፡ መያዣው ፡ ሥራው ፡ እንደ ፡ ዓሣ ፡ መረብ ፡ ያለ ፡ አፉ ፡ ሰፊ ፡ የሆነ ፡ ባንድ ፡ በረጅም ፡ የቀርቀሃ ፡ ዘንግ ፡ ላይ ፡ የታሠረ ፡ የገ መድ ፡ ትብትብ ፡ ነው ። አደን ፡ አስተማሪው ፡ ካራት ፡ እስከ ፡ አሥር ፡ ሰዎች ፡ እየመረጠ ፡ ዳክዬዎቹ ፡ እንዳያዩዋቸው ፡ አድርጎ ፡ አምስቱን ፤ በግንቡ ፡ ቀኝ ፡ አምስቱን ፡ በግራ ፡ አቁሞ ፡ እርሱ ፡ በስተ ፡ ውጭ ፡ በግ ንቡ ፡ ቀዳዳ ፡ እየተመለከተ ፡ በቦዩ ፡ ውሀ ፡ ውስጥ ፡ የመጡትን ፡ ዳክዬዎ ች ፡ ይቆጥራል ። አሥር ፡ ዳክዬዎች ፡ መጥተው ፡ እንደሆነ ፡ አሥሩን ፡ ጣቶቹን ፡ አውጥቶ ፡ ያሳያል ። ከነዚህም ፡ ያነሡ ፡ ቢሆኑ ፡ በቍጥራቸው ፡ ልክ ፡ ጣቱን ፡ አውጥቶ ፡ ያሳያል ። እንደዚህም ፡ ማድረጉ ፡ ዳክዬዎቹ ፡ የሰው ፡ ድምጥ ፡ ሲሰሙ ፡ እየተመለሱ ፡ እንዳይሔዱ ፡ ነው ። ጣቶቹን ም ፡ አውጥቶ ፡ ካሳየ ፡ በኋላ ፡ አዳኞቹን ፡ ወደ ፡ ዳክዬዎቹ ፡ እንዲዞሩ ፡ በእጁ ፡ ያመለክታቸዋል ። እርሱ ፡ ግን ፡ ዳክዬዎቹ ፡ ወደ ፡ ባሕሩ ፡ እ ንዳይመለሱ ፡ በፍጥነት ፡ ሔዶ ፡ ወደ ፡ ባሕሩ ፡ መመለሻውን ፡ ቦይ ፡ በብ ረት ፡ ሽቦ ፡ ይዘጋዋል ። አዳኞቹም ፡ መረባቸውን ፡ እየያዙ ፡ ብቅ ፡ ሲሉ ፡ ዳክዬዎቹ ፡ እየደነገጡ ፡ ከውሀው ፡ ላይ ፡ ይነሣሉ ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ አዳ ኞቹ ፡ በፍጥነት ፡ በመረቡ ፡ እየጠለፉ ፡ ከአየሩ ፡ ላይ ፡ ይይዙዋቸዋል ። አ

ንድ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ማፍጠኑ ፡ ሁለትም ፡ ሶስትም ፡ ዳክዬዎች ፡ ይይዛል ። አንዳንዱ ፡ ግን ፡ በጭራሽ ፡ ሳይዝ ፡ ይቀራል ። ከሁሉም ፡ የሚያስደንቀው ነገር ፡ ዳክዬዎቹ ፡ ከአዳኞቹ ፡ አምልጠው ፡ በሔዱ ፡ ጊዜ ፡ ጠፍተው ፡ እንዳይቀሩ ፡ ተብሎ ፡ ለማዳ ፡ ጭልፊት ፡ በገመድ ፡ ተይዞ ፡ ይቀርብና ፡ አንዲቱ ፡ ዳክዬ ፡ አምልጣ ፡ በሔደች ፡ ጊዜ ፡ ጭልፊቱን ፡ ሲለቁት ፡ ከአየሩ ፡ ላይ ፡ ይዞ ፡ ያወርዳታል ። ስለ ፡ አወረዳትም ፡ በላይዋ ፡ ተቀምጦ ፡ ይቆያል ፡ እንጂ ፡ አይበላትም ። አለመብላቱም ፡ ስለ ፡ ተቀጣ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሳያምረው ፡ ቀርቶ ፡ አይደለም ።

ነገር ፡ ግን ፡ እርሱ ፡ የያዛቸው ፡ ዳክዬዎቹ ፡ ሁሉ ፡ ለብቻ ፡ ተጠራቅመው ፡ ቆይተው ፡ አደኑ ፡ ሲያልቅ ፡ ልብ ፡ ልባቸውን ፡ እያወጡ ፡ ይሰጡታል ። የእርሱ ፡ ሽልማቱና ፡ ጉርሻው ፡ ይህ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

ከእኛም ፡ ወገን ፡ ልጅ ፡ ተፈራና ፡ ልጅ ፡ አርአያ ፤ አቶ ፡ ዳባም ፡ አደራረጉን ፡ ገና ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ በማየታቸው ፡ ዳክዬዎቹን ፡ በመረቡ ፡ በመያዛቸው ፡ በዚያ ፡ ያሉት ፡ መኳንንቶች ፡ ተደነቁ ። ብዙ ፡ አውሮጶች ፡ እነዚህን ፡ ዳክዬዎች ፡ በመረብ ፡ ለማደን ፡ እያስፈቀዱ ፡ መያዙ ፡ እያስቸገራቸው ፡ ያዝናሉ ። እናንተ ፡ ግን ፡ ባንድ ፡ ቀን ፡ አይታችሁ ፡ ወዲያው ፡ መያዛችሁ ፡ ያስደንቃል ፡ እያሉ ፡ አመሰገኗቸው ።

በዚህም ፡ ቀን ፡ በመረብ ፡ የተያዙት ፡ ዳክዬዎች ፡ ፷፬ ፡ ናቸው ። እነዚህም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ሔደው ፡ ለየባለ ፡ ድርጎው ፡ ይታደላሉ ፡ ብለው ፡ ነገሩን ። ከነዚሁም ፡ ሀያውን ፡ ያህል ፡ ለእኛ ፡ ልከውልን ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ ያለንበት ፡ ስፍራ ፡ በሆቴል ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ለእኛ ፡ ምንም ፡ አያደርጉልን ፡ ብለን ፡ ለባልደረባችን ፡ ለሙሴ ፡ ኩሮኪ ፤ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ላክንለት ።

---

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

በኅዳር ፡ ፬ ፡ ቀን ፡ ኢምፔርያል ፡ ዩኒበርሲቲ ፡ የሚባለውን ፡ ለማየት ፡ ሔድን ። ኢምፔርያል ፡ ማለት ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ማለት ፡ ነው ።

ዩኒበርሲቲ ፡ ማለትም ፡ የሊቃውንት ፡ ትምሕርት ፡ ቤት ፡ ማለት ፡ ነው ። የሊቃውንት ፡ ትምሕርት ፡ ሲባል ፡ እንደ ፡ ሀገራችን ፡ የዜማ ፤ የቅኔ ፡ የመጻፍ ፡ ትርጓሜ አይደለም ። የዚህ ፡ ዩኒበርሲቲ ፡ ለብቻው ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ወገን ፡ ነው ። ይህ ፡ ግን ፡ የወታደርነት ፡ የዳኝነት ፡ የንግድ ፤ የእ

ርሻ ፤ የቀኍጥር ፤ በጠቅላላው ፡ የአሳብና ፡ የእጅ ፡ ሥራ ፡ መማሪያ ፡ ነው ። መማሪያ ፡ ነው ፡ ማለትም ፡ እንደ ፡ ሀገሩ ፡ ደንብ ፡ የማንም ፡ ልጅ ፡ ቢሆን ፡ ከ፯ ፡ ዓመቱ ፡ ጀምሮ ፡ በመጀመሪያ ፡ በታችኛው ፡ ትምሕርት ፡ ቤት ። ሁለተኛ ፡ በመካከለኛው ፡ ትምሕርት ፡ ቤት ፡ እየተማረ ፡ ትምሕርቱን ፡ ሲጨርስ ፡ ትምሕርቱን ፡ የሚመረምርበትና ፡ የሚያጠራበት ፡ አዋቂም ፡ ሆኖ ፡ ቢገኝ ፡ እገሌ ፡ ይህን ፡ ሥራ ፡ ለመሥራት ፡ ይችላል ፡ ተብሎ ፡ ምስክር ፡ የሚቀበልበት ፡ ማለት ፡ ነው ። እንደ ፡ ሀገራቸው ፡ ሕግ ፡ ማንም ፡ ቢሆን ፡ በዩኒበርሲቲ ፡ ገብቶ ፡ ተምሮና ፡ ተመርምሮ ፡ ትምሕርቱን ፡ አጣርቶ ፡ ይህን ፡ ሥራ፡ለመሥራት ፡ ይችላል ፡ የሚል ፡ የምስክር ፡ ወረቀት ፡ ካልተቀበለ ፡ ከመንግሥት ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ ዋና ፡ ሹም ፡ ለመሆን ፡ አይችልም ፡ ።

ይህም ፡ በቶኪዮ ፡ የተሠራው ፡ ኢምፔርያል ፡ ዩኒበርሲቲ ፡ የሚባለው ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ ካሉት ፡ ከሌሎቹ ፡ ዩኒበርሲቲዎች ፡ የሚበልጠው ፡ ነው ። በውስጡም ፡ የሚማሩ ፡ ልጆች ፡ በዚህ ፡ ዓመት ፡ ፰ሺ ናቸው ፡ አስተማሪዎቹም ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ናቸው ። ምናልባት ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ዝቅ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ከፍ ፡ ይል ፡ ይሆናል ።

ገንዘቡም ፡ በያመቱ ፡ ፬ ፡ ፭ ፡ ሚሊዮን ፡ ዬን፡ከመንግሥት፡ይከፈላል ። ደግሞ ፡ መንግሥት ፡ የመሬት ፡ ርስት ፡ ሰጥቷልና ፡ ከርስቱ ፡ ላይ ፡ የዛፍም ፡ ያታክልትም ፡ የሌላም ፡ ዓይነት ፡ ሽያጭ ፡ ሆኖ ፤ ተማሪዎቹም ፡ የሚከፍሉት ፡ ባንድነት ፡ ታስቦ ፡ ፫ ሚሊዮን ፡ ዬን ፡ ይገባል ፤ በድምሩ ፡ ያመቱ ፡ ገቢ ፡ ፯ ሚሊዮን ፡ ዬን ፡ ማለት ፡ ነው ።

ገንዘብ ፡ ከከፈለ ፡ ማንም ፡ የውጭ ፡ አገርም ፡ ልጅ ፡ ቢሆን ፡ እየገባ ፡ እንዲማር ፡ ተፈቅድዋል ። ይህንም ፡ ዩኒበርሲቲውን ፡ በየክፍሉ ፡ እያገቡ ፡ ካሳዩን ፡ በኋላ ፡ የምድር ፡ መናወጥ ፡ ወደ ፡ ሚመረመርበት ፡ ወሰዱን ።

የምድር ፡ መናወጥ ፡ ከእስያ ፡ ክፍል ፡ በጃፓን ፤ ከአውሮፓም ፡ ክፍል ፡ በኢጣልያ ፡ ይጸናል ። ይልቁንም ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ በጣም ፡ ይጸናል ፤ ምንም ፡ እንኳ ፡ ትልቅ ፡ ጉዳት ፡ ባያመጣ ፡ በየሳምንቱ ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ ምድር ፡ መናወጡ ፡ አይቀርም ፡ በየ፫ ፡ ወርና ፡ በየ፬ ፡ ወርም ፡ ጥቂት ፡ በርታ ፡ ያለ ፡ መናወጥ ፡ ይሆናል ። በ፫ ዓመትና ፡ ባራት ፡ ዓመት ፡ ግን ፡ ጥቂት ፡ ጉዳት ፡ የሚያመጣ ፡ የምድር ፡ መናወጥ ፡ ይደረጋል ። ስለዚህ ፡ ይህን ፡ የምድርን ፡ መናወጥ ፡ ነገር ፡ በዩኒበርሲቲ ፡ በጣም ፡ ለመመርመር ፡ ይጣጣሩበታል ።

የዛሬ ፡ ፶ዓመት፡ምስተር፡ ሚልን ፡ የሚባል ፡ የእንግሊዝ ፡ አገር ፡ ሊቅ፡ ለዚሁ ፡ ለምድር ፡ መናወጥ ፡ መመርመሪያ ፡ አንድ ፡ አዲስ ፡ መኪና፡ አውጥቶ ፡ አመራመሩን ፡ አስተምሮ ፡ ነበር ፤ አሁን ፡ ግን ፡ ራሳቸው ፡ ጃፓኖች፡ ያንኑ ፡ መሠረት ፡ አድርገው ፡ በጣም ፡ እያጣሩ ፡ ተምረው ፡ ያወቁ ፡ በቶኪዮ ፡ ዩኒበርሲቲ ፡ ብቻ ፡ አሥር ፡ ሊቃውንቶች ፡ ይገኛሉ ።

ስለዚህ ፡ በመላው ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ የምድር ፡ መናወጥ ፡ ያለበትን ፡ ሥፍራ ፡ መርምረው ፡ አግኝተው ፡ በካርታ ፡ ላይ ፡ በምልክት ፡ አስቀምጠውታል ። ኃይሉንም ፡ ገምተው ፡ ከዚህ ፡ አገር ፡ የሚነሣው ፡ እስከዚህ ፡ አገር ፡ በጣም ፡ ጉዳት ፡ ያመጣል ፤ እስከዚህ ፡ አገር ፡ ጥቂት ፡ ብቻ ፡ ይናወጣል ፡ እያሉ ፡ ጽፈውታል። ነገር ፡ ግን፡ በዚህ ፡ አገር ፡ ያለው ፡ የሚነሣው ፡ በዚህ ፡ ወር ፡ በዚህ ፡ ዓመት ፡ ነው ፡ ለማለት ፡ እስካሁን ፡ አልቻሉምና ፡ ገና ፡ ወደፊት ፡ ይመረምራሉ ።

በማናቸውም ፡ ቢሆን ፡ እንደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ቍጥር ፡ ፲፰፻፸፬ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ በ፵ ፡ ዓመት ፡ ውስጥ ፡ በምድር ፡ መናወጥ ፡ ምክንያት ፡ የሞቱት ፡ ሰዎች ፡ ፪፻፲፱ሺ ፡ ፯፻፳፬፡ናቸው። የፈረሱትም፡ ቤቶች ፡ ፩ ሚሊዮን ፡ ፩፲፯ሺ፯፻፵፫ ፡ ናቸው ። የጠፋው ፡ ገንዘብ ፡ ግን ፡ ይህን፡ ያህል ፡ ነው ፡ ለማለት ፡ አይቻልም ።

የሚመረምርበትም ፡ መኪና ፡ ከዚያው ፡ ከዩኒበርሲቲው ፡ ሳይወጣ ፡ እንደ ፡ ራዲዮ ፡ (የነፋስ ፡ ሥልክ ፡ )በዚህ ፡ ሥፍራ ፡ የምድር ፡ መናወጥ ፡ አለበት ፤ ሲናወጥም ፡ ከዚህ ፡ እስከዚህ ፡ ትልቅ ፡ ጉዳት ፡ ያመጣል ። ከዚህ ፡ እስከዚህ ፡ መንቀጥቀጥ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ጉዳት ፡ አያመጣም ፡ እያለ ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ። አደራረጉንና ፡ መመልከቱን ፡ ግን ፡ ከነዚያው ከሊቃውንቱ ፡ በቀር ፡ የሚያውቀው ፡ የለም ። የምድር ፡ መናወጥ ፡ መጀመሪያ ፡ የሚነሣበት ፡ ሥራ ፡ ቱርክስታን ፡ በሚባለው ፡ አገር ፡ ላይ ፡ ነው ፡ በማለት ፡ ሊስማሙበት ፡ ተቃርበዋል ፡ ይባላል ።

ከዚያም ፡ ወጥተን ፡ የመጽሐፍ ፡ ቤቱን ፡ ለማየት ፡ ወደ ፡ አንደኛው ፡ ቤት ፡ ገባን ። በዚህም ፡ ቤት ፡ ፳፻ሺ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ መጻሕፍት ፡ ነበሩበት ። ነገር ፡ ግን ፡ በ፲፱፻፲፬፡ ዓ ፡ ም ፡ በቶኪዮ ፡ ምድር ፡ በተናወጠ፡ ጊዜ ፡ ሁሉም ፡ ተቃጠሉና ፡ አመድ ፡ ሆኑ ። አሁን ፡ ግን ፡ ምስተር ፡ ሮኬሎሌር ፡ የሚባል ፡ አሜሪካዊ ፡ ፬ ሚሊዮን ፡ ዬን ፡ ሰጥቶ ፡ ቤቱ ፡ እንደገና ፡ ተሠራ ። ከያገሩም ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ እርዳታ ፡ ብዙ ፡ መጻሕፍት፡ ተላከልን ፡ ብሎ ፡ የመጻሕፍት ፡ ቤት ፡ ሹም ፡ ነገረን ። ስለ ፡ ኢትዮጵ

ያም ፡ ሙሴ ፡ ሬይ ፡ በጻፈው ፡ መጽሐፍ ፡ የግርማዊት ፡ ንግሥት ፡ ዘውዲቱና ፤ የግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ሥዕል ፡ ያለበትን ፡ ገጽ ፡ ገልጠው ፡ አኑረውት ፡ ይታያል ።

የዩኒበርሲቲውም ፡ አስተማሪዎች ፡ ምሳ ፡ ጋብዘውን ፡ ነበርና ፡ ምሳችንን ፡ ከበላን ፡ በኋላ ፡ የአይሮፕላን ፡ አኳኋን ፡ የሚመረመርበትን ፡ ለማየት ፡ ሔድን ። እንደ ፡ እኛ ፡ አሳብ ፡ አይሮፕላን ፡ ሲባል ፡ ባንድ ፡ ፋብሪካ ፡ ተሠርቶ ፡ ሰው ፡ ተቀምጦበት ፡ የሚበር ፡ ብቻ ፡ ይመስለን ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ እንኳን ፡ እኛና ፡ እነዚያውም ፡ አይሮፕላኑን ፡ የሚሠሩት፡ሰዎች ፡ የማያውቁት ፡ ትልቅ ፡ ምርምርና ፡ ፈተና ፡ መኖሩን ፡ ቢያሳዩን ፡ በጣም ፡ አደነቅን ።

በዚህም ፡ በአይሮፕላን ፡ መመርመሪያ፡ ቤት ፡ ያየነውን ፡ ሁሉ ፡ ብዙ የረቀቀ ፡ ብልሃት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ለመረዳት ፡ አልቻልሁምና ፡ ጥቂት ፡ የተረዳሁትን ፡ አንዳንዱን ፡ እጽፋለሁ ።

፩ኛ ። የነፋስ ፡ ማስነሻ ፡ መኪና ፡ ሠርተው ፡ ለዚያውም ፡ ትንሽ ፡ አይሮፕላን ፡ ሠርተው ፡ በነፋሱ ፡ ላይ ፡ ያስኬዱታል ። አስቀድሞ ፡ የነፋሱን ፡ ኃይል ፡ እየመዘኑ ፡ ነፋሱም ፡ ኃይሉ ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ ሲሆን ፡ አይሮፕላኑ ፡ ደኅና ፡ ይሔዳል ። ኃይሉ ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ ሲሆን ፡ ያግደዋል ። በዚህ፡ጊዜ፡ይህን ፡ መንገድ ፡ ትቶ ፡ ይህን ፡ መንገድ ፡ መያዝ ፡ ይሻላል ፡ እያሉ ፡ የነፋሱን ፡ ኃይል ፡ መርምረው ፡ ለአይሮፕላን ፡ ነጂዎች ፡ የሚያስተምሩበት ፡ ነው ።

፪ኛ ። ከአይሮፕላን ፡ ውስጥ ፡ አንድ ፡ ትንሽ ፡ ነገር ፡ ሲሰናከል ፡ ደውሎ ፡ የሚያሰማና ፡ ወዲያው ፡ሠራተኛው ፡(ሜካኒሲያው) እንዲያየው ፡ የሚያስተምር ፡ ነው ።

፫ኛው ። አይሮፕላኑ ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ሲወርድ ፡ አደጋ ፡ እንዳያገኘው ፡ እየተጠማዘዘ ፡ እንዲወርድ ፡ አወራረዱን ፡ የሚያመለክት ፡ ነው ።

የቀረውን ፡ የመኪናውን ፡ ምርመራ ፡ እንደዚህ ፡ ነው ፡ ብዬ ፡ ለመጻፍ ፡ ብዙ ፡ ይቸግረኛል ።

ይህንም ፡ ሁሉ ፡ ካየን ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ዲሬክተሩ ፡ ጽሕፈት ፡ ቤት፡ ገብተን ፡ ፊርማችንን ፡ በደብተር ፡ ላይ ፡ ፈርመን ፡ ወደ ፡ ማረፊያችን፡ ቤት ፡ ተመለስን ።



በዮኮሳካ ፡ ባሕር ፡ ዳር ፡ ያሉትን ፡ የጦር ፡ አይሮፕላኖች ፡
ለማየት ፡ ከጀኔራሉ ፡ ጋራ ፡ እንደ ፡ ተቀመጥን ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

በኅዳር ፡ ፫ ፡ ቀን ፡ ከጧቱ ፡ በ፫ ሰዓት ፡ ከቶኪዮ ፡ ተነሥተን ፡ የጦር ፡ መርከቦችና ፡ የጦር ፡ አይሮፕላኖች ፡ ለማየት ፡ ወደ ፡ ዮካሳካ ፡ ሔድን ። ካዋሳኪ ፡ ከሚባለው ፡ ከተማ ፡ ስንደርስ ፡ እግረ ፡ መንገዳችንን ፡ የኤሌክትሪክ ፡ ማብሪያ ፡ ብርጭቆ ፡ ወደ ፡ ሚሠራበት ፡ ፋብሪካ ፡ ገብተን ፡ አይተን ፡ ወዲያውም ፡ ምሳ ፡ ተጋብዘን ፡ ወጣን ።

ዮካሣካም ፡ በደረስን ፡ ጊዜ ፡ የጦር ፡ አይሮፕላኖች ፡ ሹሞችና ፡ ዋናው ፡ ጀኔራል ፡ ተቀበሉን ። በዚያም ፡ ሶስት ፡ አይሮፕላኖች ፡ በባሕሩ ፡ ላይ ፡ ተሽከርክረው ፡ ሲበሩ ፡ ካሳዩን ፡ በኋላ ፡ ከምድር ፡ የሚነሡትን ፡ የጦር ፡ አይሮፕላኖች ፡ ለማሳየት ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ሥፍራ ፡ ወሰዱን ። በደረስንም ፡ ጊዜ ፡ ሶስት ፡ አይሮፕላኖች ፡ ተነሥተው ፡ መብረር ፡ ጀመሩ ። አካሔዳቸውም ፡ አንደኛው ፡ ትንሽ ፡ ቀደም ፡ ብሎ ፥ ሁለቱ ፡ በስተኋላው ፡ ቀኝና ፡ ግራ ፡ ሆነው ፡ ሳይዛቡና ፡ ሳይቀዳደሙ ፡ በትክክል ፡ እየሆኑ ፡ ነው ። እነዚሁም ፡ አይሮፕላኖች ፡ አንድ ፡ አንድ ፡ መትረየስና ፡ ቦምብ ፡ ይዘው ፡ ሔደው ፡ አደጋ ፡ የሚጥሉባቸውና ፡ የሚዋጉባቸው ፡ ናቸው ። ቦምባውንም ፡ በማናቸውም ፡ ሥፍራ ፡ ሆነው ፡ ለመጣል ፡ ይችላሉ ። መትረየስ ፡ ሲተኩሱ ፡ ግን ፡ ጥቂት ፡ ወደ ፡ መሬት ፡ መቅረብ ፡ የሚያስፈልግ ፡ ስለሆነ ፡ በጣም ፡ እርቆ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ከወጣ ፡ በኋላ ፡ ተመልሶ ፡ ቁልቁል ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ቀርቦ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ አቀራረቡንና ፡ አተኳኰሱን ፥ ወደ ፡ ላይም ፡ መውጣቱን ፥ በአየርም ፡ ላይ ፡ ሆነው ፡ በጐድናቸው ፥ በጀርባቸውም ፥ በፊታቸውም ፥ እየተገለባበጡ ፡ ሲሔዱ ፡ አሳዩን ። በዚህም ፡ ሥፍራ ፡ የሚኖሩት ፡ የባሕር ፡ አይሮፕላኖች ፡ ሰማንያ ፡ አንድ ፡ ናቸው ። ሰላሣ ፡ አንዱ ፡ ግን ፡ አሁን ፡ ወደ ፡ ቻይና ፡ ባሕር ፡ ሔደዋል ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ከአይሮፕላኑ ፡ ጀኔራል ፡ ተሰነባብተን ፡ ናጋታ ፡ የተባለውን ፡ አንድ ፡ ትልቅ ፡ የጦር ፡ መርከብ ፡ ለማየት ፡ ሔድን ። ካፒቴኑም ፡ ከጥቂት ፡ ወታደሮች ፡ ጋራ ፡ ተሰልፎ ፡ ተቀበለን ፥ ወዲያውም ፡ በመርከቡ ፡ ላይ ፡ ያሉትን ፡ ስድስት ፡ ትልልቅ ፡ መድፎች ፡ በውጭ ፡ ካሳየን ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ውስጥ ፡ አግብቶ ፡ ጥይቱ ፡ ሲገባና ፡ ሲተኰስ ፡ እንደምን ፡ እንደሆን ፡ አሳየን ። ከዚህም ፡ በቀር ፡ ሌሎች ፡ አነስ ፡ አነስ ፡ ያሉ ፡ ስድስት ፡ መድፎች ፡ ወደ ፡ አየር ፡ ተደግነው ፡ አይሮፕላን ፡ ለማውረድ ፡

የሚጠባበቁ ፡ ናቸው ፡ ብለው ፡ አሳዩን ። በመርከቡም ፡ መካከል ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ በብረት ፡ የተሠራው ፡ የ፩ቁ ፡ ርዝመት ፡ እ፩ግ ፡ ያስደንቃል ። እንደዚህም ፡ በጣም ፡ አስረዝመው ፡ መሥራታቸው ፡ በጦርነት ፡ ጊዜ ፡ ካፒቴኑ ፡ በዚያ ፡ ላይ ፡ ሆኖ ፡ በባሕር ፡ የሚመጡትን ፡ የጠላቶች ፡ መርከቦች ፡ በሩቁ ፡ ለመጠባበቅ ፡ እንዲመቸው ፡ ተብሎ ፡ ነው ።

የመርከቡ ፡ ክብደት ፡ ፴፫ሺ፰፻ ፡ ቶን ፡ ነው ። በውስጡም ፡ ያሉት ፡ ወታደሮች ፡ አንድ ፡ ሺ ፡ አንድ ፡ መቶ ፡ ናቸው ። በዚህም ፡ በዮካማካ ፡ ባሕር ፡ አሁን ፡ ለጊዜው ፡ ያሉት ፡ የጦር ፡ መርከቦች ፡ ትንሹ ፡ ትልቁም ፡ ፭፰ ፡ ናቸው ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

ከዚህም ፡ ወጥተን ፡ ጃፓኖች ፡ ከመስኮቦች ፡ ጋራ ፡ የተዋጉ ፡ ጊዜ ፡ አድሚራል ፡ ቶጎ ፡ ተዋግቶ ፡ ድል ፡ ያደረገበትን ፡ ሚስካ ፡ የሚባለውን ፡ አርጌ ፡ የጦር ፡ መርከብ ፡ ለማየት ፡ ሔድን ። ይህም ፡ የጦር ፡ መርከብ ፡ አሥር ፡ ሺ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ቶን ፡ ነው ። የጦር ፡ አዛዥ ፡ የነበረው ፡ አድሚራል ፡ ቶጎ ፡ በጃፓንና ፡ በመስኮብ ፡ ጦርነት ፡ ጊዜ ፡ ለአገሩ ፡ በርትቶ ፡ የተዋጋ ፡ ነው ። ወታደሮቹንም ፡ ሲያጽናና ፡ ሁለትና ፡ ሶስት ፡ መንግሥቶች ፡ አንድ ፡ ላይ ፡ ሆነው ፡ ካልመጡብን ፡ ለአንድ ፡ ለመስኩብ ፡ መንግሥት ፡ ጃፓን ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ አትሸነፍምና ፡ አይዞዋችሁ ፡ እያለ ፡ ያበረታታቸው ፡ ነበር ።

ወደ ፡ ላይኛውም ፡ ደርብ ፡ አውጥተው ፡ ያንጊዜ ፡ ሲዋጉ ፡ ከጠላት ፡ ወገን ፡ የመድፍ ፡ ጥይት ፡ መርከቡን ፡ ይመታ ፡ ነበርና ፤ ሹማምንቶቹ ፡ ደህና ፡ ደህናውን ፡ ዕቃ ፡ እየያዙ ፡ ገብተው ፡ የተቀመጡበትን ፡ ትልቅ ፡ የብረት ፡ ድስት ፡ አሳዩን ። አድሚራል ፡ ቶጎ ፡ ግን ፡ ፩ግና ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በወለሉ ፡ ላይ ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ እየተመላለሰ ፡ መድፎቹን ፡ ያስተኩስ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ በዚያ ፡ ውስጥ ፡ አልገባም ፡ ነበር ፡ አሉን ። በዚያም ፡ ጊዜ ፡ መድፍ ፡ የመታው ፡ሥፍራ ፡ ሁሉ ፡ በመርከቡ ፡ ላይ ፡ በቀይ ፡ ቀለም ፡ ምልክት ፡ ተደርጎበታል ። አድሚራል ፡ ቶጎም ፡ መስኮቦችን ፡ ድል ፡ ሲያደርግ ፡ የመስኩብ ፡ ጄኔራል ፡ እንደ ፡ ቆሰለ ፡ ተማርኮ ፡ ወደ ዚህ ፡ መርከብ ፡ አምጥተው ፡ አስተኝተውት ፡ ነበርና ፡ በኋላ ፡ አድሚራል ፡ ቶጎ ፡ ቀርቦ ፡ እጁን ፡ ይዞ ፡ እንደ ፡ ጠየቀው ፡ አድርገው ፡ ሥለው ፡ በዚሁ ፡ መርከብ ፡ ውስጥ ፡ በመስተዋት ፡ አድርገው ፡ ሰቅለውታል ።

ደግሞ ፡ ያንጊዜ ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ተዋጉ ፡ የሚያሳይ ፡ ናፖሊዮንና ፡ ዱክ ፡ ውሊንግቶን ፡ እንደ ፡ ተዋጉበት ፡ እንደ ፡ ወተርሎ ፡ የመስታ



በዮኮሳካ ፡ ባሕር ፡ ያለው ፡ ናጋታ ፡ የሚባለው ፡ ትልቁ ፡ የጃፓን ፡ የጦር ፡ መርከብ ።

ወት ፡ ሥዕል ፡ ሆኖ ፡ ጦርነቱ ፡ የተጋጠመ ፡ መስሎ ፡ ይታያል ። ጦርነቱም ፡ ካለፈ ፡ ብዙ ፡ ዘመኑ ፡ ነው ። መርከቡ ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ድል ፡ አድራጊው ፡ ስለ ፡ አድሚራል ፡ ቶጎ ፡ መታሰቢያ ፡ ሆኖ ፡ እስካሁን ፡ በባሕሩ ፡ ዳር ፡ ተቀምጧል ።

ደግሞ ፡ ከመስኮቦች ፡ የተማረኩ ፡ ብዙ ፡ የመድፍ ፡ ጥይቶች ፡ ስለ ፡ መታሰቢያ ፡ በመርከቡ ፡ ላይ ፡ ተደርድረው ፡ ይታያሉ ።

አድሚራል ፡ ቶጎ ፡ ዛሬ ፡ እድሜው ፡ ፹፰ ፡ ዓመት ፡ ይሆናል ። እስካሁንም ፡ ድረስ ፡ ገና ፡ በሕይወት ፡ አለ ። ይህም ፡ አሮጌ ፡ የጦር ፡ መርከብ ፡ መጨረሻ ፡ ከእንግሊዝ ፡ አገር ፡ ተገዝቶ ፡ የመጣ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ያንጊዜ ፡ ጃፓን ፡ መርከብ ፡ መሥራትን ፡ አልለመደችም ፡ ነበር ።

ከዚያ ፡ ወዲህ ፡ ግን ፡ የጃፓን ፡ ልጆች ፡ በትምህርትና ፡ በእውቀት ፡ እየሰለጠኑ ፡ ስለ ፡ ሔዱ ፡ የጦር ፡ መርከባቸውን ፡ እነርሱ ፡ ይሠራሉ ፡ እንጂ ፡ ከውጭ ፡ አገር ፡ መግዛት ፡ ትተዋል ፡ ብሎ ፡ እዚያ ፡ ያለው ፡ የመርከቡ ፡ ካፒቴን ፡ ነገረን ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ቶኪዮ ፡ ተመለስን ።

---

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

የጃፓንን ፡ መሬት ፡ ከረገጥንበት ፡ ከጥቅምት ፡ ፳፰ ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ኅዳር ፡ ፩ ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ሙሉ ፡ በተለየ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ እንግዶች ፡ ሆነን ፡ሰንብተን ፡ ነበርን ። አሁን ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ሀገራቸው ፡ ልማድ ፡ በተለየ ፡ የመንግሥቱ ፡ እንግዶች ፡ ሆነን ፡ ፳፬ ፡ ቀን ፡ እንድንቀመጥ ፡ ስለ ፡ ተወሰነ ፡ በ፳፬ቱ ፡ ቀኖች ፡ ውስጥ ፡ እየዞርን ፡ የምናየውን ፡ የሚያስታውቅ ፡ ፕሮግራም ፡ ባልደረባችን ፡ ሙሴ ፡ ኩሮኪ ፡ ከውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስቴር ፡ አምጥቶ ፡ ሰጠን ። በዚሁም ፡ በ፳፬ቱ ፡ ቀን ፡ ውስጥ ፡ እንደ ፡ ፕሮግራሙ ፡ ቃል ፡ በያገሩ ፡ ስንዛወር ፡ በልዩ ፡ ባቡር ፡ እንድንዛወር ፡ በየደረስንበትም ፡ ስፍራ ፡ አገረ ፡ ገዥዎችና ፡ ባለ ፡ ሥልጣኖች ፡ ሹሞች ፡ ሁሉ ፡ በክብር ፡ እንዲቀበሉን ፡ ታዞልን ፡ ነበር ። ስለዚህ ፡ የጃፓን ፡ ወታደሮች ፡ እርሳስ ፡ በሌለበት ፡ የጦር ፡ መሣሪያ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ እየተዋጉ ፡ የጦርነት ፡ ሥራ ፡ የሚያሳዩበትን ፡ ለማየት ፡ በኅዳር ፡ ፬ ፡ ቀን ፡ ከጧቱ ፡ በ፫ ፡ ሰዓት ፡ ወደ ፡ አሚያ ፡ ሔድን ።

የጃፓን ፡ መንግሥት ፡ አሁን ፡ ማናቸውንም ፡ አሳቡንና ፡ ኃይሉን ፡ ሁሉ ፡ በወታደር ፡ ትምሕርት ፡ ላይ ፡ አድርጎታል ። ሌላውስ ፡ ይቅርና፡ በ

መጀመሪያ ፡ ትምሕርት ፡ ቤት ፡ ለሚማሩት ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ አንዳንድ ፡ የወታደር ፡ አለቃ ፡ እየገባ ፡ የወታደርነት ፡ ትምሕርት ፡ እንዲያስተምር ፡ ተደንብቷል ። የጦር ፡ መሣሪያ ፡ ፋብሪኮችም ፡ የጠመንጃው ፡ የመትረየሱም ፤ የመድፉም ፤ የጦር ፡ አይሮፕላን ፤ የታንኩ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ በትጋት ፡ ተይዟል ። ወታደሮች ፡ ሁሉ ፡ በየሰፈራቸው ፡ በሳምንት ፡ በሳምንት ፡ እኩሉ ፡ እንደ ፡ ጠላት ፡ እየሆኑ ፡ እየመጡ ፤ እኩሉም ፡ ተከላካዮች ፡ እየሆኑ ፡ እንደ ፡ ጦርነት ፡ ጊዜ ፡ አደጋ ፡ መጣልና ፡ መዋጋት ፡ ይማራሉ ።

በመት ፡ በመት ፡ ግን ፡ መላው ፡ የጃፓን ፡ ወታደር ፡ ከሁለት ፡ እየተከፈለ ፡ እርሳስ ፡ በሌለበት ፡ ጠመንጃና ፡ መትረየስ ፡ እርስ ፡ በርሱ ፡ እየተዋጋ ፡ የጦርነት ፡ አኳኋን ፡ እያሳየ ፡ ይፈተናል ።

ምሳሌ ። አምስት ፡ ደጃዝማቾች ፡ ባንድ ፡ ወገን ፡ ሆነው ፡ ከአዲስ ፡ ዓለም ፡ እስከ ፡ መናገሻ ፡ ይሰለፋሉ ። ደግሞ ፡ አምስት ፡ ደጃዝማቾች ፡ ባንድ ፡ ወገን ፡ ሆነው ፡ ከአዲስ ፡ አበባ ፡ እስከ ፡ ገፈርሳ ፡ ይሰለፋሉ ። ሲሰለፉም ፡ አንዱ ፡ ደጃዝማች ፡ ፳ ፡ ወይም ፡ ፴ ፡ ኪሎ ፡ ሜትር ፡ እየተራራቁ ፡ አንዱ ፡ ላንዱ ፡ ደጀን ፡ እየሆኑ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በንድነት ፡ አይሰለፉም ። የመጀመሪያው ፡ ደጃዝማች ፡ ከጠላት ፡ ጋራ ፡ ተዋግቶ ፡ ድልም ፡ ቢያደርግ ፡ ድልም ፡ ቢሆን ፡ ወደኋላው ፡ ተመልሶ ፡ ከደጀኑ ፡ ጋራ ፡ የሚገናኝበትን ፡ ኀይልና ፡ ማቋረጫ ፡ መንገድ ፡ ያስባል ፡ እንጂ ፡ ድል ፡ ካደረግሁ ፡ ወደፊት ፡ ልሒድ ፡ አይልም ።

ማስረጃ ። ድልም ፡ ቢያደርግ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ብዙ ፡ ወታደሮቹ ፡ ሳይሞቱበት ፤ ባይሞቱበትም ፡ መዳከማቸው ፡ አይቀርምና ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ የሚጠብቀውን ፡ ጠላት ፡ ብቻውን ፡ ድል ፡ ለማድረግ ፡ አይችልም ፡ ተብሎ ፡ ነው ።

ድልም ፡ ቢሆን ፡ ሁሉም ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ አያልቁምና ፡ የተረፉት ፡ ከደጀናቸው ፡ ጋራ ፡ ተቀላቅለው ፡ በንድነት ፡ እንዲዋጉ ፡ ነው ። እርሳስ ፡ ብቻ ፡ የለበትም ፡ እንጂ ፡ ያደጋ ፡ አጣጣሉም ፡ የመድፉም ፡ የመትረየሱም ፡ ተኵሰና ፡ ጉዞ ፡ ልክ ፡ እንደ ፡ ጦርነት ፡ ጊዜ ፡ ነው ።

የአደጋ ፡ አጣጣሉንና ፡ ያሰላለፉን ፡ ያተኳኰሱንና ፡ ያቀራረቡን ፡ ሁሉ ፡ የሚመረምሩ ፡ በጣም ፡ የጦርነት ፡ ሥራ ፡ ያወቁ ፡ ጀኔራሎች ፡ ከሁለቱም ፡ ሰልፍ ፡ ወገን ፡ ተመርጠው ፡ እየዞሩና ፡ እያዩ ፡ መቸም ፡ ሁሉም ፡ ለመንግሥታቸው ፡ ጥቅም ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እነእገሌ ፡ ድል ፡ ሆኑ ፡ እነእገሌ ፡ ድል ፡ አደረጉ ፡ በማለት ፡ አድልዎ ፡ የለባቸውምና ፡ ጦር



በኦሚያ ፡ ሰልፍ ፡ ጊዜ ፡ ከጦር ፡ አለቆች ፡ ጋራ ፡ እንደ ፡ ተገናኘን ።

ነቱ ፡ ካለቀ ፡ በኋላ ፡ የወዲያኛውና ፡ የወዲህኛው ፡ ሰልፍ ፡ መርማሪዎች ፡ ባንድነት ፡ ተገናኝተው ፡ ራፖር ፡ ያደርጋሉ ።

ይኸውም ፡ አደራረግ ፡ ጊዜ ፡ አጋጥሞን ፡ እኛ ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ በደረስንበት ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡ መሆኑ ፡ ለማየቱ ፡ የተመቸ ፡ ጊዜ ፡ ሆኖልን ፡ ነበር። ግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ግን ፡ ኩማሞቶ ፡ በሚባል ፡ አገር ፡ ፸፻ ፡ ወታደር ፡ የጦርነት ፡ ሥራ ፡ የሚያሳይበትን ፡ ለማየት ፡ ሲሔዱ ፡ የሔዱበት ፡ አገር ፡ ከቶኪዮ ፡ እጅግ ፡ የራቀ ፡ ስለሆነ ፡ እኛ ፡ ከቶኪዮ ፡ ፩ ፡ ሰዓት ፡ ብቻ ፡ በሚወስድ ፡ በአሚያ ፡ አገር ፡ ፵፻ ፡ ወታደር ፡ የጦርነት ፡ ሥራ ፡ የሚያሳይበትን ፡ እንድናይ ፡ አዘውልን ፡ ነበር ። በ፰ሰዓት ፡ የባቡር ፡ ዋገኑንና ፡ ሐር ፡ የሚሠራባቸውን ፡ ፋብሪኮች ፡ እግረ ፡ መንገዳችንን ፡ አይተን ፡ በ፯ሰዓት ፡ ወታደሩ ፡ ለጦርነት ፡ ወደ ፡ ሚኀዝበት ፡ ሥፍራ ፡ ደረስን ።

በዚያም ፡ ስድስት ፡ የወታደር ፡ አለቆች ፡ መጥተው ፡ ከተቀበሉን ፡ በኋላ ፡ ወታደሩ ፡ ሲኀዝ ፡ በሚታይበት፡ከፍ ፡ ባለ ፡ ሥፍራ ፡ አስቀመጡን ። ከ፯ሰዓት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሰዓት ፡ ወታደሩ ፡ በያለቃው ፡ ሲኀዝ ፡ አይተን ፡ በማግሥቱ ፡ ጧት ፡ የመጨረሻው ፡ ጦርነት ፡ ወደሚታይበት ፡ ስፍራ ፡ ሔድን ። የምንሔደውም ፡ በሰልፉ ፡ መከከል ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ መድፉም ፡ መትረየሱም ፡ ጠመንጃው ፡ ይተኰስ ፡ ነበርና ፡ መተላለፊያ ፡ እየቸገረን ፡ አውቶሞቢላችን ፡ ከ፫ ፡ እስከ ፡ ፭ ፡ ደቂቃ ፡ በመንገድ ፡ ላይ ፡ ይቆም ፡ ነበር ። የጦርነቱም ፡ ድል ፡ የሚታየው ፡ በማግሥቱ ፡ ጧት ፡ባንድ ፡ ሰዓት ፡ ነበርና ፡ ከሌሊቱ ፡ በ፲፩ ፡ ሰዓት ፡ ካደርንበት ፡ ሥፍራ ፡ ተነሥተን ፡ ሔድን ።

ከባላገሩም ፡ ወንዱም ፡ ሴቱም ፡ የድሉን ፡ መጨረሻ ፡ ለማየት ፡ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ ሲኀዝ ፡ አድሮ ፡ ነበርና ፡ የአቶሞቢል ፡ መተላለፊያ ፡ መንገድ ፡ ቸግሮን ፡ በብዙ ፡ ድካም ፡ ከስፍራው ፡ ደረስን ።

ከአንድ ፡ ሰዓት ፡ ጀምረው ፡ እስከ ፡ ሶስት ፡ ሰዓት ፡ በመድፍም ፤ በመትረየስም ፤ በጠመንጃም ፡ እየተታኰሱ ፡ ቆይተው ፡ በመጨረሻው ፡ ተቃረቡና ፡ በሳንጃ ፡ የመዋጋት ፡ ጦርነት ፡ አሳይተው ፡ ሲጨርሱ ፡ ጥሩምባ ፡ ተነፋና ፡ ጦርነቱ ፡ ቆመ ።

ወዲያውም ፡ የሁለቱም ፡ ወገኖች ፡ ጀኔራሎች ፡ ወደ ፡ እኛ ፡ እየመጡ ፡ ሰላምታ ፡ ሰጡን ። የሰልፉንና ፡ የጦርነቱንም ፡ አኳኋን ፡ ስለ ፡ ማየታችን ፡ አመሰገኑን ።

ምዕራፍ ፣ ፲፬

በኅዳር ፣ ፩ ፣ ቀን ፣ በሚሊታሪ ፣ ክለብ ፣ ለራት ፣ ተጠርተን ፣ ነበርና ፣ ወደዚያ ፣ ሔድን ። ይህንም ፣ ክለብ ፣ ያቆሙ ፣ ሰዎች ፣ የሚበዙት ፣ በጦር ነት ፣ ሥራ ፣ መንግሥታቸውን፣ሲያገለግሉ ፣ ኖረው ፣ ስለደከሙ ፣ አሁን ፣ የማያደክም ፣ ትንሽ ፣ ሥራ ፣ እየሠሩ ፣ የሚበቃ ፣ የመጦሪያ ፣ ደሞዝ ፣ እየ ተቀበሉ ፣ በደስታ ፣ የሚኖሩ ፣ ናቸው ።

ከነዚህም ፣ በቀር ፣ ፕሮፌሰሮች፣ (አስተማሪዎች፣)ሚኒስትሮችም ፣ ከነ በሩት ፣ ወገንና ፣ ሌሎችም፣ያገር ፣ ትልልቆች ፣ ሰዎች ፣ ናቸው።ስለ፣እኛም፣ ክብር፣በዚህ፣ቀን ፣ ለራት ፣ የተሰበሰቡት፣ሰዎች፣ቊጥራቸው፣፫፻፩፣ነበር ።

እነዚህም ፣ ትልልቆች ፣ ሰዎች ፣ ስለ ፣ ኢትዮጵያ ፣ መንግሥት ፣ ክብ ር ፣ ሲሉ ፣ ሚሊታሪ ፣ ክለብ፣ የሚባለውን ፣ ቤት፣ በውጭም ፣ በግቢም፣ በኢትዮጵያና ፣ በጃፓን ፣ ባንዴራ ፣ አስጊጠው ፣ ይጠብቁን ፣ ነበርና ፣ በደረስን፣ጊዜ፣ዳር፣እስከ ፣ ዳር ፣ አጨበጨቡ ። የመብሉም ፣ ገበታ ፣ ስስ ት ፣ አውራጃ ፣ ነበር ። በራትም ፣ ላይ ፣ አራት ፣ ሰዎች ፣ በየተራ ፣ እ የተነሡ ፣ ዲስኩር ፣ ተናገሩ ። ከነዚሁም ፣ አንዱ ፣ አድሚራል ፣ አሪማ፣ የሚባለው ፣ የተናገረው ፣ ከዚህ ፣ ቀጥሎ ፣ ያለው ፣ ነው ።

ክቡር ፣ ሆይ ። እርስዎንና ፣ ከርስዎ ፣ ጋራ ፣ ያሉትን ፣ ሰዎች ፣ በራ ሴና ፣ በጃፓን ፣ ሕዝብ ፣ ስም ፣ ሆኜ ፣ እንኳን ፣ ደህና ፣ መጣችሁ ፣ ለ ማለት ፣ የተመቸ ፣ ጊዜ ፣ ማግኘቴ ፣ ለእኔ ፣ ትልቅ ፣ ክብር ፣ ነው ።

የኢትዮጵያና ፣ የጃፓን ፣ አኳኋን ፣ በብዙ ፣ ወገን ፣ ይመሳሰላል ።

፩ኛ ። የኢትዮጵያ ፣ ነገሥታትና ፣ የጃፓን ፣ ነገሥታት ፣ ዘራቸው ፣ ከብዙ ፣ ሺህ ፣ ዘመን ፣ ጀምሮ ፣ ሳያቋርጥ ፣ ተያይዞ ፣ የመጣ ፣ በመሆኑ፣ ነው ። የነገሥታቶቻችንም ፣ ዘር ፣ ሳያቋርጥ ፣ ተያይዞ ፣ የመጣ ፣ በመሆ ኑ ፣ እኛ ፣ ጃፓኖች ፣ እንኰራበታለንና ፣ አሁን ፣ ደግሞ ፣ እንደዚሁ ፣ በ ነገሥታቶቻቸው ፣ ዘር ፣ ጥንታዊነት ፣ የሚኰሩ ፣ ሌሎች ፣ ሰዎች ፣ መገ ኘታቸው ፣ የምስራች ፣ የሚያሰኝ ፣ ነገር ፣ ነው ። ሳያቋርጥ ፣ ተያይዞ ፣ የመጣ ፣ የነገሥታት ፣ ትውልድ ፣ ለመንግሥቱ፣ ኃይል ፣ ለሕዝቡም ፣ ክብር ፣ መሆኑ ፣ የማይጠረጠር ፣ ነው ።

በሌላውም ፣ ወገን ፣ ሁለቱም ፣ መንግሥቶች ፣ ጃፓን ፣ በእስያ ፣ ኢ ትዮጵያ ፣ በአፍሪቃ ፣ የታወቁ ፣ በመሆናቸው ፣ ለሁለቱም ፣ መንግሥቶ ች ፣ ሕዝብ ፣ እጅግ ፣ ደስ ፣ የሚያሰኝ ፣ ነው ።



የጃፓን ፡ መኳንንቶች ፡ በሚሊታሪ ፡ ክለብ ፡ ራት ፡ እንደ ፡ ጋበዙን ።

፪ኛ ። በአፍሪቃ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ለማንም ፡ ሳትገዛ ፡ ነጻነቷን ፡ ጠብቃ ፡ እንድትኖር ፡ በእስያም ፡ ጃፓን ፡ ነጻነቷን ፡ ጠብቃ ፡ ለማንም ፡ ሳትገዛ ፡ በመኖሯ ፡ ከኢትዮጵያ ፡ ጋራ ፡ ትመሳሰላለች ።

በአፍሪቃ ፡ ሊቤሪያ ፡ የምትባለው ፡ አገር ፡ ምንም ፡ ነጻነት ፡ አላት ፡ ቢባል ፡ ባንድ ፡ በኃይለኛ ፡ መንግሥት ፡ ውስጥ ፡ ጥገኛ ፡ ሆና ፡ ትኖራለች ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ሙሉ ፡ ነጻነት ፡ የላትም ።

፫ኛ ። የኢትዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ በመንፈሳቸውና ፡ በሀሳባቸው ፡ ኃይል ፡ የዚህን ፡ የጃፓንን ፡ አገር ፡ ሕዝብ ፡ ይመስላሉ ።

እነዚህም ፡ በብዙ ፡ ወገን ፡ የሚመሳሰሉት ፡ መንግሥቶች ፡ አሁን ፡ በኋለኛው ፡ ዘመን ፡ ወደ ፡ ዲፕሎማቲክ ፡ ወዳጅነት ፡ ደርሰው ፡ የንግድ ፡ ውል ፡ መዋዋላቸው ፡ ትልቅ ፡ የምስራች ፡ የሚያሰኝ ፡ ነው ።

ይህንንም ፡ ወዳጅነት ፡ ለማጽናትና ፡ ለማስፋት ፡ ሲሉ ፡ ግርማዊ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ክቡርነትዎን ፡ ልዩ ፡ መላክተኛ ፡ አድርገው ፡ ስለ ፡ ላኩዎ ፡ እኛ ፡ የጃፓን ፡ ሕዝብ ፡ ባንድነት ፡ ሆነን ፡ ከጥልቅ ፡ ልባችን ፡ እንኳን ፡ ደህና ፡ መጡ ፡ እንልዎታለን ።

ኢትዮጵያ ፡ የጃፓንን ፡ ወዳጅነት ፡ ለማጽናትና ፡ ለማስፋት ፡ ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ ሀሳብ ፡ እንዳላት ፡ ከብዙ ፡ ሰዎች ፡ ሰምተናል ። ጃፓንም ፡ እንደዚሁ ፡ የኢትዮጵያ፡ ወዳጅነት ፡ ይሰማታልና ፡ ትልቅነትና ፡ እውቀት፡ ባገራችሁ ፡ እየሰፋ ፡ እንዲሔድ ፡ እየተመኘን ፡ በታሪክና ፡ በጠባይ ፡ ሁለቱ ፡ ሕዝቦች ፡ ይመሳሰላሉ ፡ ያልንበት ፡ ዋናው ፡ ነገር ፡ ስለዚህ ፡ ነው ።

ክቡር ፡ ሆይ ። የዛሬውም ፡ ማታ ፡ ግብዣችንና ፡ አቀባበላችን ፡ የኢትዮጵያን ፡ ወዳጅነት፡መፈለጋችንን፡ የሚያስረዳ ፡ ነው። ወደ ፡ አገርዎም፡ በተመለሱ ፡ ጊዜ ፡ መንግሥታችንም ፡ ሕዝባችንም ፡ በመልካም ፡ እንደተቀበልንዎ ፡ በሁለቱም ፡ አገሮች ፡ መካከል ፡ ወዳጅነት ፡ እንዲጸና ፡ ምኞታችንና ፡ ሀሳባችን፡መሆኑን ፡ ለወገኖችዎ፡ እንዲያስረዱልን፡ ተስፋ፡ አለን።

ይህንን ፡ ምክንያት ፡ አድርጌ ፡ ባንዛይ ፡ ባንዛይ ፡ ባንዛይ ፡ እያልሁ ፡ ስለ፡ኢትዮጵያ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት፡ጤና፡ ጽዋዬን፡ አነሣለሁ። ብሎ ፡ጨረሰ።

ባንዛይ ፡ ማለት ፡ እሰይ ፡ (ሁሬ ፡ )እንደ ፡ ማለት ፡ ነው ። እኔም ፡ ለዲስኩሩ ፡ ምላሽ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ያለውን ፡ ቃል ፡ ተናገርሁ ።

ክቡራን፡ታላላቆች፡መኳንንቶችና፡ፕሮፌሰሮች፡ሆይ።የኢትዮጵያ፡ምሥራቅ ፡ ወደምትሆን ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ መጥቼ ፡ ዛሬ ፡ ማታ ፡ በመካከላችሁ ፡ በመሆኔ ፡ ደስታዬ ፡ ከልክ ፡ ያለፈ ፡ ነው ። ኢትዮጵያና ፡ጃፓን ፡ በነገ

ሥታቱ፡ዘር፡ጥንታዊነት ፤ በሕዝቡም ፡ ልማድና ፡ ጅግንነት ፡ መመሳሰላቸ ው፡ን፡አሁን፡አድሚራል፡አሪማ፡ተናግረው፡ታልና፡እውነት፡ነው ፡ብዬ፡ነገራቸው ን፡ከማጽደቅ፡በቀር፡ሌላ ፡ ነገር ፡ለመጨመር፡አለማስፈለጉን፡ አስረዳችኋለሁ።

የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ ከተመሠረተ ፡ ዘመኑ ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ነውና ፡ ከሥሩ ፡ ጀምሬ ፡ ፡ ታሪኩን ፡ ለመናገር ፡ ሰዓቱ ፡ አይበቃንም ። ስለዚህ ፡ ከገናናዋና ፡ ከስመ ፡ ጥሩዋ ፡ ከንግሥተ ፡ ሳባ ፡ አስቀድሞ ፡ የነ በረውን ፡ ዘመን ፡ ትቼ ፡ ከንግሥተ ፡ ሳባ ፡ ወዲህ ፡ ያለውን ፡ ዘመን ፡ ሁ ለት ፡ ሺ፱፻፳፬ ፡ ነው ፡ ብዬ ፡ ስነግራችሁ ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ነገሥት ፡ ጂሙ ፡ ትዝ ፡ እንዲላችሁ ፡ እርግጥ ፡ ነው ። የጃፓን ፡ መንግሥት ፡ ጥንታዊና ፡ የ ሕዝቡ ፡ መኩሪያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ጂሙ ፡ እንደሆነ ፡ የኢትዮጵያም ፡ መንግሥት ፡ ጥንታዊና ፡ የሕዝቡ ፡ መኩሪያ ፡ ንግሥተ ፡ ሳባ ፡ ናት ። የ ዛሬው ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ግርማዊ ፡ ሂሮሂቶ ፡ ለጂሙ ፡ ፻፳ ፬ተኛ ፡ እንደሆኑ ፡ የዛሬውም ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ግርማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ለንግሥተ ፡ ሳባ ፡ ፻፳፮ተኛ ፡ ናቸው ። የእነዚህም ፡ የሁ ለቱ ፡ ነገሥታት ፡ ዘር ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ እንኳ ፡ ሳያቋርጥ ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ ተያይዞ ፡ የመጣ ፡ መሆኑን ፡ የሁለቱም ፡ አገሮች ፡ ታሪክ ፡ ይመሰክራል ።

በዚህም ፡ ባለፈው ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፲፰፻፳ ፡ ዓመ ፡ ምሕ ፡ በ ኢትዮጵያ ፡ እንደ ፡ ዛሬ ፡ ዘመን ፡ መድፍና ፡ ጠመንጃ ፡ አልነበረምና ፡ የኢትዮጵያ ፡ ነገሥታትና ፡ አርበኞች ፡ ጦር ፡ እየወረወሩ ፤ ጐራዴ ፡ እየ መዘዙ፤ጋሻ ፡ እየመከቱ፡አገራቸውን፡ከጠላት ፡ ጠብቀው ፤ ነጻነቷን ፡አጽን ተው ፡ ለእኛ ፡ ለኋላ፡ልጆች፡ማቆየታቸውን፡ስነግራችሁ፡በቀድሞ ፡ዘመን፡ የነበሩት ፡ የጃፓን ፡ ነገሥታትና፡አርበኞች፡ትዝ፡ ሳይሏችሁ ፡ አይቀሩም።

እነዚህም ፡ በብዙ ፡ ነገር ፡ የሚመሳሰሉት ፡ የሁለቱ ፡ አገሮች ፡ ነገሥ ታትና ፡ ሕዝብ ፡ ሳይተዋወቁ ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ ዘመን ፡ መኖራቸው ፡ እ ጅግ ፡ የሚያስደንቅ ፡ ነው ። የዚህንም ፡ ምሳሌ ፡ በዓይኖቻችን ፡ ለመመ ሰል ፡ ይቻላል ። ዓይኖቻችን ፡ ቅርብ ፡ ለቅርብ ፡ ሆነው ፡ ሌላውን ፡ ሁሉ ፡ ሲያዩ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ሳይተያዩ ፡ ይኖራሉ ። ነገር ፡ ግን ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ በመስታወት ፡ ለመተያየት ፡ ይችላሉና ፡ ያሁኑ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ መ ስታወት ፡ ሆኖ ፡ የሁለቱ ፡ አገሮች ፡ ጥንታውያንና ፡ ትልልቆች ፡ ነገሥ ታት ፡ የወዳጅነትና ፡ የንግድ ፡ ውል ፡ ስለ ፡ ተዋዋሉ ፡ ተቃርበንና፡ ተገናኝ ተን ፡ ባንድ ፡ ገበታ ፡ ተቀምጠን ፡ ለመጋበዝ ፡ ደርሰናልና ፡ እስካሁን ፡ሳን ገናኝ ፡ በመቆየታችን ፡ ልናዝንበት ፡ አይገባንም ።

ክቡር ፡ አድሚራል ፡ ሆይ ። እኛን ፡ ዛሬ ፡ በመካከላችሁ ፡ ሆነን ፡ እንዳያችሁን ፡ ከእናንተም ፡ ወገን ፡ ትልልቅ ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ኢትዮጵ ያ ፡ መጥተው ፡ በመካከላችን ፡ እንድናያቸው ፡ የልቤን ፡ ምኞት ፡ እየ ገለጥሁ ፡ ስለ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ ልማት ፤ ስለ ፡ ጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ጤና ፡ ጽዋዬን ፡ አነሣለሁ ፡ ብዬ ፡ ስጨርስ ፡ ዳር ፡ እስከ ፡ ዳር ፡ ተጨ በጨበና ፡ ባንድነት ፡ ፎቶግራፍ ፡ ተነሥተን ፡ ከሌሊቱ ፡ በ፫ሰዓት ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ተመለስን ።

## አራተኛ ፡ ትልልቅ ፡ ክፍል ።

በጃፓን ፡ ምዕራብና ፡ ደቡብ ፡ አገሮች ፡ ስለ ፡ ሆነው ፡ ነገር ።

አዳዋራ ። ሚያኖሽታ ። ፉጂያ ፡ ሆቴል ። የፉጂ ፡ ተራራ ። ናጎያ ። የሰሐንና ፡ የሲኒ ፡ ፋብሪካ ። የሻምብር ፡ አፍ ፡ ኮሜርስ ፡ ግብዣ ። የዶ ሮ ፡ ማርቢያ ፡ ፋብሪካ ። የአይሮፕላንና ፡ የባቡር ፡ ዋጎን ፡ ፋብሪካ ። የ ናጎያ ፡ ከንቲባ ፡ ግብዣ ። የናጎያ ፡ ካስል ። የናጎያ ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ ግብዣ ። ከናጎያ ፡ መነሣት ። ዘማች ፡ ወታደር ፡ ማየት ። ኪዮቶ ፡ መድረስና ፡ ቤተ ፡ መንግሥቱን ፡ ማየት ። የሚጂን ፡ መቃብር ፡ መጎብኘት ። የኪዮቶ ፡ ተ ራራ ። የጦርነት ፡ ትምሕርት ፡ ክለብ ። የሲኒማ ፡ ፋብሪካ ። የናራ ፡ ከተማ ። አጋዘኖች ። የሸንቶ ፡ ሽራይን ። የቡዳሃ ፡ መቅደስ ። ወደ ፡ አሳካ ። የአሳ ካን ፡ ካስል ፡ ማየት ። በያይነቱ ፡ የቆሙትን ፡ ፋብሪኮችን ፡ ሁሉ ፡ ማ የት ። የሻምብር ፡ አፍ ፡ ኮሜርስ ፡ ግብዣ ። ወደ ፡ ሚያጂማ ፡ መሔድ ። ያዋታ ፡ ከተማ ። የብረት ፡ ፋብሪካ ። የቤፑ ፡ ከተማ ። ተራሮችና ፡ ፍል ፡ ውሆች ። ሆስፒታል ። በሲቲ ፡ ሀል ፡ ትያትር ፡ ማየት ። በሆቴል ፡ ዘፈን ። በመርከብ ፡ ወደ ፡ አሳካ ፡ መመለስ ። ከአሳካ ፡ ወደ ፡ ኮቤ ። የላስቲክ ፡ ፋብሪካ ። የሻምብር ፡ አፍ ፡ ኮሜርስ ፡ ግብዣ ። የኮቤ ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ ግብዣ ። ወደ ፡ ቶኪዮ ፡ መመለስ ።

### ምዕራፍ ፡ ፲፰ ፤

በኅዳር ፡ ፲ ፡ ቀን ፡ ከጧቱ ፡ በ፫ ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ከቶኪዮ ፡ ተነሥተ ን ፡ ወደ ፡ አዳዋራ ፡ ሔድን ። ዮኮሀማ ፡ ስንደርስ ፡ የዮኮሀማ ፡ አውራጃ ፡ ገዢ ፡ እስከ ፡ ባቡር ፡ መቆሚያ ፡ መጥቶ ፡ ተቀበለን ። እስከ ፡ ሁለተኛው ም ፡ ጣቢያ ፡ ድረስ ፡ መጥቶ ፡ ዋና ፡ ጸሐፊው ፡ ከእኛ ፡ ጋራ ፡ እስከ ፡ አዳ ዋራ ፡ እንዲሸኘን ፡ አድርጎ ፡ ተመለሰ ። በ፮ ፡ ሰዓት ፡ አዳዋራ ፡ ደረስን ።

ከዚያም ፡ በ፴ ፡ ደቂቃ ፡ ወደ ፡ ሚያኖሽታ ፡ ወጥተን ፡ ፉጂያ ፡ በሚባል ፡ ሆቴል ፡ ገባን ።

ፉጂያ ፡ የሚባለው ፡ ሆቴል ፡ ከባሕር ፡ ከፍታው ፡ ሺ፫፻፸፫ ፡ ጫማ ፡ በሚሆን ፡ በተራራ ፡ ወገብ ፡ ላይ ፡ የተሠራ ፡ ነው ። በአትክልቱና ፡ በዛፉ ፡ በአበባውም ፡ በቤቱም ፡ ማማር ፡ እጅግ ፡ የተመሰገነ ፡ ነው ። በውስጡ ፡ የ መዋኛ ፡ ባሕርና ፡ ዓሣ ፡ የሚረባበት ፡ ባሕር ፡ አለ ። ስለዚህ ፡ በበጋ ፡ ጊዜ ፡ ብዙ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ለመናፈስ ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ ሲመጡ ፡ የሚ ያርፉት ፡ በዚህ ፡ ስፍራ ፡ ነው ።

ከዚህም ፡ በቀር ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ የሆነ ፡ ፍልና ፡ ቀዝቃዛ ፡ ሚኔራል ፡ ውሀ ፡ (ጠበል ፡)አለበትና ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ በሽታ ፡ ያለባቸው ፡ ሰዎች ፡ ሀኪም ፡ ወደ ፡ ሚያኖሽታ ፡ ሔዳችሁ ፡ እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ ጠበል ፡ ጠጡ ፡ እያላ ቸው ፡ እየሔዱና ፡ እየጠጡ ፡ የሚድኑ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የታወቀ ፡ ስፍራ ፡ ነው ። በቶኪዮም ፡ የሚኖሩ ፡ አምባሳደሮችና ፡ ሚኒስትሮች ፡ ቆንስሎችም ፡ ሌሎ ችም ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ዕረፍት ፡ ባስፈለጋቸው ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ሚያ ኖሽታ ፡ ይሔዳሉ ። ባለ ፡ ሆቴሉም ፡ ሙሴ ፡ ክናያ ፡ ይባላል ።

ለሆቴሉ ፡ ባንድ ፡ ቀን ፡ የሚከፈለው ፡ ፲፰ዬን ፡ ነው ። ከዚህም ፡ በቀ ር ፡ መጠጥ ፡ የሚጠጣና ፡ ሌላም ፡ ልዩ ፡ ሙብል ፡ አሰናዱልኝ ፡ ብሎ ፡ የሚ ያዝ ፡ ሰው ፡ ዋጋው ፡ የሚከፍለው ፡ ለብቻው ፡ ነው ።

ነገር ፡ ግን ፡ ምንም ፡ ሆቴሉ ፡ እንደዚህ ፡ ቢያምርና ፡ ብዙ ፡ ገንዘብም ፡ ቢገባ ፡ ባለ ፡ ሆቴሉ ፡ ሙሴ ፡ ክናያ ፡ ሚስትም ፡ ልጆችም ፡ የሌሉት ፡ ስለ ሆነ ፡ ርስቱና ፡ ገንዘቡ ፡ ሁሉ ፡ ለማንም ፡ የሚያልፍ ፡ በመሆኑ ፡ ያሳዝ ናል ። እርሱ ፡ ግን ፡ ምናልባት ፡ ሚስት ፡ ከማግባትና ፡ ልጆች ፡ ከመውለ ድ ፡ ያሁኑ ፡ ኑሮው ፡ የሚሻል ፡ መስሎ ፡ ታይቶት ፡ ይሆናል ።

እኛም ፡ የሩቅ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ስለ ፡ ሆንን ፡ ሙሴ ፡ ክናያ ፡ በማክ በርና ፡ በወዳጅነት ፡ ዓይን ፡ ያየን ፡ ነበርና ፡ ቆመን ፡ ስንነጋገር ፡ በጃፓንና ፡ በሺኖች ፡ መካከል ፡ ጡብ ፡ በመነሣቱ ፡ እየተናደደ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ያለ ውን ፡ ቃል ፡ ተናገረ ።

እኛ ፡ ጃፓኖች ፡ ዛሬ ፡ ለሲን ፡ ይቅርና ፡ ለሌላም ፡ ትልቅ ፡ መንግሥት ፡ ቢሆ ን ፡ አንደነግጥም ። ሕዝባችን ፡ እጅግ ፡ የተማረና ፡ እውቀት ፡ ያለው ፡ ሕዝብ ፡ ሆኗል ።

ወታደሮቻችንም ፡ የጦርነት ፡ ሥራ ፡ ተምረው ፡ ጨርሰዋል ። ስለ ዚህ ፡ ለ፳ ፡ ሺንዋ ፡ ፩ ፡ ጃፓን ፡ ይበቃቸዋል ። ከዛሬ ፡ ፳ ፡ ዓመት ፡ በ ፊት ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡ ይኮሩብን ፡ ነበር ።



በታምራት ፡ ከመሬት ፡ ተወርውሮ ፡ ወደ ፡
ላይ ፡ ወጣ ፡ የሚባለው ፡ የፉጂ ፡ ተራራ ።

ሌላስው ፡ ይቅርና ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ሆቴል ፡ እየመጡ ፡ ሲበሉ ፡ ሲጠጡ፡ ሰንብተው ፡ በሚሔዱበት ፡ ጊዜ ፡ ዋጋ ፡ ክፈሉ ፡ ያልኋቸው ፡ እንደሆነ ፡ እምቢ ፡ እያሉ ፡ ይሔዱ ፡ ነበርና ፡ ለቆንስላቸው ፡ ለመንገር ፡ ወደ ፡ ዮክ ሃማ ፡ ወይም ፡ ወደ፡ቶኪዮ ፡ ድረስ ፡ እሔድ ፡ ነበር ።

ዛሬ ፡ ግን ፡ መንግሥታችን ፡ ራሱን ፡ የቻለ ፡ በመሆኑና ፡ የሚበቃ ፡ ዘበኛም ፡ ስለ ፡ አቆመልን ፡ እነርሱም ፡ እምቢ ፡ አይሉም ። ቢሉም ፡ እዚ ሁ ፡ ይዘን ፡ በግድ ፡ እናስከፍላቸዋለን ፡ እያለ ፡ የመንግሥቱን ፡ ጽናት ፡ የሕዝቡን ፡ ንቃትና ፡ ትጋት ፡ እያመሰገነ ፡ ነገረኝ ።

እኛም ፡ በፉጂያ ፡ ሆቴል ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ አድረን ፡ በማግሥቱ ፡ በ፫ ሰዓት ፡ ተነሥተን ፡ ወደ ፡ አዳዋራ ፡ ተመለስን ።

ከአዳዋራም ፡ በአራት ፡ ሰዓት ፡ በባቡር፡ ተሣፍረን ፡ ወደ ፡ ናጎያ ፡ ተ ጓዝን ። ስድስት ፡ ሰዓት ፡ ሲሆን ፡ የፉጂን ፡ ተራራ ፡ ማየት ፡ ጀመርን ።

የፉጂ ፡ ተራራ ፡ ከባሕር ፡ ርዝመቱ ፡ ፲፪ሺ ፡ ፫፻፷ ፡ ጫማ ፡ ነው ። ጃፓኖች ፡ ቃል ፡ ለቃል ፡ ተያይዞ ፡ እንደመጣላቸው ፡ የፉጂ ፡ ተራራ ፡ ከ ክርስቶስ፡ልደት፡በፊት፡በታምራት፡በ፻ዝ፡እጅ ፡ ከምድር፡የወጣ፡ነው ፡ እያሉ ፡ ያመልኩበት ፡ ነበር ። ስለዚህም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ቅዱስ ፡ ተራራ ፡ ይባላል ።

ይህም ፡ ከቀድሞ ፡ ጀምሮ ፡ በያገሩ ፡ ሲደረግ ፡ የሚኖር ፡ ልማድ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በጃፓን ፡ ብቻ ፡ አይደለም ።

ሙሴ፡በሲና ፡ ተራራ ፡ እየወጣ፡እግዚአብሔርን ፡ ያመልክ፡ ነበር። ሌሎችም ፡ እስራኤሎች ፡ ለእግዚአብሔርም ፡ ቢሆን ፤ ለጣዖትም ፡ ቢሆን ፤ መሠዊያ ፡ እየሠሩ ፡ የሚያመልኩበት ፡ በተራራ ፡ ላይ ፡ ነበር ። በጌታ ችንም ፡ዘመን ፡ አንዲት ፡ ሣምራዊት ፡ ሴት ፡ አባቶቻችን ፡ በዚህ ፡ በዚህ ፡ ተራራ ፡ ይሰግዳሉ ፡ እያለች ፡ ለጌታችን ፡ ተናግራለች ። ጌታችንም ፡ ጌ ትነቱን ፡ ለደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ የገለጠላቸው ፡ በታቦር፡ ተራራ ፡ላይ፡ነው ።

ባገራችንም ፡ ትልልቁ ፡ ገዳሞች ፡ የተሠሩት ፡ በቢዘን ፡ ተራራ ፤ በ ዳሞ ፡ ተራራ ፤ በግሼን ፡ ተራራ ፤ በዝቋላ ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ነው ።

ጋሎችም ፡ በአዲስ ፡ አበባ ፡ አጠገብ ፡ ያለውን ፡ የመናገሻን ፡ ተራራ፡ ቅዱስ ፡ ተራራ ፡ ነው ፡ እያሉ ፡ በያመቱ ፡ እየተሰበሰቡ ፡ እየወጡ ፡ ይ ሰግዱበታል ።

እስላሞችም ፡ በባሌ ፡ ኖራ ፡ ሁሴን ፡ የሚባለውን ፡ ተራራ ፡ ቅዱስ ፡ ተራራ ፡ ይሉታል ።

ጃፓኖችም ፡ የፉጂን ፡ ተራራ ፡ ቅዱስ ፡ ተራራ ፡ ማለታቸው ፡ እንደዚሁ ፡ በ ልማድ ፡ ቃል ፡ ለቃል ፡ ሲያያዝ ፡ ስለ ፡ መጣላቸው ፡ መሆኑ ፡ አይጠረጠርም ።

የፉጂ ፡ ተራራው ፡ አኳሆን ፡ በአዲስ ፡ አበባ ፡ ደቡብ ፡ እንዳለው ፡ እን ደ ፡ ዝቋላ ፡ ተራራ ፡ ይመስላል ። ቢሆንም ፡ የዝቋላ ፡ ተራራ ፡ ከመሬት ፡ ላይ ፡ ቀጥ ፡ ብሎ ፡ የወጣ ፡ ነው ፤ የፉጂ ፡ ተራራ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ሥሩ ፡ ሰፊ ፡ አገር ፡ ሆኖ ፡ ቀጥታው ፡ በየጥቂቱ ፡ ሆኖ ፡ የወጣ ፡ ነውና ፡ ከዝቋላ ፡ ተራራ ፡ ልዩነቱ ፡ በዚህ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

በጫፉም ፡ ላይ ፡ የበረዶ ፡ ውርጭ ፡ (አስሐትያ ፡) ስለ ፡ አለበት ፡ ዘወትር ፡ የጥጥ ፡ ንድፍ ፡ የተቆለለበት ፡ መስሎ ፡ ይታያል ።

እንደዚህም ፡ በፍጥረቱ ፡ የተዋበውን ፡ የፉጂን ፡ ተራራ ፡ እያየን ፡ አንድ ፡ ሰዓት ፡ ያህል ፡ ከተጓዝን ፡ በኋላ ፡ ካይናችን ፡ ተሰወረ ፡

በ፰ ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ናጎያ ፡ ከተማ ፡ ደረስን ። በባቡር ፡ መቆሚ ያም ፡ የናጎያ ፡ አገረ ፡ ገዢና ፡ ከንቲባው ፡ ከከተማው ፡ ዋና ፡ ዋና ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ ሆነው ፡ በባቡር ፡ መቆሚያ ፡ ተቀበሉን ።

ከነዚሁም ፡ አንደኛው ፡ ሙሴ ፡ ሚዩር ፡ የሚባለው ፡ በናጎያ ፡ ያለ ው ፡ የሰሐንና ፡ የስኒ ፡ ፋብሪካ ፡ ዋና ፡ ጸሐፊ ፡ በ፲፱፻፲፱ ፡ ዓ ፡ ም ፡ ወደ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ መጥቶ ፡ ተዋውቀን ፡ ነበርና ፡ እርሱን ፡ በዚያ ፡ ስማግኘቴ ፡ ብዙ ፡ ደስ ፡ አለኝ ።

---

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

በናጎያ ፡ ሆቴል ፡ ገብተን ፡ እኩል ፡ ሰዓት ፡ ያህል ፡ ካረፍን ፡ በኋላ ፡ የሰሐኑንና ፡ የስኒውን ፡ ፋብሪካ ፡ ለማየት ፡ ሔድን ።

ዲረክተሩም ፡ በየፋብሪካው ፡ ክፍል ፡ እየዞረ ፡ የሰሐኑንና ፡ የሲኒውን ፡ ሥራ ፡ ከአፈሩ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ መጨረሻው ፡ አሳየን ። ሁሉም ፡ የ ሚሠራው ፡ በኤሌክትሪክ ፡ ኃይል ፡ በሚዞር ፡ መኪና ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ሥ ራው ፡ በፍጥነት ፡ መጨረሱ ፡ በጣም ፡ ያስደንቃል ።

በዚሁም ፡ ፋብሪካ ፡ የሚሠሩት ፡ ሠራተኞች ፡ ወንዶችም ፡ ሴቶች ም ፡ በንድነት ፡ ሆነው ፡ ፱፻፱፻ ፡ ናቸው ፡ ብለው ፡ ነገሩን ። በየክፍሉ ም ፡ እየገባን ፡ ካየን ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ተመለስን ።

በዚሁም ፡ ቀን ፡ የናጎያ ፡ ሻምብር ፡ አፍ ፡ ኮሚርስ ፡ ራት ፡ ጋብዘ ውን ፡ ነበርና ፡ ከማታው ፡ ባንድ ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ሔድን ። በናጎያ ፡ ያሉት ፡ የንግድ ፡ ቤት ፡ ዲረክተሮችና ፡ የናጎያ ፡ አገረ ፡ ገዢ ፡ ከንቲ



# Menu



Dèjeuner

Su 25 Novembre 1931



Hors-d' Œuvre

Consommé à la Bouquetière

"Tai" Grille Sauce Hollandaise

Médaillon de Bœuf aux Légume

Salade de saison

Marron à la Chantilly

Dessert

Ethipia Café

በናጎያ ፡ ከተማ ፡ ሻምብር ፡ ኦፍ ፡ ኮሜርስ ፡ ራት ፡ ጋብዘን ፡ የቀረበው ፡ ምግብ ፡ ዓይነትና ፡ ቍጥር ፡፡

ባውም ፡ ከእኛ ፡ ጋራ ፡ ለእራት ፡ ተጠርተው ፡ ነበር ። ቍጥራቸውም፡ አምሳ ፡ ይሆናል ። የራት ፡ ግብዣው ፡ እንደ ፡ ጃፓኖች፡ልማድ ፡ በጃፓን ፡ ሆቴል ፡ በፍራሽ ፡ ላይ ፡ እየተቀመጥን ፡ ነበር ።

ራትም ፡ ሳይጀመር ፡ የሻምብር ፡ ኦፍ ፡ ኮሜርስ ፡ ፕሬዚዳን ፡ ባደራሹ፡ መካከል ፡ ቆሞ ፡ የኢትዮጵያና ፡ የጃፓን ፡ ሕዝብ ፡ የሚገናኙበትን ፡ ንግዳቸው ፡ የሚሰፋበትን ፡ ረጅም ፡ ዲስኩር ፡ ተናገረ ።

እኔም ፡ ለዚሁ ፡ ለሁለቱ ፡ መንግሥቶች ፡ ሕዝብ ፡ መገናኘትና ፡ ለንግዳቸው ፡ መስፋት ፡ መሥራች ፡ በመሆኔ ፡ ደስታዬን ፡ እየገለጥሁ፡ ለዲስኩሩ ፡ ምላሽ ፡ ከተናገርሁ ፡ በኋላ ፡ ዳር ፡ እስከ ፡ ዳር ፡ ተጨበጨበ ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ክራር ፡ እየተመታ ፡ የጃፓኖች ፡ ዘፈን ፡ እየተዘፈነ ፡ ከሌሊቱ ፡ እስከ ፡ ፯ ፡ ሰዓት ፡ ቆይተን ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ተመለስን ።

በኅዳር ፡ ፳ ፡ ቀን ፡ በናጎያ ፡ ያለውን ፡ የዶሮ ፡ ማርቢያ ፡ ፋብሪካ ፡ አየን ። እንቍላሉን ፡ በሳጥን ፡ እየሞሉ ፡ በየክፍሉ ፡ እያኖሩ ፡ ሙቀቱን ፡ በኤሌክትሪክ ፡ ኃይል፡በልክ ፡ እያሞቁ፡በ፳፩ኛው፡ ቀን ፡ ጫጩት ፡ እየሆነ፡ በገዛ ፡ እጁ ፡ ይቀፈቀፋል ። ባንዳንድ ፡ ቀን ፡ ፲ሺ ፡ ጫጩት ፡ ይቀፈቀፋሉ ፡ ብለው ፡ ነገረን ። ሲቀፈቀፉም ፡ ዕለቱን ፡ ወንድና ፡ ሴቱን ፡ እየለዩ ፡ ሉብቻ ፡ ያኖርዋቸዋል ። ከተቀፈቀፉ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ፩ ወር ፡ ለብቻቸው ፡ ሥፍራ ፡ አላቸው ። እንደዚሁ ፡ ፩ ፡ ወር ፡ የሞላቸውን ፡ ለብቻቸው ፡ ፪ወር ፡ የሞላቸውን ፡ ለብቻቸው ፡ ፫ ወር ፡ የሞላቸውን ፡ ለብቻቸው ፡ ያኖርዋቸዋል ። በ፫ተኛው ፡ ወር ፡ ለመበላት ፡ ይደርሳሉ ።

የዶሮ ፡ ማርቢያ ፡ ፋብሪካ ፡ ብዬ ፡ ስጽፍ ፡ ምናልባት ፡ አንዳንድ ፡ ሰዎች ፡ ነገሩን ፡ ይንቁት ፡ ይሆናል ። ነገር ፡ ግን ፡ ያለ ፡ ብዙ ፡ ድካም ፡ ትልቅ ፡ ብልጥግና ፡ የሚገኝበት ፡ ከዚህ ፡ በቀር ፡ የለም ።

ባንድ ፡ ቀን ፡ ፲ሺ ፡ ጫጩት ፡ ሲቀፈቀፉ ፡ ፩ ፡ ዶሮ ፡ ፩ ፡ ዩን ፡ ተኩል ፡ ታወጣለች ፡ ብለዋልና ፡ ባንድ ፡ ቀን ፡ ፲፭ሺ ፡ ዩን ፡ ማግኘታቸው ፡ ነው ። እንደዚህ ፡ ሲሆን ፡ ባንድ ፡ ወር ፡ የሚያገኙት ፡ ፬፻፶ሺ ፡ ዩን ፡ መሆኑ ፡ ነው ።

ስለዚህ ፡ የዶሮ ፡ ማርባትን ፡ ሥራ ፡ መናቅ ፡ አይገባም ።

የዶሮ ፡ ማርቢያውንም ፡ ፋብሪካ ፡ ካየን ፡ በኋላ ፡ የአይሮፕላንና የባቡር ፡ ዋጐን ፡ የሚሠራበትን ፡ ፋብሪካ ፡ ለማሳየት ፡ ወሰዱን ። ይህንም ፡ ሁሉ ፡ እያዞሩ ፡ ካሳዩን ፡ በኋላ ፡ የናጎያ ፡ ከተማ ፡ ከንቲባ ፡ ምሳ ፡ ጋብዞን ፡ ነበርና ፡ ወደዚያ ፡ ሔድን ። የጋበዘንም ፡ በሹመቱ ፡ ቤት ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ በማዘጋጃ ፡ ቤት ፡ አልነበረም ።

በዚያም ፡ በናጎያ ፡ ከተማ ፡ በየፋብሪካው ፡ የሚሠራው ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ለዓይነት ፡ ተሰብስቦ ፡ በመተላለፊያው ፡ ሥፍራ ፡ ነበርና ፡ እያዞሩ ፡ አሳዩን ። የዕቃውም ፡ ዓይነት ፡ በዚያ ፡ የተሰበሰበበት ፡ ምክንያቱ ፡ እርሱ ፡ የከተማው ፡ ከንቲባ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ዘንድ ፡ የሚሔዱ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ እንግዶች ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ያንን ፡ እያዩ ፡ ዕቃ ፡ ለመግዛት ፡ ይጠይቃሉና ፡ ስለ ፡ ከተማው ፡ ሕዝብ ፡ ጥቅም ፡ ተብሎ ፡ ነው ።

ከእኛም ፡ ጋራ ፡ ለምሳ ፡ የተጋበዙ ፡ የከተማው ፡ ትልልቅ ፡ ሰዎች ፡ ፳፩ ፡ ነበሩ ። ምሳውም ፡ ሲጨረስ ፡ ከንቲባው ፡ የናጎያን ፡ ከተማ ፡ ቀደምትነት ፤ የፋብሪካውን ፡ ብዛት ፤ የንግዱን ፡ ስፋት ፤ እያስረዳ ፡ ረጅም ፡ ዲስኩር ፡ ተናገረ ። እኔም ፡ በናጎያ ፡ ከተማ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ፋብሪኮች ፡ በማየታችን ፡ ማድነቃችንን ፤ በየፋብሪካውም ፡ ያሉት ፡ ሹሞችና ፡ ሠራተኞች ፡ በፍቅርና ፡ በማክበር ፡ ስለ ፡ ተቀበሉን ፡ ማመስገናችንን ፤ በፋብሪካውም ፡ አንዳንድ ፡ ዕቃ ፡ ለማሠራትና ፡ ለመግዛት ፡ መፍቀዳችንን ፡ ገልጬ ፡ ስለ ፡ ተናገርሁ ፡ በዚያ ፡ የነበሩ ፡ ትልልቆች ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ በደስታ ፡ አጨበጨቡና ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ተመለስን ።

ከዚያም ፡ ስንወጣ ፡ የናጎያን ፡ ካስል ፡ ለማየት ፡ ሔድን ። ይህን ፡ ካስል ፡ ያሠራው ፡ ከዛሬ ፡ ፫፻ ፡ ዓመት ፡ በፊት ፡ በፌዩዳል ፡ ዘመን ፡ የነበረው ፡ ቶኩጋዋ ፡ የሚባለው ፡ መስፍን ፡ ነው ።

በዚያ ፡ ዘመን ፡ መሳፍንቱ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ይፈራሩ ፡ ነበርና ፡ በቅጥሩ ፡ ግቢ ፡ የተመሸገውን ፡ ብርቱ ፡ ምሽግ ፡ ሁሉ ፡ አየን ።

በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ ከነበሩት ፡ ጠንካሮች ፡ ምሽጎች ፡ ይህ ፡ የቶኩጋዋ ፡ ምሽግ ፡ ሶስተኛ ፡ ነው ፡ ይባላል ። የድንጋዩም ፡ ትልልቅነት ፡ በዚያው ፡ የተፈጠረ ፡ ይመስላል ፡ እንጂ ፡ በሰው ፡ጉልበት፡ከሌላ፡ ስፍራ ፡ መጥቶ ፡ የተሠራ ፡ አይመስልም ።

ዋናው ፡ ካስል ፡ ፯ ፡ ደርብ ፡ ነው ። ፯ቱ ፡ ደርብ ፡ ሁሉ ፡ የዘበኞች ፡ ማደሪያ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ የመስፍኑ ፡ መኝታ ፡ ቤትና ፡ እንግዳ ፡ መቀበያ ፡ ቤት ፡ በተለየ ፡ ለብቻው ፡ ነው ።

የላይኛው ፡ ጣሪያው ፡ ሞላላ ፡ ሆኖ ፡ በጫፉና ፡ በጫፉ ፡ የወርቅ ፡ ጉልላት ፡ አለበት ። በእኛ ፡ አገር ፡ ፩ ፡ ወቄት ፡ ወርቅ ፡ የሚባለው ፡ ሚዛኑ ፡ ፩ ፡ ብር ፡ እንደሆነ ፡ በዚያም ፡ ዘመን ፡ በጃፓን ፡ እንደ ፡ ነበረው ፡ የወርቅ ፡ ሚዛን ፡ ልክ ፡ ሁለቱ ፡ ጉልላት ፡ የፈጀው ፡ ወርቅ ፡ ፲፫፻፶፱፻፸፭ ፡ ወቄት ፡ ነው ፡ ይባላል ። እስከ ፡ ዛሬም ፡ ወርቅነቱ ፡ ሳይለወጥ ፡ በሩቅ ፡ ይታያል ።



በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ በናጎያ ፡ የመስፍኑ ፡ የቶኩጋዋ ፡ ቤት ፡ የነበረው ።

ይህም ፡ ካስል ፡ የትልልቅ ፡ ጌቶች ፡ ማረፊያ ፡ ሆኖ ፡ ሲኖር ፡ በ፲፰፻ ፺፫ ፡ ዓ ፡ ም ፡ በንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሜጂ ፡ ዘመን ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ቤተ ፡ ዘመዶች ፡ ርስት ፡ እንዲሆን ፡ ተፈቅዶ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ በ፲፱፻፴ (፲፱፻፳፫ ፡) ዓ ፡ ም ፡ የዛሬው ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ግርማዊ ፡ ሒሮሂቶ ፡ ለናጎያ ፡ ማዘጋጃ ፡ ቤት ፡ ርስት ፡ አድርገው ፡ ስለ ፡ ሰጡት ፡ አሁን ፡ በማዘጋጃ ፡ ቤት ፡ እጅ ፡ ሆኗል ።

በቀን ፡ በቀኑ ፡ ከከተማውም ፡ ሰው ፡ ከእንግዶችም ፡ ወገን ፡ እስከ ፡ አንድ ፡ ሺ ፡ ሰዎች ፡ እየገቡ ፡ ሳያዩ ፡ አይውሉም ። ለመግቢያውም ፡ ፈቃድ ፡ እስከ ፡ ፶ ፡ ሳንቲም ፡ ይከፈላል ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

እኛም ፡ እስከ ፡ ሰባተኛው ፡ ደርብ ፡ በወጣን ፡ ጊዜ ፡ የናጎያን ፡ ከተማ ፡ ቁልቁል ፡ አየነው ። ከዚያም ፡ ወጥተን ፡ ልብስ ፡ የሚሠራበትንና ፡ አውቶሞቢል ፡ የሚሠራበትን ፡ ፋብሪካ ፡ አየን ።

በዚሁም ፡ ቀን ፡ ከማታው ፡ በ፩ ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ የናጎያ ፡ አውራጃ ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ ራት ፡ ጋብዘን ፡ ነበርና ፡ ወደዚያ ፡ ሔድን ።

በቤቱም ፡ ውስጥ ፡ ካገራችን ፡ ከኢትዮጵያ ፡ የሔደ ፡ ጋሻና ፡ ጦር ፡ ጐራዴም ፡ ልብስም ፡ ሌላም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ዕቃ ፡ እንደ ፡ አንቲካ ፡ ተሰቅሎ ፡ ይታይ ፡ ነበር ፡

በራትም ፡ ላይ ፡ አገረ ፡ ገዥው ፡ የሁለቱን ፡ መንግሥቶች ፡ ሕዝብ ፡ የሚያገናኝና ፡ የሚያፋቅር ፡ ዲስኩር ፡ በጃፓን ፡ ቋንቋ ፡ ተናግሮ ፡ ሲጨርስ ፡ ባማርኛ ፡ ቋንቋ ፡ ስለ ፡ እርስዎ ፡ ጤና ፡ ብሎ ፡ የሻምፓኝ ፡ ብርጭቆውን ፡ ባነሣ ፡ ጊዜ ፡ ሁሉም ፡ በደስታ ፡ አጨበጨቡ ።

ይልቁንም ፡ ስለ ፡ እርስዎ ፡ ጤና ፡ ብሎ ፡ ባማርኛ ፡ ቋንቋ ፡ በመናገሩ ፡ በጣም ፡ ተሳቀለት ።

በናጎያ ፡ ከተማ ፡ ካለው ፡ ከሰሐንና ፡ ከሲኒ ፡ ፋብሪካ ፡ ተልከው ፡ ወደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ መጥተው ፡ የተመለሱ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩና ፡ የአንቲካውን ፡ ዕቃና ፡ ያማርኛውን ፡ ቋንቋ ፡ ከእነዚያ ፡ ሰዎች ፡ ያገኘው ፡ ይመስላል ።

እኔም ፡ አገረ ፡ ገዥው ፡ ለተናገረው ፡ ዲስኩር ፡ ምላሽ ፡ ተናግሬ ፡ በታላቅ ፡ ደስታ ፡ የራት ፡ ግብዣው ፡ ሲጨረስ ፡ ወደ ፡ ሌላው ፡ ክፍል ፡ ቤት ፡ ገብተን ፡ የኢትዮጵያን ፡ አገር ፡ ሲኒማ ፡ ሲያሳዩን ፡ አመሹ ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሆቴላችን ፡ ተመለስን ።

በኅዳር ፡ ፱ ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ኪዮቶ ፡ ለመሔድ ፡ ከጧቱ ፡ በ፫ ፡ ሰዓት ፡ ከናጎያ ፡ ተነሥተን ፡ ወደ ፡ ባቡር ፡ መቆሚያ ፡ ሔድን ።

በዚህም ፡ ቀን ፡ ከናጎያም ፡ ከሌላም ፡ አገር ፡ ብዙ ፡ ወታደሮችና ፡ የጦር ፡ አለቆች ፡ ሽኖችን ፡ ለመጠባበቅ ፡ ወደ ፡ ማንቹሪያ ፡ የሚሔዱ ፡ ስለ ፡

ሆነ ፡ ከከተማው ፡ ሰው ፡ ብዙዎቹ ፡ ወታደሩን ፡ ለመሰነባበት ፡ ወደ ፡ ባቡር ፡ መቋሚያ ፡ መጥተው ፡ ነበርና ፡ ከሕዝቡ ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ለመቋሚያ ፡ እንኳ ፡ ስፍራ ፡ ተቸግረን ፡ ነበር ።

በዚያም ፡ የተሰበሰበው ፡ ሕዝብ ፡ ወንዱም ፡ ሴቶቹም ፡ ልጆቹም፡ ሁሉ ፡ የጃፓንን ፡ ባንዲራ ፡ ይዘው ፡ ነበር ።

በባቡርም ፡ የመጣው ፡ ወታደር ፡ ሁሉ ፡ እንደዚሁ ፡ ባንዲራ ፡ ይዞ፡ ነበር ። በባቡር፡ መቋሚያም ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ሁሉም ፡ ባንዲራቸውን፡ እያራገቡ ፡ ደህና፡ ያግባችሁ ፡ ይቅናችሁ ፡ የሚል ፡ የመሰናበቻ ፡ ቃል፡ ተናገሩ።ወዲያውም ፡ የጃፓንን ፡ ሂምን ፡ ናሲዮናል ፡ ሁሉም ፡ ባንድ፡ቃል፡ ዘምረው ፡ በደስታ ፡ ተሰነባበቱ ።

ከደስታቸውም ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ወደ፡ሠርግ ፡ ቤት ፡ የሚሔዱ ፡ ይመስሉ፡ነበር ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ ጦርነት ፡ የሚሔዱ ፡ አይመስሉም ፡ ነበር ። ወደ ባሕር ፡ እስቲደርሱና ፡ ከባቡር ፡ እስቲወርዱ ፡ ድረስ ፡ በየባቡሩ ፡ መቋሚያ ፡ እንደዚሁ ፡ ይደረግላቸዋል ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

ወታደር ፡ ወደ ፡ ዘመቻ ፡ ለመሔድ ፡ በሚሰናበትበት ፡ ጊዜ ፡ እያለቀሱ ፡ ሆዱን ፡ ከማባባት ፡ በዘፈን ፡ በጨዋታ ፡ በደስታ ፡ ማሰናበት ፡ እጅግ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ ነው ።

እየዘፈኑም ፡ በደስታ ፡ ሲሰናበቱ ፡ አይቼ ፡ በትልቁ ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ ጊዜ ፡ አንዲት ፡ የኢጣልያ ፡ ወይዘሮ ፡ ሶስቱ ፡ ልጆችዋ ፡ ዘምተው ፡ ነበርና ፡ ሁለቱ ፡ ሞቱ ፡ ብለው ፡ ቢነግሯት ፡ ስለ ፡ ሀገራቸውና ፡ ስለ ፡ ንጉሣቸው ፡ ቢሞቱ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡ እንጂ ፡ አላዝንም፡ የማዝነውስ ፡ ፫ኛው ፡ ልጄ ፡ ስለ ፡ ሀገሩ ፡ ሳይሞት ፡ የተመለሰ ፡ እንደሆነ፡ ነው ፡ አለች ፡ ተብሎ ፡ የተወራው ፡ ነገር ፡ ትዝ ፡ አለኝ ።

እነዚህም ፡ ወታደሮች ፡ አካሔዳቸው ፡ ስለ ፡ ሀገራቸውም ፡ ነጻነትና ፡ ጥቅም ፡ መሆኑን ፡ ያውቁታልና ፡ በዘፈንና ፡ በደስታ ፡ እየተሰነባበቱ፡ መሔዳቸው ፡ አገሩን ፡ ለሚወድ ፡ ሰው ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ።

ዘማቹም ፡ ወታደር ፡ የተሣፈረበት ፡ ባቡር ፡ ከሔደ ፡ በኋላ ፡ በ፬ ፡ ሰዓት ፡ ተሳፍረን ፡ በ፰ ፡ ሰዓት ፡ ኪዮቶ ፡ ከተማ ፡ ደረስን ። በባቡር ፡ መቋሚያም ፡ የኪዮቶ ፡ አውራጃ ፡ አገረ ፡ ገዢና ፡ የከተማው ፡ ከንቲባ ፡ የትምሕርት ፡ ቤት ፡ ፕሮፌሶሮችና ፡ ሌሎችም ፡ የከተማው ፡ ትልልቅ ፡ ሰዎች ፡ ተቀበሉን። ከዚያም ፡ ሚያኮ ፡ ወደሚባለው ፡ ሆቴል ፡ ገባን ።

## ምዕራፍ ፲፺ ።



ኪዎቶ ፡ አንድ ፡ ሺ፡ከ፸ዓመት ፡ ያህል ፡ የጃፓን ፡ ነገሥታት ፡ ዋና፡ ከተማ ፡ ሆና ፡ ስትኖር ፡ በኋላ ፡ በ፲፰፻፷፰ ፡ ዓ ፡ ም ፡ የነገሠው ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂ ፡ ዋና ፡ ከተማውን ፡ በኪዎቶ ፡ ስለ ፡ አደረገ ፡ ኪዎቶ ፡ የጥሩ፡ የጥሩ ፡ ዕቃ ፡ ፋብሪካና ፡ የትልልቅ ፡ ሰዎች ፤ የካህናትም ፡ መኖሪያ ፡ ሆና ለች ። ስለ ፡ ስፍራውም ፡ መልካምነትና ፡ ስለ ፡ ከተማው ፡ ውበት ፡ የጃፓን ፡ ገነት ፡ ትባላለች ።

ኪዎቶ ፡ ዙሪያዋን ፡ በተራራ ፡ የተከበበች ፡ በዘባጣ ፡ ስፍራ ፡ ላይ ፡ የተሠራች ፡ ከተማ ፡ ናት ።

የተራራውም፡አከባበብ፡እንደ፡እንጦጦ፡ሆኖ ፡ ኪዎቶ፡ እንደ ፡ አዲስ፡ አበባ ፡ ናት። ነገር፡ግን፡በሁለት፡ነገር ፡ ብቻ ፡ ከአዲስ፡ አበባ ፡ ትለያለች ።

፩ኛው ፡ ነገር። አዲስ ፡ አበባን ፡ የእንጦጦ፡ ተራራ ፡ በጣም ፡ ተጭኖታል ።የኪዎቶ፡ ተራራ ፡ግን፡ ከከተማው ፡ ጥቂት፡ እልፍ ፡ ብሎ ፡ይታያል ።

፪ኛው ፡ ነገር ። አዲስ ፡ አበባ ፡ በምሥራቅ ፡ በየረር ፡ በኩል ፤ በምዕራብ ፡ በገፈርሳ ፡ በኩል ፤ በደቡብ ፡ በዝቋላ ፡ በኩል ፡ ግልጥ ፡ ሆኖ ፡ ይታያል ። ኪዎቶ ፡ ግን ፡ ዙሪያውን ፡ በተራራ ፡ የተከበበ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ግልጥ ፡ ሆኖ ፡ አይታይም ። የባቡርና ፡ የአውቶሞቢልም ፡ መንገድ ፡ የተሠራው ፡ በጣም ፡ እየተዘዋወረ ፡ ነው ።

ይህንም ፡ ስፍራ ፡ የንጉሡ ፡ ነገሥት ፡ ከተማ ፡ እንዲሆን ፡ የመረጠው ፡ በ፺፻፺፬ ፡ ዓመ ፡ ምሕ ፡ ነግሦ ፡ የነበረው ፡ ክዋሙ ፡ የሚባለው ፡ ንጉሥ ፡ ነው ።

የቀድሞዎቹ ፡ የጃፓን ፡ ነገሥታት ፡ በከተማ ፡ መለወጥ ፡ ነገር ፡ እንደ ቀድሞዎቹ ፡ እንደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ነገሥታት ፡ ነበሩ ። ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ የቀድሞዎቹ ፡ ነገሥታት ፡ ይቅሩና ፡ አሁን ፡ በዘመናችን ፡ የነበሩት፡ አፄ ፡ ምኒልክ ፡ አባቶቻቸው ፡ ከሠሩት ፡ ከአንኮበርና ፡ ከደብረ ፡ ብርሃን ፡ በቀር ፡ እርሳቸው ፡ ከተማ ፡ ሠርተውባቸው ፡ የነበሩት ፡ አገሮች ፡ ልቼ ፤ እናዋሪ ፤ ወረይሉ ፤ ደቦጎጆ ፤ ወጨጫ ፤ እንጦጦ ፤ አዲስ ፡ አበባ ፤ አዲስ፡ ዓለም ፤ ገነት(ሆሎታ)ናቸው ። በድምሩ ፡ ፱ከተሞች ፡ መሆናቸው ፡ነው ።

በጃፓንም ፡ የቀድሞዎቹ ፡ ነገሥታት ፡ አንድ ፡ ከተማ ፡ ሠርተው ፡ በዚያ ፡ በሽታ ፡ የገባ ፡ እንደሆን ፤ ወይም ፡ ከቡዳሃ ፡ ካህናት ፡ ወገን ፡ ሐሰተኞች ፡ የሆኑት ፡ በጥንቆላ ፡ ይህን ፡ ከተማ ፡ ልቀቅ ፡ ያሏቸው ፡ እንደሆነ፤

ወይም ፡ ለሚዋጉት ፡ ንጉሥና ፡ ለሚያቀኑት ፡ አገር ፡ የራቀባቸው ፡ እንደ ሆነ ፡ የቀድሞ ፡ ከተማቸውን ፡ እየተዉ ፡ በሌላ ፡ አገር ፡ ከተማ ፡ ይሠሩ ፡ ነበር ።

ነገር ፡ ግን ፡ ምንም ፡ ከተማቸውን ፡ ከንዱ ፡ አገር ፡ ወደ ፡ ሌላው ፡ አገር ፡ ቢያዛውሩ ፡ የፊተኛው ፡ ከተማ ፡ ቢያረጅም ፡ እየታደሰ ፤ መኳንንቱና ፡ ሕዝቡም ፡ ቤታቸውን ፡ ሳያፈርሱ ፡ የሚኖሩ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የቀድሞ ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ዛሬውኑ ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ ናቸው ። ወደ ፡ ጃፓንም ፡ የሔደ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እነዚህን ፡ የቀድሞ ፡ ዘመን ፡ ከተሞች ፡ ሳያይ ፡ ወደ ፡ ሀገሩ ፡ አይመለስምና ፡ ልዩነቱ ፡ በዚህ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

የኢትዮጵያ ፡ ነገሥታት ፡ ከሠሩዋቸው ፡ ከተሞች ፡ ምልክታቸውና ፡ ስፍራቸው ፡ ያልጠፋ ፡ በትግሬ ፡ አኵሱም ፤ በሸዋ ፡ ደብረ ፡ ብርሃን ። በቤገምድር ፡ ጎንደር ፤ እነዚህ ፡ ሶስቱ ፡ ብቻ ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ የቀሩት ፡ የ ቀድሞዎቹ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ነገሥታት ፡ የሠሩዋቸው ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ምልክታቸውና ፡ ስፍራቸው ፡ በመጥፋቱ ፡ እጅግ ፡ ያሳዝናል ።

በኅዳር ፡ ፲ ፡ ቀን ፡ የንጉሡ ፡ ነገሥቱን ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ለማየት ፡ ሔድን ። በኪዮቶ ፡ የንጉሡ ፡ ነገሥቱ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ በየጊዜው ፡ በ እሳትም ፡ በሌላም ፡ አደጋ ፡ እየተበላሸ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ከንዱ ፡ ቦታ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ቦታ ፡ እየተዛወረ ፡ የተሠራ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከቀድሞ ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ ባንድ ፡ ቦታ ፡ ላይ ፡ ተሠርቶ ፡ የቆየ ፡ አይደለም ።

ያሁኑ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ዙሪያውን ፡ በግንብ ፡ የተቀጠረና ፡ በቅጥር ፡ ግቢ ፡ ያለው ፡ ቦታ ፡ እጅግ ፡ ሰፊ ፡ የሆነ ፡ ነው ።

ቢሆንም ፡ በአታክልትና ፡ በአበባ ፤ በዛፍ ፡ ያጌጠ ፡ መንገዱና ፡ አደባባዩ ፡ እጅግ ፡ የሰፋና ፡ ያማረ ፡ በመሆኑ ፡ ይመሰገናል ፡ እንጂ ፡ የቤቱ ፡ ሥራ ፡ እንደ ፡ ቀድሞ ፡ ጃፓኖች ፡ ቤት ፡ ነው ። አቋራጩም ፡ ሁሉ ፡ የተ ሠራው ፡ በእንጨትና ፡ በልብስ ፡ በያመቱም ፤ በሚታደስ ፡ በነጭ ፡ ወረቀት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በድንጋይ ፡ ወይም ፡ በሲምንቶ ፡ አይደለም ። የቤቱም ፡ ክፍል ፡ እንደ ፡ ሀገሩ ፡ ልማድ ፡ የእንግዳ ፡ ማረፊያና ፡ መገናኛ ፡ የመሳፍንት ፡ ማረፊያና ፡ መገናኛ ፤ የትልልቆች ፡ ሰዎች ፡ ማረፊያና ፡ መገናኛ ፤ የቤተ ፡ ዘመዶች ፡ ማረፊያና ፡ መገናኛ ፡ እየተባለ ፡ የተከፈለ ፡ ነው ።

በየቤቱም ፡ ክፍል ፡ ሁሉ ፡ ለንጉሡ ፡ ነገሥቱ ፡ መቀመጫ ፡ ፍራሽ ፡ የሚዘረጋበት ፡ ከመሬት ፡ ሠላሳ ፡ ሳንቲም ፡ ያህል ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ሣንቃ ፡ ይታይበታል ፡ እንጂ ፡ ወንበር ፡ ወይም ፡ ሌላም ፡ ዓይነት ፡ መቀመጫ ፡ አይታይም ።





በኪዮቶ ፡ ከተማ ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥትና ፡ እቴጌይቱ ፡
ሥርዓተ ፡ ንግሥ ፡ ሲያደርጉ ፡ የሚቀመጡባቸው ፡ ዙፋኖች ።





ግርማዊ ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥትና ፡ እቴጌይቱ ፡ በቀድሞ ፡ በጃፓን ፡
ነገሥታት ፡ ልብሰ ፡ መንግሥት ፡ ሥርዓተ ፡ ንግሥ ፡ ሲደርስላቸው ፡፡

መሳፍንቱና ፡ መኳንንቱ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ በምን ፡ ይቀመጣሉ ፡ ብለን ፡ ብንጠይቃቸው ፤ በጃፓን ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ከንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ በቀር ፡ በፍራሽ ፡ ላይ ፡ የሚቀመጥ ፡ የለም ። መሳፍንቱና ፡ መኳንንቱም ፡ ቢመጡ ፡ በፊቱ ፡ ይቆማሉ ፡ እንጂ ፡ ለመቀመጥ ፡ አይፈቀድላቸውም ።

ምናልባትም ፡ ብርቱ ፡ ረጅም ፡ ጉዳይ ፡ ቢኖራቸው ፡ በፊቱ ፡ በጉልበታቸው ፡ እየተንበረከኩ ፡ ተናግረው ፡ ይወጣሉ ።

በሙብል ፡ ቤቱና ፡ በሌላውም ፡ በተለየው ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ መቀመጫ ፡ በፍራሽ ፡ ላይ ፡ ነው ፤ መሳፍንቱና ፡ ሚኒስትሮች ፡ መኳንንቶቹም ፡ የሚበሉበት ፡ በተለየ ፡ ስፍራ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ጋራ ፡ አይደለም ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

ደግሞ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ጧት ፡ ጧት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚጸልይበት ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ምንጣፍ ፡ የሌለበት ፡ ነጭ ፡ ቀለም ፡ ብቻ ፡ የተቀባ ፡ ማንቃ ፡ አሳዩን ። ለብርድም ፡ ጊዜ ፡ ባጠገቡ ፡ ከማንቃው ፡ ጋራ ፡ አብሮ ፡ የተሠራ ፡ የእሳት ፡ መሞቂያ ፡ አለበት ።

ይህንም ፡ ሁሉ ፡ ካየን ፡ በኋላ ፡ ሥርዓተ ፡ ንግሥ ፡ የሚደረግበትን ፡ መንበረ ፡ መንግሥቱ ፡ የቆመበትን ፡ ሌላውን ፡ የቤት ፡ ክፍል ፡ አሳዩን ።

መንበረ ፡ መንግሥቱ ፡ እንደኛ ፡ አገር ፡ ዙፋን ፡ አይደለም ። ነገር ፡ ግን ፡ ከመሬት ፡ አንድ ፡ ሜትር ፡ ከ፶ ፡ ሳንቲም ፡ ያህል ፡ ከፍ ፡ ብሎ ፡ በ፰ማዕዘን ፡ ሆኖ ፡ እጅግ ፡ ባጌጠና ፡ ባማረ ፡ በእንጨት ፡ አዕማድ ፡ የተሠራ ፡ አጎበር ፡ ነው ።

ስፋቱ ፡ ፬ ፡ ሜትር ፡ ይሆናል ። አልፎ ፡ አልፎ ፡ የማዕዘኑ ፡ አዕማድ ፡ በሚገናኝበት ፡ ላይ ፡ በወርቅ ፡ ያጌጠ ፡ ነው ። በላይም ፡ በስምንቱ ፡ ማዕዘን ፡ እጅግ ፡ ያማረ ፡ መርገፍ ፡ የሚመስል ፡ ጌጥ ፡ አለበት ። በየማዕዘኑም ፡ መጨረሻ ፡ እጅግ ፡ የሚያምሩ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ አእዋፍ ፡ በወርቅ ፡ በሌላም ፡ በሚያምር ፡ ቀለም ፡ እየተቀረጹ ፡ ይታያሉ ። በመካከሉም ፡ ላይ ፡ አንገቱ ፡ በጣም ፡ የረዘመ ፡ አሞራ ፡ በወርቅ ፡ ተቀርጾ ፡ ይታያል ። እንኳን ፡ ወርቅና ፡ ብር ፡ ተጨምሮበት ፡ እንጨቱም ፡ ብቻ ፡ ቢሆን ፡ ከወርቅና ፡ ከብር ፡ ይልቅ ፡ ያማረ ፡ ነው ።

የደረጃውም ፡ እንጨት ፡ ሁሉ ፡ በድብልብል ፡ እየታነጸ ፡ መጋጠሚያውና ፡ መካከሉ ፡ ሁሉ ፡ በወርቅ ፡ የተለበጠ ፡ ነው ። ወደ ፡ አጎበሩ ፡ የመውጫው ፡ ደረጃ ፡ በሶስት ፡ ገጽ ፡ በኩል ፡ ነው ።

፩ኛው ፡ ገጽ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ከወደ ፡ ውስጥ ፡ መጥተው ፡ የሚወጡበት ፡ ነው ። ፪ተኛው ፡ ገጽ ፡ ወደ ፡ እቴጌይቱ ፡ ዙፋን ፡ የሚወስድ ፡

ነው ። ፫ተኛው ፡ ገጽ ፡ መሳፍንቱና ፡ መኳንንቱ ፡ በሚቆሙበት ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ነው ።

በአንበሩ ፡ መካከል ፡ ዳርና ፡ ዳሩ ፡ በወርቅ ፡ ያጌጠ ፡ ተድበልብሎ ፡ ከታነጸ ፡ እንጨት ፡ የተሠራ ፡ አንድ ፡ መጠነኛ ፡ ወንበር ፡ ተዘርግቶበ ታል ። በወንበሩ ፡ ቀኝና ፡ ግራ ፡ ስፋታቸው ፡ ፶ ፡ ሳንቲም ፡ የሚሆን ፡ ከድንጋይ ፡ የተሠሩ ፡ የሚመስሉ ፡ ሰማያዊና ፡ አረንጓዴ ፡ ቀለም ፡ የተ ቀቡ ፡ ጠረጴዛዎች ፡ ይታያሉ ።

እነዚህም ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ በወንበር ፡ ላይ ፡ ሲቀመጡ ፡ ሰይፋንና ፡ ሌላውንም ፡ የንግሡን ፡ መሣሪያ ፡ የሚያሳርፉባቸው ፡ ናቸው ፡ አሉን ።

ከዚህም ፡ ከንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ አጎበር ፡ በስተ ፡ ግራ ፡ ፫ ፡ ሜትር ፡ ያ ህል ፡ አልፎ ፡ የኢቴጌይቱ ፡ አጎበር ፡ ይታያል ። ከመሬት ፡ ከፍታውና ፡ ስፋቱ ፡ የአዕማዱም ፡ አቋቋም ፡ የመውጫውም ፡ ደረጃ ፡ እንደ ፡ ንጉሠ ነገሥቱ ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ የወርቁ ፡ ክፈፍና ፡ የአእዋፉ ፡ ቅርጽ ፤ በየ ማዕዘኑም ፡ ላይ ፡ ያለው ፡ የወርቁ ፡ ጌጥ ፤ ልዩ ፡ ነው ። በመካከሉም ፡ ላይ ፡ አንገተ ፡ ረጅሙ ፡ አሞራ ፡ የለበትምና ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ የዙፋኑ ፡ ከፍታ ፡ ከእቴጌይቱ ፡ የሚለየው ፡ በዚህ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ በዚህ ፡ አጎበር ፡ ውስጥ ፡ በወንበር ፡ ተቀምጠው ፡ የሚታዩት ፡ የዘውድ ፡ በዓል ፡ በሚደረግበት ፡ ቀን ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በሌላ ፡ ቀን ፡ በዚያ ፡ ላይ ፡ አይቀመጡም ።

ትልቁ ፡ ንጉሠ፡ነገሥት ፡ ሚጂ ፡ የተወለደበትና ፡ የነገሠበት ፡ በዚሁ ፡ በኪዎቶ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፤ አሁን ፡ እርሱን ፡ ስለ ፡ ማክበር ፡ ልጁ ፡ ቴሾና ፡ የልጅ ፡ ልጁ ፡ የዛሬው ፡ ንጉሠ ፡ነገሥት ፡ ግርማዊ ፡ ሒሮሂቶ ፡ ሥርዓተ ፡ ንግሥ ፡ ያደረሱት ፡ በዚሁ ፡ በኪዎቶ ፡ ከተማ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

በሀገራችን ፡ በኢትዮጵያም ፡ ነገሥታቱ ፡ በትግሬ ፡ በነበሩበት ፡ ዘመ ን ፡ ሥርዓተ ፡ ንግሥ ፡ የሚያደርሱት ፡ በአክሱም ፡ ነበር ።

አሁንም ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ መኖሪያ ፡ ዋና ፡ ከተማ ፡ አዲስ ፡ አበባ፡ እንዲሆን ፡ በሕግ ፡ ስለ ፡ ተወሰነ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ለሚነግሡ ፡ ነገሥታት፡ ሥ ርዓተ ፡ ንግሥ ፡ የሚደረግላቸው ፡ በአዲስ ፡ አበባ ፡ ከተማ ፡ ነው ። አንዳ ንድ ፡ ሰዎች ፡ ለኢትዮጵያ ፡ ነገሥታት ፡ ሥርዓተ ፡ ንግሥ ፡ የሚደረግላቸ ው ፡ በአክሱም ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እያሉ ፡ ይናገራሉ ።

ነገር ፡ ግን ፡ ይህን ፡ የመሰለው ፡ ነገር ፡ በማናቸውም ፡ ታሪክ ፡ ተጽፎ ፡ አይገኝም ።



በኪዮቶ ፡ ከተማ ፡ እንግድነት ፡ የተቀበለን ፡ ወዳጃችን ፡ ሙሴ ፡ ኢንባታና ፡ ልጆቹ ።

ነገሥታቱ ፡ በትግሬ ፡ በነበሩበት ፡ ዘመን ፡ ሥርዓተ ፡ ንግሥ ፡ የሚደረግላቸው ፡ በአክሱም ፡ መሆኑ ፡ እርግጥ ፡ ነው ። የነገሥታቱ ፡ መኖሪያ ፡ በፊት ፡ በሸዋ ፣ ቀጥሎም ፡ በጎንደር ፡ በነበረ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ በዚያው ፡ በየ ዋናው ፡ ከተማቸው ፡ ቅብዓ ፡ መንግሥት ፡ እየተቀበሉ፡ ከመንገሥ ፡ በቀር ፡ ወደ ፡ አክሱም ፡ አይሔዱም ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ አንዳንድ ፡ ነገሥታት ፡ ግብር ፡ ለመቀበልና ፡ አገር ፡ ለማየት ፡ ወደ፡ትግሬ ፡ በሔዱ ፡ ጊዜ ፡ ወደ፡ አክሱም ፡ ሲገቡ ፡ ዘውድ ፡ ጭነው ፡ በሥርዓተ ፡ መንግሥት ፡ ሆነው ፣ እንደ ፡ ሀገሩ ፡ ልማድ ፡ በአክሱም ፡ ቅጥር ፡ ግቢ ፡ ወርቅ ፡ እየበተኑ ፣ ደናግል ፡ የሚይዙትን ፡ የሐር ፡ ገመድ ፡ በሰይፋቸው ፡ እየቆረጡ ፡ ይገቡ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ የፊተኛው ፡ ቅብዓ ፡ መንግሥት ፡ የማይጠቅም ፡ ሆኖ ፡ ሁለተኛ ፡ በአክሱም ፡ ቅብዓ ፡ መንግሥት ፡ መቀባታቸውን ፡ የሚያስረዳ ፡ አንድ ፡ እንኳ ፡ ታሪክ ፡ አይገኝም ።

የንጉሠ ፡ ነገሥቱንም ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ካየን ፡ በኋላ ፡ የአልጋ፡ ወራሹን ፡ ቤት ፡ ለማየት ፡ ሔድን ።

የቤቱ ፡ ሥራ ፡ ማማር ፡ ከቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ቢበልጥ ፡ እንጂ ፡ አያንስም ። የተሠራውም ፡ ከዛሬ ፡ ፫፻ ፡ ዓመት ፡ በፊት ፡ ነው ። የሠራውም ፡ ቶኮጋዋ ፡ የሚባለው ፡ እጅግ ፡ ኃይለኛና ፡ ባለጠጋ ፡ የነበረው ፡ መስፍን ፡ ነበር ። ከዚያ ፡ ጀምሮ ፡ ወደ ፡ ኪዮቶ ፡ ለሚመጡ ፡ መሳፍንት ፡ ማረፊያ ፡ ሆኖ፡ ሲኖር ፡ በ፲፰፻፺፱ ፡ ዓ ፡ ም ፡ ትልቁ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂ ፡ ሕገ ፡ መንግሥት ፡ ሲያቆም ፡ ቤቱ ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ቤተ ፡ ዘመዶች ፡ እንዲሆን፡ ስለ ፡ ተፈቀደ ፡ በኪዮቶ ፡ የአልጋ ፡ ወራሹ ፡ ማረፊያ ፡ ቤት ፡ ይሁን ፡ ተብሎ ፡ አልጋ ፡ ወራሾቹ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ኪዮቶ ፡ ሲመጡ ፡ የሚያርፉበት ፡ በዚህ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

---

## ምዕራፍ ፲፰ ።

በኅዳር ፡ ፲፩ቀን ፡ ከጧቱ ፡ በ፩ሰዓት ፡ ተነሥተን ፡ በትልቁ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ በሚጂ ፡ መቃብር ፡ ላይ ፡ አበባ ፡ ለማስቀመጥ ፡ ሔድን ።

ሚጂ ፡ ትልቁ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የተባለበት ፡ ስለ ፡ ሁለት ፡ ነገር ፡ ነው ።

፩ኛው ፡ ነገር ፡ ማናቸውም ፡ ሥራና ፡ ሥልጣኔ ፡ ብልጥግናም ፡ ያለትምሕርት ፡ እንዳይሆን ፡ አውቆ ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ ገንዘብ ፡ ያለው ፡ በገንዘቡ ፣ ገንዘብ ፡ የሌለው ፡ በመንግሥት ፡ ገንዘብ ፡ ልጁን ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አገር ፡ እየሰደደ ፡ እንዲያስተምር ። በገሩም ፡

ውስጥ ፡ በየከተማውና ፡ በያውራጃው ፡ የትምሕርት ፡ ቤት ፡ እንዲቆም፡አ ዋጅ ፡ አድርጎ ፡ የጃፓን ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ እንዲማሩ ፡ ስለ ፡ አደረገ ፡ ነው ።

፪ተኛው ፡ ነገር ። የጃፓን ፡ አገር ፡ በመሳፍንት ፡ ተከፍሎ ፡ ንጉሡ ፡ በስም ፡ ብቻ ፡ ገዥ ፡ ተብሎ ፡ መሳፍንቱ ፡ እንደ ፡ ፈቃዳቸው ፡ እየገዙ ፡ በጣም ፡ ተጨንቆና ፡ ተበድሎ ፡ ነበርና ፡ ይህን ፡ የመሰለው ፡ አገዛዝ ፡ ባገሩ ፡ ላይ ፡ ጥፋት ፤ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ጉዳት ፡ እንዲያመጣ ፡ አውቆ ፡ በፈቃዱ ፡ ሕገ ፡ መንግሥት ፡ አቁሞ ፡ ሕዝቡን ፡ ከክፉ ፡ አገዛዝ ፡ ነጻ ፡ ስለ ፡ አወጣቸው ፡ ለመሳፍንቱም ፡ የሚበቃ ፡ ትዳር ፡ ሰጥቶ ፤ የጠሩን ፡ ኃይል ፡ አበርትቶ ፤ አንድነትን ፡ አጽንቶ ፡ ጃፓን ፡ በነጻነቷ ፡ እንድት ኖር ፡ ስለ ፡ አደረገ ፡ ነው ።

በእርሱም ፡ ዘመን ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ አጤ ፡ ምኒል ክ ፡ ነበሩ ። በጃፓን ፡ አገር ፡ ሚጂ ፡ ትልቁ ፡ ንጉሥ ፡ እንደሚባል ፡ በኢትዮጵያም ፡ አጤ ፡ ምኒልክ ፤ እስካሁን ፡ ድረስ ፡ ትልቁ ፡ ንጉሥ ፡ ሲባሉ ፡ ይኖራሉ ። ትልቁ ፡ ንጉሥ ፡ የተባሉትም ፡ ስለ ፡ አራት ፡ ነገ ሮች ፡ ነው ።

፩ኛው ፡ ነገር ። ከአጤ ፡ ምኒልክ ፡ አስቀድሞ ፡ የነበሩት ፡ ነገሥታት ፡ እግዚአብሔር ፡ ለጻድቃንና ፡ ለኃጥአን ፤ ለደጎቹና ፡ ለክፎቹም ፡ በትክ ክል ፡ ፀሐይ ፡ ማውጣቱን ፤ ዝናም ፡ ማዝነሙን ፡ እያሰቡ ፡ ሕዝባቸ ውን ፡ በትክክል ፡ በመግዛትና ፡ በመጠበቅ ፡ ፋንታ ፡ በሃይማኖት ፡ ነገ ር ፡ አንተ ፡ እስላም ፡ ነህ ፤ አንተ ፡ ፈላሻ ፡ ነህ ፤ አንተ ፡ አረማዊ ፡ ነህ ና ፡ በግድ ፡ እየተጠመቅህ ፡ ክርስቲያን ፡ ሁን ፡ እያሉ ፡ አልጠመቅም ፡ ክርስቲያንም ፡ አልሆንም ፡ ያለውን ፡ እየገረፉ ፡ እየቆረጡ ፤ ርስቱን ፡ እየነቀሉ ፤ ካገር ፡ እያሳደዱ ፡ ይኖሩ ፡ ነበርና ፡ አጤ ፡ ምኒልክ ፡ በነገው ፡ ጊዜ ፡ ይህን ፤ የመሰለ ፡ የጭካኔ ፡ ሥራ ፡ በእግዚአብሔርም ፤ በሕዝቡ ም ፡ ዘንድ ፡ ያልተወደደ ፡ መሆኑን ፡ አይተው ፡ እንደ ፡ አባትህ ፡ በየ ሃይማኖትህ ፡ እንድትኖር ፡ ፈቅጄልሃለሁ ፡ ብለው ፡ አዋጅ ፡ ነግረው ፡ በዕረፍትና ፡ በሰላም ፡ እንዲኖር ፡ ስለ ፡ አደረጉ ፡ ነው ።

፪ተኛው ፡ ነገር ። ከአጤ ፡ ምኒልክ ፡ አስቀድሞ ፡ የነበሩ ፡ ነገሥታ ት ፡ ወታደሩን ፡ በየባላገሩ ፡ ቤት ፡ ምሪት ፡ እየሰደዱ ፤ ተሰሪ ፡ እየሆነ ፡ በየቤቱ ፡ እየገባ ፡ ባላገሩን ፡ እያስጨነቀ ፤ ገንዘቡን ፡ እየነጠቀ ፡ ሲ ያስለቅሰው ፡ ይኖር ፡ ነበርና ፡ አጤ ፡ ምኒልክ ፡ ሲነግሡ ፡ ይህ ን ፡ ሁሉ ፡ ክፉ ፡ ልማድ ፡ አስቀርተው ፡ ባላገሩ ፡ እህል ፡ እያወጣ ፡

ለወታደር ፡ እንዲሰጥ ፡ እንጂ ፡ ወታደር ፡ ወደባላገር ፡ ቤት ፡ ምሪተኛ ፡ ተሰሪ ፡ እየሆነ ፡ እንዳይገባ ፡ ስለ ፡ አደረጉ ፤ ቀጥለውም ፡ ከመሬቱ ፡ ሰብል ፤ አሥራት ፡ እያወጣ ፡ እንዲሰጥ ፡ አዋጅ ፡ ስለ ፡ አደረጉና ፡ ሕዝ ቡን ፡ ደስ ፡ ስላለው ፡ ነው ።

፫ኛው ፡ ነገር ። ከብት ፡ ባለቀበት ፤ ወታደሩና ፡ ባላገሩም ፡ ገንዘብ ፡ በተቸገረበት ፡ ዘመን ፡ የዳር ፡ አገሩን ፡ ሁሉ ፡ ማቅናት ፡ ጀምረው ፡ ነበ ርና ፡ ለወታደሩ ፡ የምርኮውን ፡ ከብትና ፡ ገንዘብ ፡ ስለ ፡ መረቁለት ፡ ለባ ላገሩም ፡ ከምርኮው ፡ ከብትና ፡ ገንዘብ ፡ ስለ ፡ ሰጡትና ፡ ደስ ፡ ስለ ፡ አሰኙት ፡ ነው ።

፬ኛው ፡ ነገር ። ከውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ ጦርነት ፡ ለማድረግ ፡ ሳይፈልጉ ፡ በግድ ፡ ቢመጣባቸው ፡ ስለ ፡ ሀገራቸው ፡ ነጻነት ፡ ሲከላከሉ ፡ አድዋ ፡ ላይ ፡ ከኢጣልያ ፡ ጋራ ፡ ተዋግተው ፡ ድል ፡ ስለ ፡ አደረጉ ፡ ነው ።

በዚህም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ኢትዮጵያና ፡ አውሮጳ ፡ እንዲገናኙ ፡ አድ ርገው ፡ በኢትዮጵያ ፡ የአውሮጳ ፡ ሥልጣኔና ፡ የንግድ ፡ ዕቃ ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ እንዲገባ ፡ ስለ ፡ ተጀመረ ፤ ለውጭ ፡ አገርም ፡ ቋንቋ ፡ መማ ሪያ ፡ የትምሕርት ፡ ቤት ፡ እንዲቆም ፡ ስለ ፡ አደረጉ ፡ ትልቁ ፡ ንጉሥ ፡ ምኒልክ ፡ መባልን ፡ አገኙ ።

በማናቸውም ፡ ቢሆን ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የአፄ ፡ ም ኒልክና ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የሚጂ ፡ ሥራ ፡ በብዙ ፡ ነገር ፡ በ ጣም ፡ ይመሳሰላል ።

በኢትዮጵያ ፡ ስልክና ፡ ፖስታ ፡ የቆመው ፤ የምድር ፡ ባቡር ፡ ሥ ራና ፡ ከውጭ ፡ አገር ፡ መንግሥቶች ፡ ጋራ ፡ የንግድና ፡ የወዳጅነት ፡ ውል ፡ መዋዋል ፡ የተጀመረው ፡ በአፄ ፡ ምኒልክ ፡ ዘመን ፡ ነው ። በ ጃፓንም ፡ ይህን ፡ የመሰለው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ የተጀመረው ፡ በንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂ ፡ ዘመን ፡ ነው ።

ዘመነ ፡ መንግሥታቸውም ፡ በጣም ፡ የተቃረበ ፡ ነው ። አፄ ፡ ምኒ ልክ ፡ በሺ ፰፻፵፯ ፡ ዓመ ፡ ምሕ ፡ ንጉሠ ፡ ሸዋ ፡ ተብለው ፡ ነገሡ ። ሚ ጂም ፡ የነገሡው ፡ በሺ ፰፻፷፩ ፡ ዓመ ፡ ምሕ ፡ ነው ። አፄ ፡ ምኒልክ ፡ ንጉሥ ፡ ከተባሉበት ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ ፵፯ ዓመት ፡ ገዝተው ፡ አረፉ ። ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂም ፡ ያረፈው ፡ ፵፭ ዓመት ፡ ገዝቶ ፡ ነው ።

በዚያ ፡ ዘመን ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ ነግሠው ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ ስማቸው ፡ የተጠራው ፡ በኢትዮጵያ ፡ አፄ ፡ ምኒልክ ። በእንግሊዝ ፡ ንግሥት ፡ ቢክቶሪያ ። በጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂ ፡ እነዚህ ፡ ሶስቱ ፡ ነበሩና ፡ እጅግ ፡ መታደል ፡ ነው ።

እኛም ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መላክተኞች ፡ ሆነን ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ ሔደን ፡ ኪዮቶ ፡ ስለ ፡ መድረሳችን ፡ እንደ ፡ ሌሎች ፡ ነገሥታት ፡ መላክተኞች ፡ ደንብ ፡ በትልቁ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ በሚጂ ፡ መቃብር ፡ ላይ ፡ አበባ ፡ ለማስቀመጥ ፡ ሔድን ።

መቃብሩም ፡ ከኪዮቶ ፡ ከተማ ፡ አጠገብ ፡ ባለው ፡ ዱር ፡ ውስጥ ፡ በትንሽ ፡ ተራራ ፡ ጥግ ፡ ነው ።

ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂ ፡ በሕይወቱ ፡ ሳለ ፡ በኪዮቶ ፡ ከተማ ፡ ዙሪያ ፡ በዱር ፡ ውስጥ ፡ እየተዛወረ ፡ አገር ፡ ሲያይ ፡ አሁን ፡ በተቀበረበት ፡ ስፍራ ፡ ሲደርስ ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ዱርና ፡ መልካም ፡ ሥፍራ ፡ በሌላ ፡ ዘንድ ፡ አላየሁም ፡ እያለ ፡ ስፍራውን ፡ አመስግኖ ፡ ተናግሮ ፡ ነበርና ፡ ኪዮቶን ፡ ትቶ ፡ ቶኪዮን ፡ ዋና ፡ ከተማ ፡ አድርጎ፡ሲኖር፡ቶኪዮ ፡ ላይ በሞተ ፡ ጊዜ ፡ ይህን ፡ አሁን ፡ የተቀበረበትን ፡ ስፍራ ፡ ሲያመሰግን ፡ የሰሙ ፡ ሰዎች ፡ ነገሩን ፡ ስለ ፡ ተናገሩ ፡ የተወለደውም ፡ ሥርዓተ ፡ ንግሥ ፡ ያደረሰውም ፡ በኪዮቶ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በዚያው ፡ እርሱ ፡ ባመሰገነው ፡ ስፍራ ፡ ይቀበር ፡ ተብሎ ፡ ከቶኪዮ ፡ አምጥተው ፡ ቀብረውታል ።

በመቃብሩ ፡ ላይ ፡ ቤት ፡ አልተሠራም ፡ ነገር ፡ ግን ፡ የተራራውን ፡ ጥግ ፡ በሰፊው ፡ ቆፍረው ፡ ዋሻ ፡ አድርገው ፡ ላዩን ፡ በድንጋይ ፡ ከረትና ፡ በሲሚንቶ ፡ እያደረጉ ፡ በፍጥረቱ ፡ የተቆለለ ፡ ድንጋያማ ፡ መሬት ፡ አስመስለው ፡ ሠርተውታል ።

ከበሩ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ መቃብሩ ፡ ድረስ ፡ መንገዱ ፡ በወንዝ ፡ አሸዋ ፡ የተሠራ ፡ እጅግ ፡ ያማረና ፡ የሰፋ ፡ ግራና ፡ ቀኙም ፡ በዛፍና ፡ በበባ ፡ ያጌጠ ፡ ነው ።

በቀን ፡ በቀኑ ፡ የከተማው ፡ ሕዝብ ፡ ወንዱም ፡ ሴቱም ፡ የሚጂን ፡ መቃብር ፡ ለመሳለም ፡ የሚሔዱ ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ናቸው ። ቢሆንም ፡ ገና ፡ አንድ ፡ ኪሎ ፡ ሜትር ፡ ሲቀረው ፡ ከአውቶሞቢል ፡ ወርደው ፡ በእግራቸው ፡ ይሔዳሉ ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ ቅጥሩ ፡ ውስጥ ፡ በአውቶሞቢል ፡ ለመግባት ፡ አይፈቀድላቸውም ።



Tomb of Emperor Meiji, at Momoyama near Kyoto

በኪዮቶ ፡ ከተማ ፡ ዳር ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂ ፡ መቃብር ።

እኛም ፡ ከደጀ ፡ ሰላሙ ፡ ስንደርስ ፡ እንደ ፡ ሕጋቸው ፡ በጠበሉ ፡ ውሀ ፡ እጃችሁን ፡ ታጠቡ ፡ ብለውን ፡ ከታጠብን ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ መቃብሩ ጉዞ ፡ ጀመርን ። አደራረጉንም ፡ ሁሉ ፡ የሚያስረዳን ፡ የመታሰቢያው ፡ ቤት ፡ ዘበኞች ፡ አለቃ ፡ የማዕርግ ፡ ልብሱን ፡ ለብሶ ፡ በፊት ፡ በፊታችን ፡ ይሔድ ፡ ነበር ።

ወደ ፡ መቃብሩ ፡ ለመቅረብ ፡ ገና ፡ ሶስት ፡ መቶ ፡ ሜትር ፡ ያህል ፡ ሲቀረን ፡ የዘበኞቹ ፡ አለቃ ፡ ባርኔጣውን ፡ ሲያወልቅ ፡ አይተን ፡ እኛም ፡ አውልቀን ፡ በእጃችን ፡ ያዝን ። አደራረጉና ፡ አከባበሩም ፡ ሁሉ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂ ፡ በሕይወቱ ፡ ሳለ ፡ እንደሚደረግለት ፡ ነውና ፡ መሬቱን ፡ ስትረግጡ ፡ ስትናገሩም ፡ በቀስታ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ነገረን ።

መቸም ፡ ወደ ፡ መቃብሩ ፡ ድረስ ፡ ለመግባት ፡ ለማንም ፡ አይፈቀድለትምና ፡ እኛ ፡ አስቀድመን ፡ የላክነውን ፡ አበባ ፡ ከመቃብሩ ፡ አምሳ ፡ ሜትር ፡ ያህል ፡ እርቆ ፡ በወለሉ ፡ ላይ ፡ ከመሬት ፡ ከፍ ፡ አድርገው ፡ ሰቅለው ፡ አቆይተውን ፡ ነበር ። ከዋናውም ፡ ቀጥር ፡ ስንደርስ ፡ የዘበኞቹ ፡ አለቃ ፡ ወደ ፡ መቃብሩ ፡ እጅ ፡ ነሥቶ ፡ ቆመ ። እኛም ፡ አበባው ፡ ወደ ፡ ተሰቀለበት ፡ ድረስ ፡ ሔደን ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ በሕይወቱ ፡ ሳለ ፡ እንደሚደረግለት ፡ እጅ ፡ ነሥተን ፡ የኋሊት ፡ እያፈገፈግን ፡ ወደ ፡ ደረጃው ፡ ተመለስን ፡ ከዚያም ፡ ሶስት ፡ መቶ ፡ ሜትር ፡ ያህል ፡ አልፈን ፡ ወደ ፡ እቴጌይቱ ፡ መቃብር ፡ ሔድን ።

የእቴጌይቱም ፡ መቃብር ፡ ሥራው ፡ ልክ ፡ እንደ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ መቃብር ፡ ነው ። ወደዚያም ፡ አበባችን ፡ ቀድሞ ፡ ተልኮ ፡ ነበርና ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ መቃብር ፡ እንደ ፡ አደረግነው ፡ አከባበር ፡ አደረግን ።

ወዲያውም ፡ እቴጌይቱ ፡ የሞቱት ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ በሞተ ፡ በ፪ኛው ፡ ወር ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ነገሩን ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ኪዮቶ ፡ የምንመለስበት ፡ ሰዓት ፡ ደርሶ ፡ ነበርና ፡ እግረ ፡ መንገዳችንን ፡ የሐሩን ፡ ፋብሪካ ፡ አይተን ፡ ተመለስን ።

በኅዳር ፡ ፲፪ ፡ ቀን ፡ በኪዮቶ ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ወጥተን ፡ የኪዮቶን ፡ ከተማ ፡ ቍልቍል ፡ ለማየት ፡ በኤሌክትሪክ ፡ ኃይል ፡ በሚሔድ ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ገብተን ፡ ወጣን ። የተራራው ፡ ርዝመት ፡ ከአዲስ ፡ አበባ ፡ ጥግ ፡ እንደ ፡ እንጦጦ ፡ ራጉኤል ፡ ይሆናል ። አቀበቱም ፡ እንደ ፡ ሽምበቆ ፡ ቀጥ ፡ ያለ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ጋደም ፡ ብሎ ፡ የወጣ ፡ አይደለም ። በኤሌክትሪኩም ፡ ኃይል ፡ በ፱ ፡ ደቂቃ ፡ ከአፋፉ ፡ ደረስን ። በዚያም ፡ ጥቂ

ት ፡ ቆይተን ፡ ሁለተኛውን ፡ ተራራ ፡ ለማየት ፡ ጥቂት ፡ መንገድ ፡ በእግራችን ፡ ከሔድን ፡ በኋላ ፡ ሌላ ፡ የኤሌክትሪክ ፡ መኪና ፡ ከቆመበት ፡ ደረስን ። በዚያም ፡ ካንዱ ፡ ተራራ ፡ ወደ ፡ ሌላው ፡ ተራራ ፡ ወፍራም ፡ የብረት ፡ ገመድ ፡ ተዘርግቶ ፡ ይታያል ። ወዲያውም ፡ ሞላልነቱ ፡ ፫ ፡ ሜትር ፤ ጎድኑ ፡ ፬ ፡ ሜትር ፡ በሚሆን ፡ በትንሽ ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ከገባን ፡ በኋላ ፡ መኪናውን ፡ ቢያስነሣው ፡ በብረቱ ፡ ገመድ ፡ ላይ ፡ እየተሽከረከረ ፡ እንደ ፡ አይሮፕላን ፡ በአየሩ ፡ ላይ ፡ ወስዶ ፡ ከወዲያኛው ፡ ተራራ ፡ አደረሰን ።

ምሳሌ ። አንደኛው ፡ ተራራ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ በቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ግቢ ፡ ላይ ፡ ሆኖ ፡ ሁለተኛው ፡ ተራራ ፡ አራዳ ፡ ገበያ ፡ ላይ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ከዚያም ፡ ስንወርድ ፡ ወንዶችም ፡ ሴቶችም ፡ የድሮውን ፡ የጃፓንን ፡ የኀይልና ፡ የጦርነት ፤ ሌላም ፡ የጅምናስቲክ ፡ ትምሕርት ፡ የሚማሩበትን ፡ ለማየት ፡ ወደ ፡ ክለቡ ፡ ሔድን ። ክሉብ ፡ ማለት ፡ የማኅበር ፡ ቤት ፡ ማለት ፡ ነው ። የማኅበሩም ፡ ቍጥር ፡ ፫ ፡ ሚሊዮን ፡ ነው ። ነገሥታቱ ፡ እንኳ ፡ ይህንኑ ፡ የኀይልና ፡ የጦርነት ፡ ትምሕርት ፡ ለማየት ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ይመጣሉ ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

ያሳዩንም ፡ የጦርነትና ፡ የኀይል ፡ ትምሕርት ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ያለው ፡ ነው ።

፩ኛ ። በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ ሴቶች ፡ ወደ ፡ ጦርነት ፡ እየሔዱ ፡ ይዋጉ ፡ ነበርና ፡ አሁንም ፡ እንደዚያው ፡ የቀድሞውን ፡ ዘመን ፡ ጦርና ፡ ጐራዴ ፡ የሚመስል ፡ የእንጨት ፡ ጦርና ፡ ጐራዴ ፡ አበጅተው ፡ በወለሉ ፡ ላይ ፡ ያጋጥሟቸዋል ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ በጨበጣ ፡ ሲዋጉና ፡ ጦር ፡ ለጦር ፡ ሲመካከቱ ፤ በጐራዴም ፡ ሲማቱና ፡ ጐራዴ ፡ ለጐራዴ ፡ ሲመካከቱ ፡ ሰውነታቸውንም ፡ ሲጠብቁ ፡ ማየት ፡ በጣም ፡ ያስደንቃል ።

በብዙ ፡ ብልሃት ፡ አንዱ ፡ በጦሩ ፡ ወይም ፡ በጐራዴው ፡ የሌላውን ፡ ሰው ፡ አካል ፡ ሲነካ ፡ አሸነፈ ፡ ይባላል ።

፪ኛ ። በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ በቀስት ፡ ይዋጉ ፡ ነበርና ፡ የቀስቱ ፡ አሸካከምና ፡ የደጋኑ ፡ አያያዝ ፤ የማነጣጠሪያውም ፡ አደራረግ ፡ እንደ ፡ ቀድሞው ፡ ሆኖ ፡ በሩቅ ፡ የላስቲክ ፡ ኢላማ ፡ ተሰቅሎ ፡ ቀስቱን ፡ ለጥጦ ፡ የይላማውን ፡ መካከል ፡ የወጋ ፡ እንደሆነ ፡ አሸነፈ ፡ ይባላል ።

ይህንም ፡ ሁሉ ፡ ካየን ፡ በኋላ ፡ የክለቡን ፡ (የማኅበሩን ፡) አለቃ ፡ ይህን ፡ የመሰለው ፡ ጦርነት ፡ መቼም ፡ በዛሬ ፡ ዘመን ፡ አይደረግም ፤ እንግዴህ ፡




Practising Fencing

በኪዮቶ ፡ ከተማ ፡ የቀድሞውን ፡ ዘመን ፡ ጦርነት ፡ የሚማሩ ፡ ሴቶች ።

የዚህ ፡ ትምሕርት ፡ ፍሬ ፡ ነገሩና ፡ ጥቅሙ ፡ ምንድነው ፡ ብዬ ፡ ብጠይቀው ፡ ሶስት ፡ ጥቅም ፡ ይገኝበታልና ፡ ዋና ፡ ትምሕርት ፡ ነው ።

፩ኛው ፡ ጥቅም ። ሕዝቡ ፡ ወንዱም ፡ ሴቱም ፡ የቀድሞ ፡ ያባቶቻቸውን ፡ ልማድ ፡ ማየትና ፡ እንደዚሁ ፡ ተዋግተው ፡ አገራቸውን ፡ በነጻ ፡ ማቆየታቸውን ፡ ማወቅ ፡ ነው ።

፪ኛው ፡ ጥቅም ። የሕዝቡ ፡ መንፈስ ፡ ዘወትር ፡ የጦርነት ፡ ነገር ፡ በማሰብና ፡ በማወቅ ፡ እየተንቀሳቀሰ ፡ የኖረ ፡ እንደሆነ ፡ ብርታትን ፡ ይለምዳልና ፡ በጦርነት ፡ ጊዜ ፡ ልቡ ፡ አይፈራበትም ።

፫ኛው ፡ ጥቅም ። ማንም ፡ ሰው ፡ ቢሆን ፡ ይህን ፡ በመሰለ ፡ ነገር ፡ ወይም ፡ በሌላ ፡ ሥራ ፡ ሰውነቱን ፡ ካላንቀሳቀሰ ፡ ደሙ ፡ እየረጋ ፡ ደካማና ፡ በሽተኛ ፡ ሰነፍ ፡ ይሆናልና ፡ ሰውነቱን ፡ ለማበርታት ፡ ነው ።

ሴቶችንም ፡ በጦርነት ፡ ጊዜ ፡ ለመዋጋትም ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ በጦርነት ፡ የቆሰሉትን ፡ ወታደሮች ፡ ለማስታመምና ፡ ለመርዳትም ፡ ቢሆን ፡ ደፋሮችና ፡ ብርቶች ፡ እያደረጉ ፡ ማቆየት ፡ የሚያስፈልግ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ መለሰልኝ ።

ባገራችን ፡ በኢትዮጵያም ፡ በጎጃምና ፡ በቤጌምድር ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ይህን ፡ የመሰለውን ፡ የበትር(የሽመል)አመካከት ፡ ስለ ፡ ለመዱ ፡ በማዘንጋት ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ አንዱ ፡ አንዱን ፡ በበትር ፡ ሊመታው ፡ አይችልም ። ስለዚህ ፡ ያመካከት ፡ ትምሕርት ፡ ማወቅ ፡ ለድንገተኛ ፡ አደጋ ፡ የሚጠቅም ፡ መሆኑን ፡ ይህ ፡ ያስረዳል ።

በዚሁም ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ማታ ፡ በኪዮቶ ፡ ያለው ፡ የትልቁ ፡ ሲኒማ ፡ ኩምፓንያ ፡ ዲሬክተር ፡ የሲኒማውን ፡ መኪና ፡ አይተን ፡ ወዳያውም ፡ ሻይ እንድንጋበዝለት ፡ ለምኖን ፡ ነበርና ፡ ወደዚያ ፡ ሔድን ።

ገና ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሳንገባ ፡ በበሩ ፡ ደጃፍ ፡ ላይ ፡ ብዙ ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ እኩሉ ፡ የሥራ ፡ ልብስ ፡ እኩሉም ፡ የበዓል ፡ ልብስ ፡ እየለበሱ ፡ ቆመው ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ እየተጣሉ ፡ በጡጫም ፡ በበትርም ፡ ሲማቱ ፡ አይተን ፡ ለጊዜው ፡ በእውነት ፡ የሚጣሉ ፡ መስሎን ፡ ነበር ። በኋላ ፡ ግን ፡ የሲኒማውን ፡ መኪና ፡ ባጠገባቸው ፡ በመንኰራኵር ፡ እያሽከረከሩ ፡ ሲወስዱት አይተን ፡ ሲኒማ ፡ መሆኑን ፡ ተረዳነው ።

ወደ ፡ ቤትም ፡ ውስጥ ፡ በገባን ፡ ጊዜ ፡ አንድ ፡ መስፍን ፡ እንደ ፡ ቀድሞ ፡ የጃፓን ፡ መስፍኖች ፡ የመስፍን ፡ ልብስ ፡ ለብሶ ፡ በስተኋላው ፡ ሁለቱን ፡ ባለሟሎቹን ፡ አስቀምጦ ፡ ዘበኞቹን ፡ ጦርና ፡ ጐራዴ ፡ እንደያዙ ፡ ዙሪያውን ፡ አቁሞ ፡ ቆነጃጅት ፡ ሴቶች ፡ ክራር ፡ እያስመቱ ፡ ሲያዘፍን ፡

በመካከሉ ፡ አምባጓሮ ፡ ተነሥቶ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ጐራዴ ፡ መዞ ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ዘበኞቹ ፡ ጌታቸውን ፡ ለማዳን ፡ ሲከላከሉ ፤ ያም ፡ አምባጓሮ ፡ ያነሣው ፡ ሰው ፡ በኃይል ፡ ገብቶ ፡ ዘበኞቹን ፡ ሁሉ ፡ እያስፈራራ ፡ በፍርሃት ፡ ጐራዴ ያቸው ፡ ከእጃቸው ፡ ሲወድቅና ፡ በፍርሃት ፡ ሲንቀጠቀጡ ፡ መስፍኑም ፡ የዘበኞቹን ፡ ፍርሃት ፡ በማየቱ ፡ ሲጨነቅ ፡ ሲኒማ ፡ እያነሡ፣ አሳዩን ።

እኛ ፡ ሲኒማ ፡ ሲባል ፡ በድንገት ፡ ያየውንና ፡ የገጠመውን ፡ እውነቱን ፡ ነገር ፡ እያነሣ ፡ የሚያሳይ ፡ ይመስለን ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ እንደዚህ ፡ በምሳሌ ፡ እየሠሩ ፡ የሚያሳዩ ፡ አይመስለንም ፡ ነበርና ፡ አሁን ፡ ከሲኒማ ፡ የሚበዛው ፡ ምሳሌ ፡ እንጂ ፡ በእርግጥ ፡ የተደረገ ፡ ነገር ፡ አለመሆኑን ፡ ተረዳነው ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ሻዩ ፡ ወደ ፡ ተዘጋጀበት ፡ ቤት ፡ ገብተን ፡ ተጋብዘን ፡ ስንወጣ ፡ በበሩ ፡ ላይ ፡ ፎቶግራፍ ፡ ተነሥተን ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ተመለስን ።

---

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

## ወደ ፡ ናራ ፡ ስለ ፡ መሔዳችን ።

ናራ ፡ በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ የጃፓን ፡ ነገሥታት ፡ ዋና ፡ ከተማ ፡ ነበር ። አሁን ፡ ግን ፡ የመናፈሻና ፡ የዕረፍት ፡ ከተማ ፡ የቡዳሃና ፡ የሽንቶ ፡ ካህናት ፡ ገዳም ፡ ሆኗል ።

በኪዮቶ ፡ ከተማ ፡ አራት ፡ ቀን ፡ ተቀምጠን ፡ ነበርና ፡ በኅዳር ፡ ፲፫ ፡ ቀን ፡ ከኪዮቶ ፡ በ፬ ፡ ሰዓት ፡ ተነሥተን ፡ በ፭ ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ናራ ፡ ከተማ ፡ ደረስን ።

የናራ ፡ አገረ ፡ ገዥና ፡ የከተማው ፡ ከንቲባ ፡ ከከተማው ፡ ትልልቆች ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ እስከ ፡ ባቡር ፡ መቋሚያ ፡ መጥተው ፡ ተቀበሉን ። ከዚያም ፡ ወደ ፡ ናራ ፡ ሆቴል ፡ ገብተን ፡ ጥቂት ፡ ካረፍን ፡ በኋላ ፡ አገረ ፡ ገዥው ፡ መጥቶ ፡ በናራ ፡ ያለውን ፡ ትልቁን ፡ የቡዳሃ ፡ መቅደስና ፡ የሽንቶን ፡ ሽራይን ፡ ለማሳየት ፡ ወሰደን ። ወደ ፡ መቅደሱና ፡ ወደ ፡ ሽራይኑም ፡ ሳንደርስ ፡ ወደ ፡ አንድ ፡ ትልቅ ፡ መስክ ፡ ወስደው ፡ አስቀመጡን ። ምክንያቱንም ፡ ብንጠይቅ ፡ አጋዘን ፡ የሚባሉትን ፡ እንስሶች ፡ ለማሳየት ፡ ነው ፡ አሉን ።



በኪዮቶ ፡ ከተማ ፡ በሲኒማ ፡ ፋብሪካ ፡ ቤት ፡ ሻይ ፡ ተጋብዘን ፡ ስንወጣ ።




የናራ ፡ ሆቴል ።



በናራ ፡ ከተማ ፡ ቅዱሳን ፡ አጋዘኖች ፡ የሚሰማሩበት ፡ ሜዳ ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ ትልልቅ ፡ የቡዳሃ ፡ መቅደስና ፡ የሽንቶ ፡ ሽራይን ፡ ባለበት ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ አጋዘን ፡ የሚባሉት ፡ የዱር ፡ እንስሶችና ፡ ርግቦች ፤ አንገተ ፡ ረጃጅም ፡ የባሕር ፡ ዝዪዎችና ፡ አንዳንድ፡ነጭ ፡ ፈረስ፡ያኖራሉ ። ምክንያቱንም፥በንጠይቃቸው፡ቡዳሃ፡የሚባለው ፡ የሃይማኖታችን፡ ጀማሪና፡ አስተማሪ፡ቤቱንና፡ንብረቱን ፤ ሚስቱንና ፡ ልጁን ፡ ትቶ ፡ መንኖ ፡ በሔደ፡ ጊዜ ፡ ባምቡ ፡ በሚባል ፡ ዱር ፡ ውስጥ ፡ በተባሕትዎ ፡ ተቀምጦ ፡ ሳለ ፡ እነዚህ ፡ እንስሶች ፡ እየመጡ ፡ ያጫውቱት ፡ ነበርና ፡ ስለዚህ ፡ ቅዱሳን ፡ እንስሶች ፡ ተብለዋል ፡ ብለው ፡ ነገሩን ። ይኸውም ፡ በገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ ለአቡነ ፡ ገብረ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ አንበሳና ፡ ነብር ፡ ያገለግሏቸው ፡ ነበር ፡ እንደሚባለው ፡ ነው ።

አጋዘን ፡ የሚባለው ፡ እንስሳ ፡ መልኩ ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ ሰስ ፡ ይመስላል ። ቀንዱ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ዛፍ ፡ በየጐኑ ፡ እያቆጠቆጠ ፡ እየወጣ ፡ አንዳንዱ ፡ ሶስት ፡ ቀንድ ፤ አንዳንዱም ፡ አራት ፡ ቀንድ ፤ አንዳንዱም፡ አምስት ፡ ቀንድ ፡ ያለው ፡ ይገኛል ።

ካገራችን ፡ ከኢትዮጵያ ፡ አጋዘን ፡ በቀንዱ ፡ ብዛት ፡ ብቻ ፡ ይለያል፡ እንጂ ፡ በጠጉሩና ፡ በቋቋሙ ፡ አንድ ፡ ነው ። ርግብና ፡ ዝዪም ፡ የዋሃን፡ ፍጥረቶች ፡ ናቸውና ፡ እንደ ፡ ንዋየ ፡ ቅድሳት ፡ ተቆጥረው ፡ በየሽራይኑ ፡ ሊኖሩ ፡ ይገባል ። ፈረሱም ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሚቀመጥበት ፡ ፈረስ ፡ ምሳሌ ፡ ነው ፡ ይላሉ ።

እነዚህም፡ከዚህ ፡ በላይ ፡ የተቆጠሩት ፡ እንስሶችና ፡ አዕዋፍ ፡ ሕይወት፡ያላቸው ፡ ባይሆኑ ፡ እንኳ ፡ ምስላቸውንና ፡ ሥዕላቸውን ፡ ያኖራሉ ።

ትልልቆቹም ፡ ሰዎች ፡ የነገሥታቱ ፡ ልጆች ፡ ሳይቀሩ ፡ እንደ ፡ ስለት ፡ እያደረጉ ፡ አንዳንድ ፡ ፈረስ ፡ ለየሽራይኑ ፡ እየሰጡ ፡ በሽራይኑ፡ ቅጥር ፡ ግቢ ፡ እየታሰረ ፡ ይቀለባል ። የዚህም ፡ ሁሉ ፡ አደራረግ ፡ ጥቂት፡ ጥቂት ፡ ይለይ፡እንጂ ፡ አሳቡ ፡ በእኛ፡በክርስቲያኖች ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፎ ፡ ይገኛል።በዘመነ፡ብሉይ፡ቀይና ፡ ዝንጉርጉር ፤ ነጭና ፤ ጥቁርም ፡ እርግቦች፡ በደብተራ፡ ኦሪት ፡ (በቤተ ፡ መቅደስ፡ )ይኖሩ ፡ ነበር ።

እግዚአብሔር ፡ በነጭ ፡ ፈረስ ፡ ይቀመጣል ፡ ስለ ፡ ማለትም ፡ ትርጓሜው ፡ ሌላ ፡ ይሁን ፡ እንጂ ፡ በንባብ ፡ ነቢዩ ፡ እንባቆም ፡ እስመ ፡ ተጽዕንከ፡ዲበ፡አፍራሲከ፡አፍራሲከኒ፡ሕይወት፡ውእቱ፡ ብሏል ። እንባ፡፫፡፰ ።

ወንጌላዊ ፡ ዮሐንስም ፡ ወወጽአ ፡ ፈረስ ፡ ጸዓዳ ። ወዘይፄእኖ ፡ ቀስት፡ ያፀንእ ፡ ወወሀብዎ ፡ አክሊለ ። ወወጽአ ፡ ከመ ፡ ይማዕ ፡ ወሞዐ ፡ ብሏል ።

ቀጥሎም ፡ ወናሁ ፡ ተርኅወ ፡ ሰማይ ፡ ወወጽአ ፡ ፈረሰ ፡ ፀዓዳ ፡ ወዘይ ፂዓኖ ፡ ስሙ ፡ መሃይምን ፡ ወጻድቅ ፡ ወይጸባዕ ፡ በጽድቅ ፡ ወበርትዕ ። ወአዕይንቲሁ ፡ ከመ ፡ ነደ ፡ እሳት ፡ ወውስተ ፡ ርእሱ ፡ አክሊል ። ወይ ተልውዎ ፡ መላእክት ፡ በአፍራስ ፡ ጸዓድው ፡ ወይለብሱ ፡ አልባሰ ፡ ጽዕ ድወ ። ይላል ። ራዕ ፡ ፲ ፡ ፱ ። ፲፱ ፡ ፲፩—፲፬ ።

ለማስረጃ ፡ ያህል ፡ ይህ ፡ ይበቃል ፡ በማለት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በሌላም ፡ ስፍራ ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ንባብ ፡ አይታጣም ።

ጃፓኖችም ፡ ይህን ፡ የመሰለው ፡ ልማድ ፡ ከቀድሞ ፡ ጀምሮ ፡ የቆያቸው ፡ ይመስላል ።

እነዚህንም ፡ አጋዘኖችና ፡ ርግቦች ፡ ዝዬዎቹንም ፡ አንዳንድ ፡ ሰዎች ፡ እንደ ፡ ስለት ፡ እያመጡ ፡ ለቡዳሃ ፡ መቅደስና ፡ ለሸንቶ ፡ ሸራይን ፡ ይሰጣ ሉ ። በከተማውና ፡ በመቅደሱ ፡ ቅጥር ፡ ግቢ ፡ በማናቸውም ፡ ስፍራ ፡ እየ ተዛወሩ ፡ ሣርና ፡ ሌላም ፡ ያገኙትን ፡ ነገር ፡ እየለቀሙ ፡ ቢበሉ ፡ አይከለከሉም ።

በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ አጋዘኑን ፡ የመታ ፡ ወይም ፡ የገደለ ፡ የሞት ፡ ፍርድ ፡ ይፈረድበት ፡ ነበር ። ከአጋዘኖቹም ፡ መካከል ፡ አንዱ ፡ የሞተ ፡ እንደሆነ ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ የመቃብር ፡ ስፍራ ፡ ተለይቶላቸዋልና ፡ ወደዚያ ፡ ወስደው ፡ ይቀብሩታል ።

በዚህም ፡ ላይ ፡ ደግሞ ፡ የከተማው ፡ ሕዝብ ፡ እንደ ፡ ምጽዋት ፡ እ ያደረገ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አጋዘኖች ፡ እያለ ፡ አታክልትም ፡ ሌላም ፡ የ ሚበላ ፡ ነገር ፡ እየወሰደ ፡ ይሰጣቸዋል ።

ደግሞ ፡ እንጸድቃለን ፡ የሚሉ ፡ ሴቶች ፡ ቂጣ ፡ እየጋገሩ ፡ በሸራ ይኑ ፡ መግቢያ ፡ እየያዙ ፡ ይቆማሉና ፡ ወደ ፡ ሸራይኑ ፡ የሚመጣ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ፔሳ ፡ ከኪሱ ፡ እያወጣ ፡ ቂጣውን ፡ እየገዛ ፡ ይሰጣቸዋል ።

ለአጋዘኖቹም ፡ ሁሉ ፡ ጠባቂና ፡ ሰብሳቢ ፡ አላቸው ። እኛም ፡ እነዚ ህኑ ፡ ለማየት ፡ በመስኩ ፡ መካከል ፡ ተቀምጠን ፡ ሳለን ፡ ጠባቂያቸው ፡ መጥቶ ፡ ጥሩምባ ፡ ቢነፋላቸው ፡ ፫፻ ፡ የሚሆኑ ፡ አጋዘኖች ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ ተሰብስበው ፡ መጡ ። እኛም ፡ ቂጣውን ፡ ከሴቶቹ ፡ ላይ ፡ እየተቀበልን ፡ አበላናቸው ። ቂጣውን ፡ ለመብላት ፡ በጣም ፡ ይሽቀዳደማሉ ። ስለዚህ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ እንዳይዋጉ ፡ እያሉ ፡ ቀንዳቸውን ፡ ባመት ፡ ባመቱ ፡ ይቆርጡላቸዋል ። የተቆረጠውንም ፡ ቀንድ ፡ በያይነቱ ፡ ትንንሽ ፡ ዕቃ ፡ እያደረጉ ፡ እየሠሩ ፡ ወደ ፡ ናራ ፡ የሚመጣ ፡ ሰው ፡ ለመታሰቢያ ፡ እያለ ይገዛዋል ። ገንዘቡም ፡ ለምግባቸው ፡ መግዣ ፡ ይሆናል ።



The Main Gate and Stone Lanterns, Kasuga-Jinsha, Nara.

በናራ ፡ ከተማ ፡ የሽንቶ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ።



በኦሳካ ፡ ከተማ ፡ አንድ ፡ ትልቅ ፡ ማህበር ፡ ለብላቴን ፡ ጌታ ፡
ኅሩይ ፡ የቀድሞ ፡ ዘመን ፡ የጃፓን ፡ ጐራዴ ፡ ሲሸልሙ ።



በኦሳካ ፡ ከተማ ፡ አሳሂ ፡ በሚባለው ፡ የጋዜጣና ፡ የመጻሕፍት ፡ ማተሚያ ፡ ቤት ፡ የሻይ ፡ ግብዣ ።

እነዚህንም ፡ ካየን ፡ በኋላ ፡ የሽንቶን ፡ ሽራይን ፡ ለማየት ፡ ወደ ፡ ተራራው ፡ ጥግ ፡ ወጣን ። በመንገዱም ፡ ቀኝና ፡ ግራ ፡ ሁለት ፡ ሺ ፡ የ ሚሆን ፡ መብራት ፡ የሚበራበት ፡ ከድንጋይ ፡ እየተቀረጸ ፡ እንደ ፡ ሀው ልት ፡ የቆመ ፡ አየን ። ወደ ፡ ሽራይኑም ፡ በደረስን፡ ጊዜ ፡ ሊቀ ፡ ካህ ናቱ ፡ ደናግሉን ፡ ሴቶች ፡ አቅርቦ ፡ ማኅሌት ፡ ቅድሳት ፡ አዘፈነልን ። ያዘፋፈናቸውን ፡ ነገር ፡ በ፵፩ ፡ ገጽ ፡ ተመልከት ።

በሽራይኑም ፡ መቅደስ፡ዙሪያ፡እንደ፡ፋኖስ፡የተሰቀለ ፡ አንድ፡ሺ ፡ ከነ ሐስ፡የተሠራ ፡ ማብሪያ ፡ አየን።በድምሩ፡ማብሪያው ፡ ፫ሺ ፡ መሆኑ ፡ ነው።

ይኸውም ፡ ባመት ፡ ባመት ፡ በሽራይን ፡ በዓል ፡ ቀን ፡ ከማታ ፡ ፫ ምሮ ፡ እስቲነጋ ፡ ድረስ ፡ ሲበራ ፡ ያድራል ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

ከዚያም ፡ ወጥተን ፡ ዲቡትሹ ፡ የሚባለውን ፡ የቡዳሃን ፡ መቅደስ ፡ ለማየት ፡ ሔድን ። ይህንም ፡ መቅደስ ፡ የሠራው ፡ በ፯፻፵፯ ፡ ዓ ፡ ም ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የነበረው ፡ ሾሙ ፡ የሚባለው ፡ ነው ።

ይህንም ፡ የቡድሃን ፡ መቅደስ ፡ የሠራበት ፡ ምክንያቱ ፡ በ፯፻፴፭ ፡ ዓ ፡ ም ፡ የፈንጣጣ፡ በሽታ ፡ ከኮሪያ ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ ገብቶ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ፈጅቶ ፡ ነበርና ፡ ይህ ፡ የፈንጣጣ ፡ በሽታ ፡ እንዲበርድ ፡ ተስሎ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ነው ፡ ይባላል ። መቅደሱም ፡ ተሠርቶ ፡ ሲያልቅ ፡ በውስጡ ፡ የ ሚቆመውን ፡ የቡድሃን ፡ ምስል ፡ ለማሠራት ፡ እርሱ ፡ ራሱ ፡ ንጉሡ ፡ ለ የመኳንንቱና፡ ለየባለጠጎቹ ፡ ገጸ ፡ በረከት ፡ ስጡኝ ፡ እያለ ፡ ይናገር ፡ ነበር ። ገንዘቡም ፡ የሚበቃ ፡ ሆኖ ፡ በተሰበሰበ ፡ ጊዜ ፡ የምስሉ ፡ መቆሚያ ፡ ሥራ ፡ እንዲጀመር ፡ አዘዘ ።

መሠረቱም ፡ በተጣለበት ፡ ቀን ፡ እርሱ ፡ ራሱ ፡ ንጉሡ ፡ በልብሱ ፡ እጅጌ ፡ ጭቃ ፡ እየተሸከመ ፡ ያመጣ ፡ ነበርና ፡ ወይዛዝሩም ፡ መኳንን ቱም ፡ እንደርሱ ፡ በልብሳቸው ፡ እጅጌ ፡ ጭቃ ፡ እየተሸከሙ ፡ ለሠራ ተኞች ፡ ያቀርቡ ፡ ነበር ፡ ይባላል ። ባገራችን ፡ በኢትዮጵያም ፡ ነገሥ ታቱ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በሚያሠሩበት ፡ ጊዜ ፡ ራሳቸው ፡ ወደ ፡ ድን ጋይ ፡ ማጋዣው ፡ ስፍራ ፡ እየሔዱ ፡ ደንጊያ ፡ በመሐርማቸው ፡ ላ ይ ፡ እያደረጉ ፡ በትከሻቸው ፡ እየተሸከሙ ፡ ለሠራተኞች ፡ ያቀርባሉ ።

ይልቁን ፡ የእንጦጦ ፡ ራጉኤል ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በተሠራ ፡ ጊዜ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ዳግማዊ ፡ ምኒልክ ፡ ድንጋይ ፡ እየጠ ረቡ ፡ ለገንቢዎች ፡ ያቀርቡ ፡ ነበር ፡ ተብሎ ፡ በታሪክ ፡ ተጽፎ ፡ አግኝ ተናልና ፡ የነገሥታቱ ፡ አሳብ ፡ መጋጠሙ ፡ ያስደንቃል ።

ይህም ፡ የቡድሃ ፡ ምስል ፡ የቆመው ፡ ከመዳብ ፡ በተሠራ ፡ በት ልቅ ፡ መደብ ፡ (መንበር)ላይ ፡ ነው ። መደቡ ፡ ከተጀመረበት ፡ እስከ ፡ ቡድሃ ፡ ራስ ፡ ርዝመቱ ፡ ፲፯ ፡ ሜትር ፡ ነው ። ምስሉ ፡ ምንም ፡ ምን ፡ ለዛ ፡ የሌለው ፡ ደረቅና ፡ ጥቁር ፡ ነው ።

የሚደነቀውና ፡ የሚመሰገነው ፡ በትልቅነቱ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የመልኩ ፡ ቅርጽ ፡ ግን ፡ በጃፓን ፡ ካሉት ፡ ከሌሎቹ ፡ የቡድሃ ፡ ምስ ሎች ፡ እጅግ ፡ የባሰ ፡ ፉንጋ ፡ ነው ፡ ይባላል ።

መደቡና ፡ (መንበሩ)ምስሉ ፡ የፈጀው ፡ መዳብ ፡ ፩ ፡ ሚሊዮን ፡ ኪሎ ፡ ነው ።

ይኸውም ፡ ለማስማሚያና ፡ ለማገናኛ ፡ ለመወልወያ ፡ ከተደባለቀው ፡ ከነሐሱና ፡ ከብሩ ፡ ከወርቁ ፡ ከባዜቃው ፡ በቀር ፡ ነው ። ደግሞ ፡ በራሱ ፡ ዙሪያ ፡ ወርቁ ፡ እንደ ፡ እግረ ፡ ፀሐይ ፡ እየተሠራ ፡ ክበቡ ፡ ፲፩ሜትር፡ ሆኖ ፡ ይታያል ። በቀኝና ፡ በግራውም ፡ ከእርሱም ፡ ምስል ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ አነስ ፡ ያሉ ፡ ሁለት ፡ ትልልቅ ፡ ምስሎች ፡ ቆመው ፡ ይታያሉ ። እነዚህ ፡ ምንድናቸው ፡ ብለን ፡ ብንጠይቅ ፡ የቡድሃ ፡ አገልጋዮቹና ፡ ጠባ ቂዎቹ ፡ ናቸው ፡ አሉን ። በኛ ፡ በክርስቲያን ፡ ልማድ ፡ ዑቃቢ ፡ መ ልአክ ፡ እንደሚባለው ፡ ነው ።

---

## ምዕራፍ ፡ ፳፤

## ከናራ ፡ ወደ ፡ አሳካ ።

በኅዳር ፡ ፲፬ ፡ ቀን ፡ ከቀኑ፡በ፰ ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ከናራ ፡ ተነሥተን ፡ በ፱ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ አሳካ ፡ ደረስን ። የአሳካ ፡ አውራጃ ፡ አገረ ፡ ገዥና ፡ ከንቲ ባው ፡ ወደ ፡ ባቡር ፡ መቋሚያ ፡ ድረስ ፡ መጥተው ፡ ተቀበሉን ። ከዚያም፡ አሳካ ፡ ሆቴል ፡ ወደሚባለው ፡ ስንሔድ ፡ እግረ ፡ መንገዳችንን ፡ አሻሒ ፡ የሚባለው ፡ የትልቁ ፡ ጋዜጣ ፡ ቤት ፡ ዲሬክተር ፡ ጋዜጣው ፡ የሚታተም በትን ፡ ቤት ፡ እንድናይ ፡ አስቀድሞ ፡ ለምኖ ፡ ነበርና ፡ ወደዚያ ፡ ገባን ። በቀን ፡ በቀን ፡ አንድ ፡ አንድ ፡ ሚሊዮን ፡ ጋዜጣ ፡ እየታተመ ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ ላሉትና ፡ በውጭም ፡ አገር ፡ ላሉት ፡ ጃፓኖች ፡ ይላክላቸዋል ። የ ጋዜጣውንም ፡ ቃል ፡ ከራሳቸው ፡ የሚያወጡና ፡ ከየጋዜጣውም ፡ ከየመ ጽሐፉም ፡ እየቀዱ ፡ የሚጽፉ ፡ መቶ ፡ ደራሲዎች ፡ አሉ ፡ ብሎ ፡ ነገረን ። ጋዜጣውም ፡ ሲታተም ፡ እንደ ፡ ዘመኑ ፡ ብልሃትና ፡ እውቀት ፡ በኤሌክት

ሪክ ፡ ኃይል ፡ ስለሆነ ፡ መኪናው ፡ እያተመና ፡ እያንዳንዱ ፡ እየቆረጠ ፡ ያወጣዋል ።

ከዚህም ፡ ወጥተን ፡ ለእውራን ፡ መማሪያ ፡ ፊደሉን ፡ በጥቅጥቅ ፡ የሚጽፍ ፡ መኪና ፡ ለማየት ፡ ሔድን ። በየክፍሉም ፡ እያዞሩ ፡ ሲያሳዩን ፡ አንድ ፡ ዓይነ ፡ ስውር ፡ በዚያው ፡ አግኝተን ፡ በመዳሰስ ፡ ለማንበብ ፡ ያስቸግራል ፡ ወይ ፡ ብለን ፡ ብንጠይቀው ፡ ቀላል ፡ ነገር ፡ ነው ፡ ምንም ፡ አያስቸግረንም ፡ ብሎ ፡ መለሰልን ።

የማተሚያ ፡ ቤቱንም ፡ ዲሬክተር ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ ምን ፡ ያህል ፡ እውሮች ፡ ይገኛሉ ፡ ብለን ፡ ብንጠይቀው ፡ በሙሉ ፡ ጃፓን ፡ ከምሥራቅ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡ ፳ሺ ፡ እውሮች ፡ ይገኛሉ ፡ ብሎ ፡ ነገረን ።

ከዚያም ፡ ወጥተን ፡ አሳካ ፡ ሆቴል ፡ ወደሚባለው ፡ ገባን ። በማግሥቱ ፡ አሳካ ፡ ካስል ፡ የሚባለውን ፡ ለማየት ፡ ሔድን ። የቀድሞው ፡ ካስል ፡ በምድር ፡ መናወጥ ስለ ፡ ተበላሸ ፡ ያሁኑ ፡ ንጉሥ ፡ አባት ፡ ግርማዊ ፡ ቴይሾ ፡ ሲነግሡ ፡ የአሳካ ፡ ከተማ ፡ ሕዝብ ፡ ለዘውዱ ፡ በዓል ፡ መታሰቢያ ፡ ይሁንልን ፡ ብለው ፡ ገንዘብ ፡ አዋጥተው ፡ ከቀድሞ ፡ ይልቅ ፡ ደህና ፡ አድርገው ፡ አሳደሱት ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

በአሳካም ፡ የልብስ ፤ የብርጭቆ ፤ የመዳብ ፤ የቆርቆሮ ፤ የመድፍ ፤ የመትረየስ ፤ የታንክ ፤ የወሀ ፡ በምባና ፡ ሞተር ፤ የትንኝና ፡ የሌሎችንም ፡ ትንንሽ ፡ ነፍሳቶች ፡ የሚገድል ፡ መድኃኒት ፡ ፋብሪካ ፡ ቤቶች ፡ እያዞሩ ፡ አሳዩን ።

ደግሞ ፡ አገረ ፡ ገዥውና ፡ ከንቲባው ፡ የሻምብር ፡ አፍ ፡ ከሚርስ ፡ ፕሬዚዳንት ፡ ባንድነት ፡ ሆነው ፡ ምሳ ፡ ጋብዘውን ፡ ነበርና ፡ በምሳ ፡ ላይ የአሳካ ፡ አውራጃ ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ ተነሥቶ ፡ የኢትዮጵያና ፡ የጃፓን ፡ ሕዝብ ፡ የሚቃረቡበትን ፡ ንግድ ፡ የሚሰፋበትን ፡ ቃል ፡ በዲስኩር ፡ ስለተናገረ ፡ ሁሉም ፡ ደስ ፡ አላቸው ።

እኔም ፡ በበኩሌ ፡ የጃፓንና ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ መቃረብና ፡ ንግዳቸው ፡ መስፋቱ ፡ የግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥታችን ፡ ፈቃድ ፡ መሆኑን ፡ በዲስኩር ፡ እየገለጽሁ ፡ ከስረዳሁዋቸው ፡ በኋላ ፡ በታላቅ ፡ ደስታ ፡ ስንነጋገር ፡ ቆይተን ፡ ወደ ፡ ሆቴላችን ፡ ተመለስን ።

በኅዳር ፤ ፲፰ ፡ ቀን ፡ ከጧቱ ፡ በ፫ ፡ ሰዓት ፡ ከአሳካ ፡ ተነሥተን ፡ እስከ ፡ ኮቤ ፡ ከተማ ፡ በአውቶሞቢል ፡ ተጉዘን ፡ ከኮቤ ፡ በ፬ ፡ ሰዓት ፡ በባቡር ፡ ተሳፍረን ፡ ሚያጅማ ፡ ወደ ፡ ሚባለው ፡ ደሴት ፡ ሔደን ። ወደ ፡ ደሴቱ ፡

ባሕር ፡ ጠረፍ ፡ ለመድረስ ፡ ገና ፡ ሁለት ፡ ጣቢያ ፡ ሲቀረን ፡ ያገረ ፡ ገዢው ፡ መላክተኞች ፡ መጥተው ፡ ተቀበሉን ። በጠረፉም ፡ ስንደርስ ፡ ከባቡር ፡ እየወረድን፡በጢስ ፡ ጀልባ ፡ ገብተን፡ ወደ ፡ ደሴቱ፡ተሻገርን።

በደሴቱም ፡ ዳር ፡ አገረ ፡ ገዢው ፡ መኳንንቶቹን፡ ሁሉ ፤ ሰብስቦ፡ ይጠብቀን ፡ ነበርና ፡ ከሁሉም፡ ጋራ፡ ከስተዋወቀን፡ በኋላ ፡ ሚያጅማ፡ ወደ ፡ ሚባለው ፡ ሆቴል ፡ ወስዶ ፡ አሳረፈን ።

ከማታውም ፡ በ፪ ፡ ሰዓት ፡ ለራት ፡ ተጋብዘን ፡ ነበርና ፡ ከረፍንበት ፡ ሆቴል ፡ ወደ ፡ ጃፓኖች ፡ ሬስቶራ ፡ ሔድን ። ለራትም ፡ የተጠሩት ፡ መኳንንቶች ፡ ከእኛ ፡ በቀር ፡ ፲፫ ፡ ነበሩ ።

ይህም ፡ የጃፓኖች ፡ ሬስቶራ ፡ ሥራው ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ ካየናቸው ፡ ከሌሎቹ ፡ ሬስቶራዎች ፡ በጣም ፡ የተሻለ ፡ ነው ።

አዳራሹ ፡ ሰፊና ፡ ሞላላ ፡ ሆኖ ፡ በጫፉ ፡ የትያትር ፡ መጨዋቻና ፡ መዝፈኛ ፡ ቦታ ፡ አለውና ፡ እኛ ፡ ራታችንን ፡ ስንበላ ፡ ትያትር ፡ ተጫዋቾቹና ፡ ዘፋኞቹ፡ጨዋታቸውን ፡ እያሳዩ ፡ እንግዶቹን ፡ ደስ ፡ ያሰኙ፡ነበር ።

በራትም ፡ ላይ ፡ አገረ ፡ ገዥው ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ያለውን ፡ ዲስኩር ፡ ተናገረ ።

ክቡር ፡ ሆይ ። እርስዎና ፡ ከእርስዎ፡ ጋራ ፡ ያሉት ፡ ትልልቅ ፡ ሰዎች ፡ ዛሬ ፡ ይህን ፡ ሚያጅማ ፡ የሚባለውን ፡ ትንሽ፡ ደሴት ፡ በመጎብኘታችሁ ፡ ደስታዬ ፡ ትልቅ ፡ ነው ።

በኢትዮጵያና፡ በጃፓን ፡ መካከል ፡ የተደረገው ፡ ውል ፡ ለሁለቱም ፡ ወገን ፡ ሕዝቦች ፡ እጅግ ፡ ትልቅ ፡ የሆነ ፡ ታሪክ ፡ መሆኑ ፡ የተገለጠ ፡ ነው ። የኢትዮጵያና ፡ የጃፓን ፡ ሕዝብ ፡ ልማዳቸውና ፡ ኑሮዋቸው ፡ ይመሳሰላል ፡ ሲሉ ፡ እየሰማሁ ፡ አደንቃለሁ ።

ይልቁንም ፡ ሁለቱ ፡ ሕዝቦች ፡ በጣም ፡ ለመቃረብ ፡ ማሰባቸውን፡ ስለ ፡ ሰማሁ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ አለኝ ። ስለዚህ ፡ ዛሬ ፡ ክቡርነትዎ ፡ይህን ፡ ደሴት ፡ መጎብኘቱ ፡ ለእኛ ፡ ክብራችን ፡ ነው ። ደግሞ ፡ በ፰፻፺፯ ዓ ፡ ም ፡ የሸራይን ፡ መቅደስ ፡ መጀመሪያ ፡ የተሠራው ፡ በዚህ ፡ በሚያጅማ ፡ ደሴት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በጃፓን፡ አገር ፡ ሁሉ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ ነው ።

ስለዚህ ፡ በያመቱ ፡ ይህን ፡ አገር ፡ ለማየት ፡ የሚመጡ ፡ የውጭ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡ ሺህ ፡ ናቸው ። ከዚህም ፡ በቀር ፡ በሥራና ፡ በሌላ ፡ ነገር ፡ ለደከሙ ፡ ሰዎች ፡ እረፍትና ፡ ጤና፡ የሚሰጥ ፡ ሥፍራ ፡ በመሆኑ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ይመጣሉ ። ደግሞ ፡ የእኛ ፡ የጃፓኖች ፡ ምግ



በኦሳካ ፡ ከተማ ፡ ባለው ፡ በሻምብር ፡ ኦፍ ፡ ኮሜርስ ፡ የምሳ ፡ ግብዣ ።




በሚያጂማ ፡ ባሕር ፡ ዳር ፡ የሽንቶ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ።

ባችንና ፡ አቀማመጣችን ፡ ምንም ፡ ልዩ ፡ ቢሆን ፡ ዛሬ ፡ በዚህ ፡ በራት ፡ ግብዣችን ፡ ደስ ፡ እንዲልዎ ፡ አልጠራጠርም ።

አሁንም ፡ ለክቡርነትዎና ፡ ከእርስዎ ፡ ጋራ ፡ ላሉት ፡ ሰዎች ፡ መንገዳችሁ ፡ ሁሉ ፡ ያማረና ፡ ጤናማ ፡ እንዲሆን ፡ የልቤን ፡ ምኞት ፡ አቀርባለሁ ፡ ብሎ ፡ ጨረሰ ።

የዲስኩር ፡ ምላሽ ።

ክቡር ፡ አገረ ፡ ገገር ፡ ሆይ ። በጃፓን ፡ አገር ፡ ከደረስንበት ፡ ጀምሮ ፡ እስካሁን ፡ ድረስ ፡ በያገሩ ፡ የተደረገልንን ፡ የክብር ፡ አቀባበል ፡ ተናግሬ ፡ ልጨርሰው ፡ አልችልም ። ይልቁንም ፡ ዛሬ ፡ በዚህ ፡ በትንሽ ፡ ደሴት ፡ ውስጥ ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ የክብር ፡ አቀባበል ፡ ይደረግልናል ፡ ብዬ ፡ አላሰብሁም ፡ ነበርና ፡ አሁን ፡ ይህን ፡ መልካም ፡ አቀባበል ፡ በማየቴ ፡ በጣም ፡ ተደነቅሁ ።

ደግሞ ፡ አሁን ፡ እንደ ፡ ተናገሩት ፡ ቃል ፡ የሁለቱ ፡ መንግሥቶች ፡ ሕዝብ ፡ በንግድ ፡ ሥራ ፡ እየተቀራረበ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ወዳጅነታቸው ፡ እየጸና ፡ መሔዱ ፡ የማይጠረጠር ፡ ነው ። በዚህም ፡ ደሴት ፡ መጀመሪያ ፡ የቆመውን ፡ ሽራይን ፡ ነገ ፡ ጧት ፡ ለማየት ፡ የልቤ ፡ ምኞት ፡ ነው ።

ክቡር ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ ሆይ ። ለእኔ ፡ ለራሴና ፡ ከእኔም ፡ ጋራ ፡ ላሉት ፡ ሰዎች ፡ ስለ ፡ አቀረቡት ፡ መልካም ፡ ምኞትዎ ፡ አመሰግንዎታለሁ ።

ለጃፓንና ፡ ለኢትዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ ልማት ፤ ለሁለቱም ፡ አገሮች ፡ ነገሥታት ፡ ጤና ፡ ጽዋዬን ፡ አነሣለሁ ፡ ብዬ ፡ ስጨርስ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ትያትሩና ፡ ዘፈኑ ፡ ተጀመረና ፡ በብዙ ፡ ደስታ ፡ ከሌሊቱ ፡ እስከ ፡ ፮ ሰዓት ፡ ቆይተን ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ተመለስን ።

በማግሥቱ ፡ ጧት ፡ በ፫ ሰዓት ፡ ለአገረ ፡ ገዥው ፡ ቢዚት ፡ ለመመለስ ፡ ሔድን ። አገረ ፡ ገዥው ፡ በትልቅ ፡ ክብር ፡ ተቀብለው ፡ ከቤተ ፡ ዘመዶቹ ፡ ጋራ ፡ አስተዋውቆ ፡ ወዲያው ፡ ባንድነት ፡ ፎቶግራፍ ፡ ተነሥተን ፡ ተሰነባብተን ፡ ወጣን ።

ከዚያም ፡ አልፈን ፡ በባሕሩ ፡ ውስጥ ፡ የተሠራውን ፡ የመጀመሪያ ፡ ሽራይን ፡ የሚባለውን ፡ ለማየት ፡ ሔድን ።

ሽራይኑ ፡ የተሠራው ፡ ከእንጨት ፡ ከመሆኑ ፡ በቀር ፡ እጅግ ፡ ያማረ ፡ ነው ። ሽራይኑም ፡ አንድ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ በባሕሩ ፡ ውስጥ ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ እያለፈ ፡ የተሠራ ፡ ነውና ፡ ካንዱ ፡ ሽራይን ፡ ወደ ፡ ሌላው ፡ ሽራይን ፡ መተላለፊያው ፡ በእንጨት ፡ ዣንቃ ፡ ላይ ፡ ነው ። የሽራይኑም ፡ ሥራ ፡

በባሕሩ ፡ ውስጥ ፡ ትልልቅ ፡ ወፍራም ፡ አምድ ፡ እየቆመ ፡ ወፍራም ፡ ወፍራም ፡ እንጨት ፡ እየተሸጋገረ ፡ በዚያ ፡ ላይ ፡ ሣንቃ ፡ እየተረበረበ ፡ ነው ።

ሊቀ ፡ ካህናቱም ፡ መምጣታችንን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ልብሰ ፡ ተክህኖ ፡ ከለበሱ ፡ ከሁለት ፡ ካህናት ፡ ጋራ ፡ እስከ ፡ ደጅ ፡ ሰላሙ ፡ ወጥቶ ፡ ተቀበለን ።

ሽራይኑንም ፡ ካየን ፡ በኋላ ፡ የቀድሞ ፡ ነገሥታትና ፡ መሳፍንት ፡ ለሽራይኑ ፡ እንደ ፡ ስለት ፡ እያደረጉ ፡ የሰጡት ፡ የጦር ፤ መሣሪያና ፡ ልብሰ ፡ መንግሥት ፡ የሚቀመጥበትን ፡ ቅዱስ ፡ ግምጃ ፡ ቤት ፡ የሚባለውን ፡ ለማየት ፡ ገባን ።

የቀድሞ ፡ ሥራ ፡ በመሆኑም ፡ ማየቱ ፡ ብቻ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ። በሽራይኑም ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ በባሕሩ ፡ ዳር ፡ ቆመን ፡ ፎቶግራፍ ፡ ከተነሣን ፡ በኋላ ፡ ቅዱሳን ፡ እንስሶች ፡ የሚባሉትን ፡ ለማዶች ፡ አጋዘኖች ፡ እያየን ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ስንመለስ ፡ የሚያጅማን ፡ በማየት ፡ ልባችን ፡ በደስታ ፡ ተመልቶ ፡ ነበር ።

ተራራው ፡ በለመለሙ ፡ ዛፎች ፡ የተሸፈነ ፡ በመሆኑ ፡ እጅግ ፡ ያምራል ። በመካከሉም ፡ ፓጎዳ ፡ የሚባለው ፡ የሸንቶ ፡ ሽራይንና ፡ የቡዳሃ ፡ መቅደስ ፡ ምልክት ፡ የሚሆን ፡ ቤት ፡ ተሠርቶበት ፡ ይታያል ። ወደ ፡ ሆቴልም ፡ በተመለስን ፡ ጊዜ ፡ ከሚያጂማ ፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡ ዕቃ ፡ ዓይነት ፡ ስናይ ፡ ቆይተን ፡ ወደ ፡ ማታ ፡ በአሥር ፡ ሰዓት ፡ ከሚያጂማ ፡ ወደ ፡ ያዋታ ፡ ለመሔድ ፡ ተነሣን ።

ከማታውም ፡ በ፲ሰዓት ፡ በባሕር ፡ ዳር ፡ ባለው ፡ ሺሞኖሳኪ ፡ በሚባለው ፡ ከተማ ፡ ደረስንና ፡ በባቡሩ ፡ መቋሚያ ፡ አጠገብ ፡ ባለው ፡ ሆቴል ፡ አደርን ። በማግሥቱም ፡ በ፱ ፡ ሰዓት ፡ ባሕሩን ፡ በጀልባ ፡ ተሻግረን ፡ በ፬ ፡ ሰዓት ፡ ያዋታ ፡ ከተማ ፡ ደረስን ።

ያዋታ ፡ የሚባለው ፡ ከተማ ፡ ለጃፓን ፡ መንግሥትና ፡ ለሕዝቡም ፡ የሚያስፈልገው ፡ ብረት ፡ ሁሉ ፡ በያይነቱ ፡ የሚሠራበት ፡ ከሁሉ ፡ የሚበልጥ ፡ ትልቅ ፡ የብረት ፡ ፋብሪካ ፡ ስፍራ ፡ ነው ።

ለመርከብም ፤ ለአይሮፕላንም ፤ ለመድፍና ፡ ለጠመንጃም ፡ ይህንም ፡ ለመሰለው ፡ ሁሉ ፡ ብረቱ ፡ እየተሠራ ፡ የሚሔደው ፡ ከዚሁ ፡ ፋብሪካ ፡ ነው ።

እንዲያው ፡ በጠቅላላው ፡ የጃፓን ፡ ሕይወት ፡ ያለበት ፡ ስፍራ ፡ በዚህ ፡ ፋብሪካ ፡ ነው ፡ ለማለት ፡ ይቻላል ። የሠራተኞቹ ፡ ቍጥር ፡ ፵ሺ ፡ ነው ። ቀላል ፡ ቀላሉን ፡ ሥራ ፤ የሚሠሩት ፡ ሴቶች ፡ ናቸው ። ብረቱ ፡

እንደ ፡ ውሀ ፡ እየቀለጠ ፡ ሲወርድ ፡ ከተራራ ፡ ላይ ፡ የሚወርድ ፡ ፏፏቴ ውሀ ፡ ይመስላል ፡ እንጂ ፡ ብረት ፡ አይመስልም ።

ሠራተኞችም ፡ ማስፈለጉ ፡ ብረቱን ፡ ለመኪናው ፡ ለማቅረብና ፡ መኪናውን ፡ ለመዘወር ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ማናቸውንም ፡ ሥራ ፡ የሚሠራው ፡ የኤሌክትሪክ ፡ ኃይል ፡ ነው ።

ከ፪ ሰዓት ፡ እስከ ፡ ፮ ሰዓት ፤ ደግሞ ፡ ከ፰ ሰዓት ፡ እስከ ፡ ፲ ሰዓት ፤ ፋብሪካውን ፡ እየዞርን ፡ ስናይ፡ቆይተን ፡ በ፲ሰዓት ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ጉዞ ፡ ስንጀምር ፡ በያዋታ ፡ ከተማውም ፡ ዳር ፡ የሠራተኞች ፡ ክለብ ፡ የሚባለውን ፡ ለማየት ፡ ገባን ። የሠራተኞች ፡ ክለብ ፡ ማለት ፡ ሠራተኞች ፡ እየተሰበሰቡ ፡ የሥራቸውን ፡ ነገር ፡ የሚማከሩበትና ፡ በበዓል ፡ ቀን ፡ ዕረፍትና ፡ ጫዋታ ፡ የሚያደርጉበት ፡ ነው ።

በቤቱም ፡ ግንባር ፡ ባለው ፡ ሜዳ ፡ ፉት ፡ ቦልና ፡ (ኳስ )ሌላም ፡ አይነት ፡ ጨዋታ ፡ ይጫወቱበታል ። የሰው ፡ ባሕርዩ ፡ ደካማ ፡ ነውና፡በሳምንትም ፡ ቢሆን ፡ በ፩ ፡ ቀንም ፡ ቢሆን ፡ ትንሽ ፡ ዕረፍትና ፡ ሰውነቱን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ነገር ፡ ካላገኘ ፡ ጤናማ ፡ አይሆንም ፡ ይባላል ። ስለዚህ ፡ ምንም ፡ ድሀ ፡ ቢሆን ፡ በሳምንት ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ዕረፍትና ፡ ደስታ ፡ ማድረግ ፡ ያስፈልገዋል ።

ከማታውም ፡ ብ፩ ፡ ሰዓት ፡ ቤቱ ፡ በደረስን ፡ ጊዜ ፡ ያውራጃው ፡ ገዥና ፡ ከ ቲባው ፤ የዘበኞችም ፡ አለቃ ፤ ወደ ፡ ባቡር ፡ መቋሚያ ፡ መጥተው ፡ ተቀበሉን ። ከዚያም ፡ ካሜኖያ ፡ ወደ ፡ ሚባለው ፡ ሆቴል ፡ ገባን ።

በኅዳር ፡ ፳፩ ፡ ቀን ፡ በከተማው ፡ ዙሪያ ፡ ያሉትን ፡ ተራሮችና ፡ ፍል ፡ ውሀዎችን ፡ ለማየት ፡ ሔድን ፡ አገሩ ፡ ቦልካኖ ፡ ያለበት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ከተራሮቹ ፡ አንደኛው ፡ ተራራ ፡ በቦልካኖ ፡ ተወርውሮ ፡ የወጣ ፡ ነው ። እስካሁንም ፡ ባንድ ፡ ወገን ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ ይጨሳል ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

በዚሁ ፡ ተራራ ፡ ጥግ ፡ ፫፻ ፡ ስፍራ ፡ ላይ ፡ ፍል ፡ ውሀ ፡ ስለ ፡ መንጨ ፡ ከፍ ፡ ባለ ፡ ስፍራ ፡ ላይ ፡ ሆኖ ፡ ለሚመለከተው ፡ ሰው ፡ የውሀው ፡ ፍላት ፡ የመድፍ ፡ ተኩስ ፡ ጢስ ፡ ይመስላል ። ከነዚሁም ፡ የፍል ፡ ውሀ ፡ ምንጮች ፡ ዋና ፡ ዋናውን ፡ እየዞርን ፡ አየን ። የከተማውም ፡ ሕዝብ ፤ ከሌላ ፡ አገርም ፡ የሚመጡት ፡ ሰዎች ፡ ፍል ፡ ውሀውን ፡ ይጠጡታል ። በከተማውም ፡ ውስጥ ፡ በ፫ሺ ፡ ቤቶች ፡ ውስጥ ፡ በመዘውር ፡ ገብቷል ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

ደግሞ ፡ ይህ ፡ በ፫፻ ፡ ስፍራ ፡ ላይ ፡ የመነጨ ፡ ፍል ፡ ውሀ ፡ ለምን ፡ ዓይነት ፡ በሽታ ፡ የሚጠቅም ፡ መሆኑን ፤ በስንት ፡ ቀን ፡ የሚያድን ፡ መሆኑን ። ምን ፡ ዓይነት ፡ መድኃኒትና ፡ ሚኒራል ፡ ያለበት ፡ መሆኑን ፡ ለመመርመር ፡ በከተማው ፡ ዳር ፡ ዩንቤርሲቴ ፡ ተሠርቶ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ የዚህኑ ፡ ነገር ፡ እየተማሩ ፡ ይመረምራሉ ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

ይህንም ፡ ካየን ፡ በኋላ ፡ የጦር ፡ መርከብ ፡ ወታደሮች ፡ ሲታመሙ ፡ እየመጡ ፡ የሚታከሙበትን ፡ ሆስፒታል ፡ ለማየት ፡ ገባን ።

በዚህም ፡ ሆስፒታል ፡ የሚያክመው ፡ ሀኪም ፡ በ፲፱፻፳፫ ፡ ዓመ ምሕ ፡ አዝሞና ፡ አጉም ፡ የሚባሉት ፡ የጃፓን ፡ ትልልቁ ፡ የጦር ፡ መርከቦች ፡ ወደ ፡ ጅቡቲ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ የመርከቡ ፡ ኮማንዳ ፡ ዋይስ ፡ አሚራል ፡ ሲኮንጂ ፡ የሚባለው ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ አንድ ፡ ዋና ፡ መላክተኛ ፡ ልከው ፡ የጦር ፡ መርከቡን ፡ እንዲያሳዩለት ፡ ለምኖ ፡ ክቡር ፡ ደጃዝማች ፡ ደስታ ፡ ዳምጠው ፡ ይህንኑ ፡ የጃፓንን ፡ የጦር ፡ መርከብ ፡ ለማየት ፡ ታዘው ፡ ወደ ፡ ጅቡቲ ፡ በወረዱ ፡ ጊዜ ፡ አሁን ፡ በዚህ ፡ ሆስፒታል ፡ ዋና ፡ ሆኖ ፡ የሚያክመው ፡ ሰርጂየን ፡ ካፒቴን ፡ ካትሱ ፡ ለጦር ፡ መርከቦች ፡ ዋና ፡ ሀኪም ፡ ሆኖ ፡ የመጣው ፡ ነበርና ፡ ከኢትዮጵያ ፡ የመጣን ፡ መሆናችንን ፡ ባወቀ ፡ ጊዜ ፡ በታላቅ ፡ ደስታ ፡ ተቀበለን ። ሆስፒታሉንም ፡ እያዞረ ፡ ካሳየን ፡ በኋላ ፡ ባንድነት ፡ ፎቶግራፍ ፡ ተነሥተን ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ተመለስን ።

በዚሁም ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ማታ ፡ በ፱ ፡ ሰዓት ፡ የከተማው ፡ ትንንሾች ፡ ልጆች ፡ ተማሪዎች ፡ ተያትሮ ፡ ይጫወታሉና ፡ ፈቃዳችሁ ፡ ቢሆን ፡ መጥታችሁ ፡ እንድታዩ ፡ ብሎ ፡ ከንቲባው ፡ ስለ ፡ ነገረን ፡ ወደዚያው ፡ ለመሔድ ፡ ስንዘጋጅ ፡ ቆየን ።

ትያትሮውም ፡ የሚታየው ፡ ሲቲ ፡ ሀል ፡ በሚባለው ፡ ቤት ፡ ነው ። ሲቲ ፡ ሀል ፡ ማለት ፡ የመላው ፡ የከተማው ፡ ሕዝብ ፡ መሰብሰቢያ ፡ ቤት ፡ ማለት ፡ ነው ። የከተማውን ፡ ሕዝብ ፡ የሚያገናኝ ፡ ጉዳይ ፡ ሲገኝ ፡ ወይም ፡ የከተማው ፡ ሕዝብ ፡ ጨዋታ ፡ ለማየት ፤ ወይም ፡ ስብከት ፡ ለማስማት ፡ ይህንም ፡ ለመሰለው ፡ ለመልካም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ መሰብሰቢያቸው ፡ በዚሁ ፡ ቤት ፡ ነው ።

ይህንም ፡ የመሰለው ፤ ቤት ፡ የሚሠራው ፡ በከንቲባው ፡ ትጋትና ፡ ትእዛዝ ፡ በከተማው ፡ ሕዝብ ፡ ገንዘብ ፡ ነው ።



በቤፑ ፡ ከተማ ፡ ዳር ፡ የተሠራውን ፡ የጦር ፡ መርከብ ፡ ወታደሮች ፡ ሆስፒታል ፡ አይተን ፡ ስንወጣ ።

እነዚህም ፡ ትያትሮ ፡ የሚያሳዩ ፡ ልጆች ፡ የከተማው ፡ ሕዝብ ፡ ልጆች ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ ትያትሮው ፡ በዚሁ ፡ ቤት ፡ ተደርጎ ፡ ነበር ። የከተማውም ፡ ሕዝብ ፡ ወንዱም ፡ ሴቱም ፡ ቤቱ ፡ እስቲሞላ ፡ ድረስ ፡ ተሰብስቦ ፡ ነበር ።

የከተማውም ፡ ከንቲባ ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ መጥቶ ፡ ሰዓቱ ፡ ደርሷልና እንሒድ ፡ ብሎ ፡ ወሰደን ።

በላይኛውም ፡ ደርብ ፡ በተዘጋጀው ፡ መቀመጫ ፡ ወጥተን ፡ በተቀመጥን ፡ ጊዜ ፡ አሥር ፡ ልጆች ፡ የሚያማምር ፡ የጨዋታ ፡ ልብስ ፡ ለብሰው ፡ ቀረቡ ።

ከነዚሁም ፡ አንደኛው ፡ ዙሪያውን ፡ በወርቅ ፡ መርገፍ ፡ ያጌጠ ፡ በጫፉም ፡ ሰንደቅ ፡ ያለበት ፡ የኢትዮጵያን ፡ ባንዲራ ፡ ይዞ ፡ ነበረ ።

በጃፓንም ፡ ቋንቋ ፡ ጥቂት ፡ ቃል ፡ ከተናገረ ፡ በኋላ ፡ ባንዲራውን ፡ በእጁ ፡ እንደያዘ ፡ ወደ ፡ ሕዝቡ ፡ ቀርቦ ፡ ጋደም ፡ አድርጎ ፡ አሳያቸው ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ በታችም ፡ በላይም ፡ ያለው ፡ ሕዝብ ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ ተነሥቶ ፡ ቆሞ ፡ አጨበጨበ ።

ባንዴራውንም ፡ እንደ ፡ አትሮኖስ ፡ ሶስት ፡ እግር ፡ ባለው ፡ ብረት ፡ መካከል ፡ አግብቶ ፡ በሕዝቡ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ አቁሞት ፡ ሔደ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሀያ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ አሥሩ ፡ የኢትዮጵያን ፡ ባንዴራ ፡ ይዘው ፤ ደግሞ ፡ አሥሩ ፡ የጃፓንን ፡ ባንዴራ ፡ ይዘው ፡ ከቀኝና ፡ ከግራ ፡ ብቅ ፡ እያሉ ፡ መጥተው ፡ በቃላቸው ፡ እየዘፈኑ ፡ በእግራቸው ፡ እያሸበሸቡ ፡ እጅግ ፡ የሚያምር ፡ ጨዋታ ፡ ተጫውተው ፡ ተመለሱ ።

ቀጥለው ፡ ፭ ፡ ሲቶች ፡ ልጆች ፡ ከቀኝ ፤ ደግሞ ፡ አምስት ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ከግራ ፡ ወጥተው ፡ በቃላቸው ፡ እየዘፈኑ ፡ በእግራቸው ፡ እያሸበሸቡ ፡ ሲጫወቱ ፡ የኢትዮጵያን ፡ ባንዲራ ፡ በኢሌክትሪክ ፡ መብራት ፡ አድርገው ፡ ቀዩ ፡ መብራት ፡ በጉልበታቸው ፡ ብጫው ፡ በወገባቸው ፡ አረንጓዴው ፡ በፊታቸው ፡ ላይ ፡ ሲያበራ ፡ እጅግ ፡ ያምር ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ የተደረገውን ፡ ይህን፡የኢትዮጵያን ፡ ደስታና፡ ክብር ፡ ብዙ ፡ ኢትዮጵያውያን ፡ ሳይኖሩ ፡ እኛ ፡ ብቻ ፡ አይተን ፡ በመቅረቱ ፡ ልባችን ፡ በጣም ፡ ያዝን ፡ ነበር ።

ምሳሌ፡ንጉሥ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ በእልፍኙ፡ውስጥ፡ብቻውን፡ምሳውን፡ከሚበላ ፡ ባዳራሽ ፡ ውስጥ ፡ ከመሳፍንቱና ፡ ከመኳንንቱ ፡ ከሻለቃውና ፡ ከወታ

ደሩ ፡ ጋራ ፡ ቢበላ ፡ ደስ ፡ እዲለው ፡ እርግጥ ፡ ነው ። እኛም ፡ ይህን ፡ የመ ሰለውን ፡ ደስታ ፡ እኛ ፡ ብቻችንን ፡ ከማየት ፡ ከብዙ ፡ ኢትዮጵያውያን ፡ ጋራ ፡ አይተን ፡ በነበረ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ ይለን ፡ ነበር ።

ይልቁንም ፡ የትያትሩ ፡ ጨዋታ ፡ በጣም ፡ ያማረውና ፡ ያስደነቀው ፡ የሚጫወቱት ፡ ወንዶቹም ፡ ሴቶቹም ፤ ልጆች ፡ እድሚያቸው ፡ ከ፯ዓመት ፡ እስከ ፡ ፲ዓመት ፡ የሚሆን ፡ ትንንሾች ፡ በመሆናቸው ፡ ነው ።

እኔም ፡ በዚያው ፡ ከፍ ፡ ባለው ፤ ስፍራ ፡ ቆሜ ፡ የኢትዮጵያን ፡ ባንዲራ ፡ በመካከላችሁ ፡ አቁማችሁ ፡ ስለ ፡ አደረጋችሁልን ፡ አቀባበል ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ ብሎናል ። እናንተም ፡ በትምሕርት ፡ አድጋችሁ ፡ አገራችሁን ፡ ለመ ርዳት ፡ ያብቃችሁ ፡ ብዬ ፡ ተማሪዎቹን ፡ ልጆች ፡ መርቄ ፤ የከተማውን ፡ ሕዝብና ፡ ከንቲባውን ፡ አመስግኜ ፡ ስለ ፡ ተናገርሁ ፡ ሁሉም ፡ በደስታ ፡ አጨበጨቡ ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ተመለስን ።

የቤፑ ፡ ሆቴል ፡ ባለቤት ፡ በእድሜ ፡ የሸመገለ ፡ ነው ። እርሱም ፡ ከ ዚህ ፡ ቀድሞ ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ ያልደረስን ፡ አዲሶች ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መላክተኞች ፡ በሆቴሉ ፡ በመግባታችን ፡ ደስታው ፡ ከልክ ፡ ያለ ፈ ፡ ሆኖ ፡ ነበርና ፡ ጧትና ፡ ማታ ፡ ወደ ፡ እልፍኛችን ፡ እየመጣ ፡ የስፍራ ውን ፡ መመቸት ፡ የምግቡን ፡ መስማማት ፡ ይጠይቀን ፡ ነበር ።

ሁለት ፡ ቀንም ፡ ካደርን ፡ በኋላ ፡ በማግሥቱ ፡ ወደ ፡ ኦሳካ ፡ ለመመለ ስ ፡ ማሰባችንን ፡ ባስታወቅነው ፡ ጊዜ ፡ ከከተማው ፡ ነዋሪዎች ፡ ዋና ፡ ዋና ቹን ፡ ሰዎች ፡ ከነወይዛዝሮቻቸው ፡ ጠርቶ ፡ ትልቅ ፡ የደስታ ፡ በዓል ፡ አድ ርጎልን ፡ አመሸ ።

በሆቴሉ ፡ አደራሽ ፡ ያለው ፡ የኤሌክትሪኩ ፡ ማብሪያ ፡ በኢትዮጵያ ፡ ባንዴሪያ ፡ በሶስት ፡ ቀለሞች ፡ በርቶ ፡ እጅግ ፡ አምሮ ፡ ይታይ ፡ ነበር ።

የተጠሩትም ፡ እንግዶች ፡ ሁሉ ፡ በሙሉ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ ባለ ፡ ሆቴ ሉ ፡ በመካከላቸው ፡ ቆሞ ፡ አዲሶቹን ፡ የኢትዮጵያን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መላክተኞች ፡ በሆቴሉ ፡ በመቀበሉ ፡ ደስታውን ፡ እየገለጠ ፡ ተናግሮ ፡ ሲጨርስ ፡ ከወይዛዝሩ ፡ መካከል ፡ እየተነሡ ፡ እኩሉ ፡ ክራር ፡ እየመቱ ፤ እኩሉም ፡ ትንንሽ ፡ የኢትዮጵያን ፡ ባንዲራ ፡ በየእጃቸው ፡ እየያዙ ፡ የቀድሞውን ፡ ዘመን ፡ የጃፓንን ፡ ዘፈን ፡ እየዘፈኑ ፡ እስከ ፡ አምስት ፡ ሰዓት ፡ በታላቅ ፡ ደስታ ፡ አመሹ ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በመካከላቸው ፡ ቆሜ ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፡ የደስታ ፡ በዓል ፡ በማድረጉ ፡ ባለሆቴሉንና ፡ እየተጠሩ ፡ የመጡትን ፡ እንግዶች ፡




በኦሳካ ፡ ከተማ ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ ቆንስል ፡ የሆነው ፡ የሙሴ ፡ አዙሚ ፡ ራት ፡ ግብዣ ።

አመስግኜ ፡ ስጨርስ ፡ ዳር ፡ እስከ ፡ ዳር ፡ ተጨበጨበና ፡ እየተሰናበቱን ፡ በየቤታቸው ፡ ሔዱ ።

በማግሥቱም ፡ በኅዳር ፡ ፳፫ ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ማታ ፡ በ፱ ሰዓት ፡ ከቤቱ ፡ ተነሥተን ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ገብተን ፡ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ ስንጓዝ ፡ አድረን ፡ ጧት ፡ በ፲፪ ሰዓት ፡ ኮቤ ፡ ከባሕሩ ፡ ወደብ ፡ ደረስን ።

በዚያም ፡ የኮቤ ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ የላከው ፡ ተቀባይ፡ አውቶሞቢል፡ ይዞ ፡ ይጠብቀን ፡ ነበርና ፡ በአውቶሞቢል ፡ ሆነን ፡ በሁለት ፡ ሰዓት ፡ አሳካ ፡ ደርሰን ፡ በአሳካ ፡ ሆቴል ፡ ገባን ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

አሳካ ፡ በገባን ፡ በማግሥቱ ፡ የኮቤ ፡ ሻምብር ፡ አፍ ፡ ኮሜርስ ፡ የንግዱን ፡ ዕቃ ፡ በያይነቱ ፡ እንድናይና ፡ ወዲያውም ፡ ሻይ ፡ እንድንጋበዝ ፡ ለምኖን ፡ ነበርና ፡ በ፯ ሰዓት ፡ ከአሳካ ፡ ተነሥተን ፡ ወደ ፡ ኮቤ ፡ ተመለስን ። ኮቤም ፡ ስንደርስ ፡ እግረ ፡ መንገዳችንን ፡ የላስቲኩን ፡ ፋብሪካ ፡ ለማየት ፡ ገባን ።

ላስቲክ ፡ ማለት ፡ ከአንድ ፡ ዛፍ ፡ የሚወጣ ፡ ደም ፡ (ሙጫ)ነው ። የላስቲክ ፡ ዛፍ ፡ እንደ ፡ ከሊፕቱስ ፡ ዛፍ ፡ በተራ ፡ እየሆነ ፡ ይተከላል ። ከሶስትና ፡ ካራት ፡ ዓመት ፡ በኋላ ፡ ዛፉ ፡ ማደጉ ፡ ታይቶ ፡ ስለት ፡ ባለው ፡ በጠንካራ ፡ ብረት ፡ ቅርፊቱን ፡ እየበጡ ፡ ይተዉታል ። ከማግሥቱም ፡ ጀምሮ ፡ እንደ ፡ ሙጫ ፡ እየሆነ ፡ በየጥቂቱ ፡ ሲወጣ ፡ ይሰኑብትና ፡ ብዙ ፡ ሙጫ ፡ መውጣቱ ፡ ከታዬ ፡ በኋላ ፡ በስለታም ፡ ብረት ፡ እየቀረፉ ፡ ያነሡታል ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በሚዛን ፡ እየተመዘነና ፡ በመጠቅለያ ፡ እየተጠቀለለ ፡ በያገሩ ፡ እየተላከ ፡ ይሸጥና ፡ ለየሥራው ፡ ወደ ፡ ፋብሪካ ፡ ይሔዳል ።

ላስቲክን ፡ ለብዙ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ሥራ ፡ ያገቡታል ። ለአውቶሞቢል ፡ መንኰራኵር ። ለውሀ ፡ ቧምቧ ። ለዝናም ፡ ልብስ ። ለእግር ፡ ጫማ ። ለእጅ ፡ ሹራብ ። ለመታጠቂያ ። ለውሀ ፡ ኮዳ ፡ (እርኮት)ለሌላም ፡ ይህን ፡ ለመሳሰለ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ሥራ ፡ ያገቡታል ።

የላስቲኩንም ፡ ፋብሪካ ፡ ካየን ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሻምብር ፡ አፍ ፡ ኮሚርስ ፡ ሔድን ።

በሻምብር ፡ አፍ ፡ ኮሜርስ ፡ የተሰበሰቡት ፡ ትልልቅ ፡ ሰዎች ፡ ቁጥራቸው ፡ መቶ ፡ ሰማኒያ ፡ ይሆናል ። እነዚሁም ፡ በኮቤ ፡ ከተማ ፡ ከሚኖሩት ፡ ከትልልቅ ፡ ነጋዴዎች ፡ ወገን ። ካገረ ፡ ገዥዎች ፡ ወገን ። ከጉም

ሩክ ፡ ሹሞች ፡ ወገን ። ከማዘጋጃ ፡ ቤት ፡ ሹሞች ፡ ወገን ። ከውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስቴር ፡ ሹሞች ፡ ወገን ። ከአስተማሪዎች ፡ ወገን ። ከመሐንድሶች ፡ ወገን ፡ ነበሩ።ለሻዩም፡ግብዣ፡የተሰናዳው፡አሬት ፡ አውራጃ ፡ ገበታ፡ነበር ።

በደረስንም ፡ ጊዜ ፡ ዳር ፡ እስከ ፡ ዳር ፡ ተጨበጨበና ፡ በኮቤ ፡ አገረ ፡ ገዥና ፡ በኮቤ ፡ ከንቲባ ፡ መካከል ፡ በተዘረጋው ፡ ወንበር ፡ ተቀመጥሁ ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የሻምብር ፡ አፍ ፡ ኮሜርስ ፡ ፕሬዚዳን ፡ (አለቃ) ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ያለውን ፡ ዲስኩር ፡ ተናገረ ።

የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ልዩ ፡ አምባሳደር ፡(መላክተኛ ፡)
ክቡር ፡ ብላቴን ፡ ጌታ ፡ ሆይ ።

በኮቤ ፡ ሻምብር ፡ አፍ ፡ ኮሜርስና ፡ በባለ ፡ ፋብሪካዎች ፡ ስም ፡ ሆኜ፡ ጥቂቶች ፡ ቃሎች ፡ በፊትዎ ፡ መናገርና ፡ አዲሱ ፡ ወዳጃችን ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ ከቀድሞ ፡ ጀምሮ ፡ ገናና ፡ መንግሥት ፡ መሆኑን ፡ ማወቅ ፡ ለ እኔ ፡ ትልቅ ፡ ክብር ፡ ነው ።

ይልቁንም ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ ከስመ ፡ ጥሩዋ ፡ ከንግሥተ፡ ሳባ፡ ጀምሮ፡ እስካሁን ፡ ድረስ ፡ ሶስት ፡ ሺ ፡ ዓመት ፡ ያህል ፡ ትውልዱ ፡ ሳያቋርጥ ፡ ተያይዞ ፡ በመጣ ፡ ንጉሥ ፡ የሚገዛ ፡ መሆኑ ፡ እጅግ ፡ የሚያ ኮራ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ ጥንታዊነት ፡ እንደ ፡ ጃፓን ፡ መንግሥትና፡ ሕዝብ፡ መሆኑ ፡ የማይጠረጠር ፡ ነው ።

ክቡር ፡ ሆይ ። አሁን ፡ የጃፓንን፡አገር፡ መጎብኘትዎ፡ በሁለቱ ፡ መንግ ሥቶች ፡ መካከል ፡ የወዳጅነት፡መሠረት ፡ የሚመሠርት ፡ መሆኑ ፡ በጣ ም ፡ ይሰማናል ። በዚህም ፡ በዛሬው ፡ መንገድዎ ፡ የንግዳችንን ፡ ስፋት ፡ የፋብሪካችንን ፡ ብዛት ፡ ማየትዎ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝዎና ፡ የሚያስደንቅዎ፡ እንዲሆን ፡ እናምናለን ።

እስካሁን ፡ ድረስ ፡ በንግድ ፡ ሥራ ፡ ሳንገናኝ ፡ እንኖር ፡ ነበር ፤ ወደ ፡ ፊት ፡ ግን ፡ ንግዳችን ፡ እየሰፋ ፡ ሕዝባችን ፡ እየተቃረበ ፡ እንዲሔድ፡ እርግጥ ፡ ነው ።

ይህም ፡ የኮቤ ፡ ከተማ ፡ ከአውሮጳና ፡ ከእስያ ፡ ከአፍሪቃም ፡ ለሚ ገባውና ፡ ለሚወጣው ፡ ንግድ ፡ ዋና ፡ በር ፡ መሆኑ ፡ የታወቀ ፡ ነው ። ክቡርነትዎም ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ መጀመሪያ ፡ የረ ገጡት ፡ የኮቤን ፡ መሬት ፡ ነውና ፡ ዛሬ ፡ ደግሞ ፡ ሁለተኛ ፡ ተመልሰ ው ፡ መጥተው ፡ በዚሁ ፡ ከተማ ፡ መቀበላችንና ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ፋብሪካ ዎች ፡ ማሳየታችን ፡ ትልቅ ፡ ደስታ ፡ ሆነልን ።



በቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ በኢምፔርያል ፡ ሆቴል ፡ ከባልደረቦቻችን ፡ ጋራ ።

አሁንም ፡ ባንዲራዋ ፡ በኃይለኛው ፡ አንበሳ ፡ ምልክት ፡ ስለ ፡ ተጌጠውና ፡ ስለ ፡ ጂግኖች ፡ አገር ፡ ስለ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ልማት ፡ ስለ ፡ ክቡር ፡ ብላቴን ፡ ጌታ ፡ ኅሩይ ፡ ጤና ፡ ጽዋዬን ፡ አነሣለሁ ፡ ብሎ ፡ ሲጨርስ ፡ ዳር ፡ እስከ ፡ ዳር ፡ ተጨበጨበ ።

እኔም ፡ የኮቤ ፡ ሻምብር ፡ ኦፍ ፡ ኮሜርስ ፡ ፕሬዚዳን ፡ የተናገረውን ፡ ዲስኩር ፡ የሚያረጋግጥና ፡ የሚያጸና ፡ ቃል ፡ ከተናገርሁና ፡ ሁሉም ፡ ደስ ፡ ካላቸው ፡ በኋላ ፡ ከሻይ ፡ መጋበዣው ፡ ቤት ፡ ተነሥተን ፡ በኮቤ ፡ ከተማ ፡ በቆመው ፡ ፋብሪካ ፡ የሚሠራው ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ በያይነቱ ፡ ወደ ፡ ተደረደረበት ፡ ስፍራ ፡ በየክፍሉ ፡ እየገባን ፡ እናይ ፡ ጀመር ፤ የዕቃው ፡ ዓይነት ፡ ብዛት ፡ የሥራው ፡ ጥራት ፡ እጅግ ፡ ያስደንቃል ። ዓይነቱንም ፡ ብቻ ፡ ለማየት ፡ ሁለት ፡ ሰዓት ፡ ያህል ፡ አቆየን ።

በዚሁም ፡ ቀን ፡ ከማታው ፡ በሁለት ፡ ሰዓት ፡ ራት ፡ እንድንጋበዝ ፡ የኮቤ ፡ አገረ ፡ ገዥና ፡ ከንቲባው ፡ ባንድነት ፡ ሆነው ፡ የግብዣ ፡ ደብዳቤ ፡ ጽፈውልን ፡ ነበርና ፡ ሰዓቱ ፡ ሲደርስ ፡ ወደዚያው ፡ ሔድን ።

ግብዣውም ፡ እንደ ፡ ጃፓኖች ፡ ልማድ ፡ በፍራሽ ፡ ላይ ፡ እየተቀመጥን ፡ ነበር ። የራቱም ፡ ግብዣ ፡ እስቲጨረስ ፡ ባዳራሹ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ባለው ፡ ስፍራ ፡ ወይዛዝሩ ፡ ክራር ፡ እየመቱ ፡ ይዘፍኑ ፡ ነበር ።

ግብዣውም ፡ በሚጨረስበት ፡ ጊዜ ፡ የኮቤ ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ ሁለቱ ፡ መንግሥቶች ፡ የወዳጅነትና ፡ የንግድ ፡ ውል ፡ በመዋዋላቸው ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ንግድ ፡ እየሰፋ ፡ እንዲሔድና ፡ የሁለቱም ፡ መንግሥቶች ፡ ሕዝብ ፡ እንዲቃረቡ ፡ ምኞቱን ፡ እየገለጠ ፡ ተናገረ ።

እኔም ፡ ይህንኑ ፡ ያገረ ፡ ገዥውን ፡ ዲስኩር ፡ የሚያጸና ፡ ረጅም ፡ ዲስኩር ፡ ተናግሬ ፡ ስጨርስ ፡ ሌላ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ የደስታ ፡ ጨዋታ ፡ እያሳዩ ፡ ከሌሊቱ ፡ እስከ ፡ አምስት ፡ ሰዓት ፡ አምሽተን ፡ ወደ ፡ ኦሳካ ፡ ተመለስን ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በጃፓን ፡ ምዕራብ ፡ የምንቆይበት ፡ ቀን ፡ ስለ ፡ ተፈጸመ ፡ በኅዳር ፡ ፳፯ቀን ፡ በ፰ሰዓት ፡ ከኦሳካ ፡ ከተማ ፡ ተነሥተን ፡ ወደ ፡ ዋናው ፡ ከተማ ፡ ወደ ፡ ቶኪዮ ፡ ተመለስን ።

## አምስተኛ ፡ ትልቅ ፡ ክፍል ።

### እንደ ፡ ገና ፡ ወደ ፡ ቶኪዮ ፡ ተመልሰን ፡ በቶኪዮና ፡ በዙሪያው ፡ ባሉት ፡ አገሮች ፡ ስለ ፡ ሆነው ፡ ነገር ።

የቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ ከንቲባ ፡ ግብዣ ። የማዘጋጃ ፡ ቤት ፡ ትምሕርት ፡ ቤት ። የመቃብር ፡ ቦታ ። የውሀ ፡ ማጠራቀሚያ ። የጥርስ ፡ ማከሚያ ፡ ዩንቤርሲቴ ። የሚኒስትሮች ፡ ሹም ፡ ሽር ። ፓርላሚንት ፡ (የሕግ ፡ መወሰኛ ፡ ቤት ) ማየት ። ልዑል ፡ ችችቦን ፡ መኀብኘት ። የሚስተር ፡ ሲሚዮካ ፡ ግብዣ ። ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ማየት ። ቤተ ፡ መንግሥት ፡ የሆነበት ፡ ምክንያት ። ወደ ፡ ዮኮሃማ ፡ መሔድና ፡ የፈረንሳዊን ፡ ቆንስል ፡ መኀብኘት ። ወደ ፡ ካማኩራ ፡ መሔድና ፡ የቡዳሃን ፡ ምስል ፡ ማየት ። የኢትዮጵያን ፡ መንግሥትና ፡ የነገሥታቷን ፡ ቀደምትነት ፤ የሕዝቡንም ፡ ክርስቲያንነት ፡ ገልጦ ፡ ማስረዳት ። የጐራዴ ፡ ሽልማት ። ኢክስሬና ፡ አፓሬቱር ፡ ማየት ። የሻይ ፡ ማኅበር ፡ ግብዣ ። የኮጁንሻ ፡ ክለብ ፡ ግብዣ ። የጃፓን ፡ ኀበዛዝት ፡ ማኅበር ። የአንበሶቻችን ፡ ጃፓን ፡ መድረስ ፡ የዩንቤርሲቴ ፡ ተማሪዎች ፡ ምስጋና ።

---

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

በኅዳር ፡ ፳፯ ቀን ፡ የቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ ከንቲባ ፡ በከተማው ፡ ስም ፡ ሆኖ ፡ ራት ፡ ጋብዘን ፡ ነበርና ፡ ከማታው ፡ በ፪ ሰዓት ፡ ወደዚያው ፡ ሔድን ።

የማዘጋጃ ፡ ቤት ፡ አማካሪዎችና ፡ በቶኪዮ ፡ የሚኖሩ ፡ የትልልቅ ፡ ንግድ ፡ ቤት ፡ እንደራሴዎች ፡ የሚሆኑ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ ክብር ፡ ተጠርተው ፡ መጥተው ፡ ነበርና ፡ እኛ ፡ በደረስን ፡ ጊዜ ፡ ከንቲባው ፡ በየተራ ፡ እያቀረበ ፡ አስተዋወቀን ።

ከራትም ፡ አስቀድሞ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ያለውን ፡ ዲስኩር ፡ ተናገረ ።

ክቡር ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ ልዩ ፡ መላክተኛ ፡ ሆይ ።

ዛሬ ፡ በራሴና ፡ በቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ ሕዝብ ፡ ስም ፡ ሆኜ ፡ ክቡርነትዎንና ፡ ከእርሰዎ ፡ ጋራ ፡ ያሉትን ፡ ኢትዮጵያውያንን ፡ መቀበሌ ፡ ለእኔ ፡ ትልቅ ፡ ክብር ፡ ነው ።

የቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ ከዛሬ ፡ ፲ዓመት ፡ አስቀድሞ ፡ በተደረገው ፡ በመሬት ፡ መንቀጥቀጥ ፡ ትልቅ ፡ አደጋ ፡ እንዳገኘትና ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ እንደ ፡



የቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ ከንቲባ ፡ ራት ፡ ግብዣ ።

ሞቱ ፤ ብዙም ፡ ቤቶች ፡ እንደ ፡ ተቃጠሉና ፡ አመድ ፡ እንደሆኑ፤ ድልድዮቿና ፡ መንገዶቿም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ፈረሱ ፡ ሳይሰሙ ፡ አልቀሩም ።

አሁን ፡ ግን ፡ በሕዝቧ ፡ ትጋትና ፡ ሥራ ፡ መውደድ ፡ ከፊተኛዋ ፡ አሥር ፡ እጅ ፡ በልጣና ፡ አምራ ፡ መሠራቷን ፡ ስነግርዎ ፡ ደስ ፡ ይለኛል።

አሁንም ፡ ዛሬ ፡ በዚህ ፡ ከተሰበሰቡት ፡ ከትልልቆቹ ፡ ሰዎች ፡ የሚበዙት ፡ ከሻምብር ፡ አፍ ፡ ኮሜርስ ፡ (ከንግድ ፡ አማካሪዎች ፡)ወገን ፡ ናቸው ። የነዚህም ፡ ሁሉ ፡ ምኞታቸው ፡ በሁለቱ ፡ መንግሥቶች ፡ መካከል ፡ ንግድ፡ እንዲሰፋና፡ የሁለቱ ፡ መንግሥቶች ፡ ሕዝቦች ፡ በጣም ፡ እንዲቃረቡ ፡ መሆኑን ፡ ለክቡርነትዎ ፡ እየገለጥሁ ፡ ስለ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ልማትና፡ስለ፡ኢትዮጵያ፡ንጉሠ፡ነገሥት፡ጤና፡ጥልቅ፡የሆነ፡ምኞቴን፡አቀርባለሁ፡፡ብለው፡ጨረሰ።

እኔም ፡ ለከንቲባው ፡ ዲስኩር ፡ ምላሽ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ያለውን ፡ ተናገርሁ ።

ክቡር ፡ የቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ ከንቲባ ፡ ሆይ ።

በራስዎና ፡ በከተማው ፡ ሕዝብ ፡ ስም ፡ ሆነው ፡ በዚች ፡ በለምለሟና፡ በትልቂቱ ፡ ከተማዎ ፡ ባደረጉልኝ ፡ የክብር ፡ አቀባበል ፡ ለደስታዬ ፡ ወሰን፡ የለውም ። ባገሬም ፡ ሳለሁ ፡ የቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ የጃፓኖች ፡ መኩሪያና ፡ ከሠለጠኑት ፡ የዓለም ፡ ከተሞች ፡ አንደኛ ፡ የእውቀት ፡ ምንጭ ፡ መሆንዋን ፡ በወሬ ፡ እየሰማሁ ፡ ሳደንቅ ፡ እኖር ፡ ነበር ። አሁን ፡ ደግሞ ፡ በመታደሌ ፡ የመሬት ፡ መንቀጥቀጥ ፡ አደጋዋ ፡ ካለፈና ፡ እንደ ፡ ገና ፡ አምራ፡ ከተሠራች ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ መጥቼ ፡ የቶኪዮን ፡ ከተማ ፡ ትልቅነት ፡ የመንገዱን ፡ ስፋትና ፡ ጥዳት ፡ የኤሌክትሪኩን ፡ ማብራት ፡ ብዛት ፡ የዘበኞቹን ፡ ትጋት ፡ ይኸንንም ፡ የመሰለውን ፡ ሁሉ ፡ ባይኔ ፡ በማየቴ፡ ደስታዬ፡ ከልክ ፡ ያለፈ ፡ ሆኗል። ከእንግዴህም ፡ ወዲህ ፡ የሁለቱም ፡ መንግሥቶች፡ ወዳጅነት ፡ እየጸና ፡ ንግዳቸው ፡ እየሰፋ ፡ እንዲሔድ ፡ ጥርጥር ፡ የለበትምና ፡ የሁለቱ ፡ መንግሥቶች ፡ ሕዝብ ፡ በአዲስ ፡ አበባና ፡ በቶኪዮ ፡ እየተዛወሩ ፡ እንዲኖሩ ፡ ተስፋ ፡ አደርጋለሁ ። ይህቺም ፡ ብርሀት ፡ የሆነችና ፡ የምታምረው ፡ ከተማ ፡ ቶኪዮ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ በጣም ፡ እንድታድግና ፡ ለወዳጃችን ፡ ለጃፓን ፡ መንግሥት ፡ የዘላለም ፡ ደስታ ፡ ሆና ፡ እንድትኖር ፡ የልቤ ፡ ምኞት ፡ መሆኑን ፡ እገልጽልዎታለሁ ።

ክቡር ፡ ከንቲባ ፡ ሆይ ። ዛሬ ፡ በተደረገልን ፡ ግብዣ ፡ ክቡርነትዎን ፡ እያመሰገንሁ ፡ ለጃፓን ፡ አገር ፡ ልማትና ፡ ለጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ጤና ፡ የልቤን ፡ ምኞት ፡ አቀርባለሁ ፡ ብዬ ፡ ጨረስሁ ።

33

ጃፓኖች ፡ ግብዣ ፡ ካደረጉ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ዲስኩር ፡ መናገራቸው ፡ አይቀርም ። ግብዣውም ፡ እንደ ፡ አውሮጳ ፡ ሥርዓት ፡ የሆነ ፡ እንደሆነ ፡ ዲስኩሩን ፡ እንደ ፡ ደምቡ ፡ በሻምፓኝ ፡ ጊዜ ፡ ይናገራሉ ። ግብዣው ፡ እንደ ፡ ጃፓን ፡ ሥርዓት ፡ የሆነ ፡ እንደሆነ ፡ ግን ፡ ዲስኩሩን ፡ የሚናገሩት ፡ በመጀመሪያ ፡ ነውና ፡ ከንቲባው ፡ ዲስኩሩን ፡ መጀመሪያ ፡ መናገሩ ፡ ስለ ዚህ ፡ ነው ።

የራቱም ፡ ግብዣ ፡ እንደ ፡ ጃፓኖች ፡ ልማድ ፡ በመልካም ፡ ፍራሽ ፡ ላይ ፡ እየተቀመጥን ፡ ነበርና ፡ በግብዣው ፡ መካከል ፡ ከራርና ፡ በገና ፡ እየመቱ ፡ ዘፈን ፡ የሚዘፍኑ ፡ ልጃገረዶች ፡ የኢትዮጵያንና ፡ የጃፓንን ፡ ትንንሽ ፡ ባንዲራ ፡ የበእጃቸው ፡ እየያዙ ፡ የቀድሞ ፡ ታሪክ ፡ ያለውን ፡ ዘፈን ፡ በመዝፈን ፡ እንግዶቹን ፡ ደስ ፡ ያሰኙ ፡ ነበር ።

በማግሥቱም ፡ በቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ የማዘጋጃ ፡ ቤት ፡ ያቆመውን ፡ የትምህርት ፡ ቤት ፡ እንድናይ ፡ ከንቲባው ፡ ስለ ፡ አስታወቀን ፡ ከጧቱ ፡ በ፬ ሰዓት ፡ የማዘጋጃ ፡ ቤት ፡ ጸሐፊ ፡ መጥቶ ፡ ትንንሽ ፡ ልጆች ፡ የሚማሩበትን ፡ ቤት ፡ በየክፍሉ ፡ እያዞረ ፡ አሳየን ። ባንዱ ፡ ክፍል ፡ ያሉ ፡ ልጆች ፡ የኢትዮጵያን ፡ ባንዲራ ፡ ከነአንበሳው ፡ እየሳሉ ፡ በግንቡና ፡ በየጠረጴዛው ፡ ላይ ፡ አኑረው ፡ አየን ።

የትምህርት ፡ ቤቱንም ፡ ካየን ፡ በኋላ ፡ የቶኪዮ ፡ ማዘጋጃ ፡ ቤት ፡ ለመቃብር ፡ ያዘጋጀውን ፡ ቦታ ፡ ለማየት ፡ ከከተማው ፡ ውጭ ፡ ፳፫ ፡ ኪሎ ፡ ሜትር ፡ ሔድን ። የመቃብሩ ፡ ቦታ ፡ ሥፋቱ ፡ ፩ ፡ ሚሊዮን ፡ ካሬ ፡ ሜትር ፡ ነው ። የተገዛውም ፡ በ፩ ፡ ሚልዮን ፡ ፺፬፻ ፡ ዬን ፡ ነው ። አንዳንድ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ቤተ ፡ ዘመዱ ፡ ብዛት ፡ ቦታውን ፡ እየገዛ ፡ በጥርብ ፡ ድንጋይ ፡ እያጠረ ፡ ይይዛል ። አንዳንዱ ፡ ግን ፡ ዘመዱ ፡ ሲሞትበት ፡ ላንድ ፡ ጊዜ ፡ ብቻ ፡ ያንጊዜውን ፡ ይገዛል ። ላንድ ፡ ሰው ፡ መቃብር ፡ እስከ ፡ ፲፫ ዬን ፡ ይከፈላል ። በብር ፡ ሒሳብ ፡ እንደ ፡ ዛሬው ፡ ምንዛሬ ፡ ፴ ብር ፡ ይሆናል ። ገንዘብ ፡ የሌላቸው ፡ ድሆች ፡ ግን ፡ የማዘጋጃ ፡ ቤት ፡ በልዩ ፡ አዘጋጅቶ ፡ ያስቀመጠው ፡ ቦታ ፡ አለና ፡ በዚያ ፡ ይቀበራሉ ፡ ብሎ ፡ ጸሐፊው ፡ ነገረን ።

ይህ ፡ የመቃብር ፡ ሥፍራ ፡ ለስንት ፡ ዓመት ፡ የሚበቃ ፡ ይመስልሃል ፡ ብዬ ፡ ብጠይቀው ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ እስካሁን ፡ እንደ ፡ ቀድሞ ፡ ዘመን ፡ ልማዳችን ፡ ሰው ፡ ሲሞት ፡ ሥጋው ፡ እየተቃጠለ ፡ የሚቀበረው ፡ አጽሙ ፡ ብቻ ፡ ስለሆነ ፡ ብዙ ፡ ሥፍራ ፡ አይፈጅምና ፡ እስከ ፡ ፪ ዓመት ፡

ሳይበቃ ፡ አይቀርም ፡ አለኝ ። የሚቹ ፡ ዘመዶች ፡ሬሳውን ፡ ለማቃጠል ፡ እንደምን ፡ ይጨክናሉ ፡ ብዬ ፡ ብጠይቀው ፡ በተለየ ፡ ለዚሁ ፡ አንድ ፡ ማኅበር ፡ (ኩምፓንያ ) አለና ፡ ሬሳውን ፡ አቃጥሎ ፡ አጽሙን ፡ ብቻ ፡ በሣጥን ፡ አግብቶ ፡ ይሰጥና ፡ ይቀበራል ፡ አለኝ ።

የሰው ፡ ሁሉ ፡ ሬሳ ፡ እንዲቃጠል ፡ ግዴታ ፡ ነወይ ፡ ብለው ፡ ያገሩ ፡ ልማድ ፡ ስለሆነ ፡ እንደዚሁ ፡ ሲደረግ ፡ ይኖራል ፡ እንጂ ፡ ግዴታ ፡ የለም ። ዛሬ ፡ ግን ፡ አንዳንድ ፡ ሰዎች ፡ እንደዚሁ ፡ ቀብሩን ፡ እያሉ ፡ እየተናዘዙ ፡ ሳይቃጠሉ ፡ መቀበር ፡ ተጀምሯል ፡ አለኝ ።

በያንዳንዱ ፡ መቃብር ፡ ላይ ፡ የተጠረበ ፡ ድንጋይ ፡ ያቆሙበታል ፡ በጥርቡም ፡ ድንጋይ ፡ አጠገብ ፡ ከድንጋይ ፡ የታነጸ ፡ ያበባ ፡ ማስቀመጫና ፡ የዕጣን ፡ ማጨሻ፡ እያኖሩ፡የሚቹ፡ዘመዶች፡አንዳንድ፡ጊዜ፡እየሔዱ፡አበባ፡ እያስቀመጡ፡ ዕጣን ፡ እያጨሱ ፡ ይመለሳሉ።ዕጣን ፡የሚሉት ፡ ባገራችን፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ የሚታጠነውን ፡ ሙጫ ፡ ብቻ ፡ አይደለም ።ነገር፡ ግን ፡ የጢሱ ፡ ሽታ ፡ ላፍንጫ ፡ የሚጣፍጠው ፡ ማናቸውም፡ነገር፡ሁሉ፡ ዕጣን ፡ ይባላልና ፡ ይኸን ፡ የመሰለውን ፡ ሁሉ ፡ በመቅደሳቸውም ፡ በመቃብርም ፡ ላይ ፡ ያጨሳሉ ።

ደግሞ ፡ በዚያው ፡ በመቃብሩ ፡ አጠገብ ፡ ስም ፡ የተጻፈበት ፡ ካርት ፡ ማኖሪያ ፡ ትንሽ ፡ ሳጥን ፡ ያስቀምጣሉና ፡ የሚቹ ፡ ወዳጆች ፡ የሆኑትና ፡ የሩቅ ፡ ዘመዶቹ ፡ መቃብሩን ፡ ለመጎብኘት ፡ ሲሔዱ፡ ካርታቸውን ፡ በዚያ ውስጥ ፡ እያገቡ ፡ ይሔዳሉ ፡ የሚቹም ፡ የቅርብ ፡ ዘመዶች ፡ አበባ ፡ ለማስቀመጥ ፡ በሔዱ ፡ ጊዜ ፡ ካርታውን ፡ እያዩ ፡ የሚቹን ፡ መቃብር ፡ ለመጎብኘት ፡ የመጣውን ፡ ወዳጃቸውን ፡ ያውቁታል ።

ጸሎትም ፡ የሚያደርጉበት ፡ ትንንሽ ፡ ክፍት ፡ መቅደስ ፡ አልፎ ፡ አልፎ ፡ ይታያል ። ክፍት ፡ መቅደስ ፡ ማለት ፡ ጣሪያና ፡ ግድግዳ ፡ የሌለው፡ በርና ፡ የድንጋይ ፡ ምልክት ፡ ብቻ ፡ ያለበት ፡ ስፋቱ ፡ ፫ ሜትር ፤ ሞላልነቱ ፡ ከ፫ ሜትር ፡ እስከ ፡ ፭ ሜትር ፡ የሚሆን ፡ ማለት ፡ ነው ።

ይህንም ፡ ካሳዩን ፡ በኋላ ፡ ለቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ የሚያስፈልግ ፡ ውሀ ፡ የተጠራቀመበትን ፡ ኩሬና ፡ ውሀውም ፡ በኤሌክትሪክ ፡ ኃይል ፡ ውስጥ ፡ ለውስጥ ፡ ወደ ፡ ከተማው ፡ የሚወረወርበትን ፡ ለማሳየት ፡ ወሰዱን ።

ማናቸውም ፡ ነገር ፡ የጥበብና ፡ የመኪና ፡ ሥራ፡ስለ፡ሆነ ፡ ያየነውን ፡ ሁሉ ፡ ለመጻፍ ፡ ያስቸግራል ። ከኩሬውም ፡ ሥፋት ፡ የተነሣ ፡ መንገደኛ፡

እንዳይቸገር ፡ ተብሎ ፡ መካከሉን ፡ በኖራ ፡ ገንብተው ፡ በአፈር ፡ ደልድለው ፡ ሰፊ ፡ የሆነ ፡ የአውቶሞቢልና ፡ የእግረኛ ፡ መንገድ ፡ ሠርተውበታል ።

በኩሬውም ፡ ዳር ፡ ባለው ፡ በውሀ ፡ መጠባበቂያው ፡ ቤት ፡ ምሳ ፡ እንድንጋበዝ ፡ ከንቲባው ፡ አዞ ፡ ነበርና ፡ በ፯ ሰዓት ፡ ምሳችንን ፡ ተጋበዝን ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በጢስ ፡ በሚሄድ ፡ ጀልባ ፡ አንደኛውን ፡ ኩሬ ፡ ተሻግረን ፡ ወደ ፡ ሁለተኛው ፡ ኩሬ ፡ አፋፍ ፡ስንደርስ ፡ አውቶ ፡ ሞቢላችን ፡ ዞሮ ፡ ይጠብቀን ፡ ነበርና ፡ በአውቶሞቢል ፡ ሆነን ፡ ሁለተኛውን ፡ ኩሬ ፡ እያየን ሶስተኛ ፡ የውሀ ፡ ኩሬ ፡ ለመሥራት ፡ የሚቆፈረውን ፡ ቦታ ፡ ለማየት ፡ ሔድን ። የዚህም ፡ ስፍራ ፡ ስፋቱ ፡ ከፊተኛው ፡ ኩሬ ፡ ይበልጣል ። ከዚህም ፡ ሥፍራ ፡ ዋጋቸውን ፡ እየተቀበሉ ፡ እንዲነሡ ፡ የታዘዙት ፡ ባላገሮች ፡ ፫፻ ይሆናሉ ። ለኩሬው ፡ ሥራና ፡ ለባላገሮቹ ፡ ከሣራ ፡ ማዘጋጃ ፡ ቤት ፡ የሚያወጣው ፡ ገንዘብ ፡ ፲፪ ሚሊዮን ፡ ዬን ፡ ታስቧል ።

አሁን ፡ መሬቱን ፡ የሚቆፍሩት ፡ ሠራተኞች ፡ ፪ሺ፫፻ ይሆናሉ ። ነገር ፡ ግን ፡ አፈሩን ፡ የሚያግዘው ፡ ባቡር ፡ መሬቱንም ፡ የሚበሳውና ፡ ድንጋዩንም ፡ የሚፈነቅለው ፡ የመኪና ፡ ኃይል ፡ ስለሆነ ፡ ብዙ ፡ ድካም ፡ የለባቸውም ። ሥራውም ፡ እስከ ፡ ፲፰ ወር ፡ እንዲጨረስ ፡ ተወስኗል ፡ ብለው ፡ ነገሩን ። ይህንም ፡ ስናይ ፡ ቆይተን ፡ በ፲ ሰዓት ፡ ወደ ፡ ቶኪዮ ፡ ተመለስን ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

በኅዳር ፡ ፴ ቀን ፡ በቶኪዮ ፡ ያለው ፡ ያንደኛው ፡ ዩኒቬርሲቴ ፡ ፕሬዚዳን ፡ (አለቃ) ዩኒቬርሲቴውን ፡ እንድናይለት ፡ በውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስቴር ፡ በኩል ፡ ለምኖ ፡ ነበርና ፡ ወደ ፡ ማታ ፡ በ፱ ሰዓት ፡ ወደ ፡ ዩኒቬርሲቴው ፡ ሔድን ። ይህም ፡ ዩኒቬርሲቴ ፡ ተማሪዎች ፡ የሰውን ፡ አካልና ፡ በሽታ ፡ የሚመረምሩበት ፡ ይልቁንም ፡ የጥርስን ፡ በሽታ ፡ እየመረመሩ ፡ በዚያው ፡ የሚያክሙበት ፡ ነው ።

የዩኒቬርሲቴውም ፡ አለቃ ፡ ወዲያው ፡ እንደ ፡ ደረስን ፡ ተማሪዎቹን ፡ ሁሉ ፡ ባንድ ፡ ክፍል ፡ ቤት ፡ ሰብስቦ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መላክተኞች ፡ ዩኒቬርሲቴውን ፡ በመጎብኘታችን ፡ ደስታውን ፡ እየገለጠ ፡ ነገራቸው ።

እኔም ፡ የጃፓን ፡ ልጆች ፡ ለትምሕርት ፡ መትጋታቸውን ፡ እያመሰገንሁ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አገርም ፡ ሳይሔዱ ፡ ባገራቸው ፡ እየተማሩ ፡ ወደ ፡ ትልቅ ፡ እውቀት ፡ መድረሳቸው ፡ መታደል ፡ መሆኑን ፡ እየገለጽሁ ፡ ከተናገርሁ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ላይኛው ፡ ደርብ ፡ አውጥቶ ፡ የጥርስ ፡ በሽታ ፡

የሚያክሙትን ፡ ተማሪዎች ፡ አሳየን ። ደግሞ ፡ በሁለተኛው ፡ ክፍል ፡ ቤት ፡ አግብቶ ፡ የጥርስ ፡ በሽታ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ መሆኑንና ፡ የሰውን ፡ አፉ ንና ፡ ጉንጩን ፡ እንደምን ፡ አድርጎ ፡ እንዲያበላሸው ፡ በሥዕል ፡ እየተ ሣለ ፡ የተቀመጠውን ፡ አሳየን ።

ቀጥሎም ፡ የሰውን ፡ ሬሳ ፡ እየቀደዱ ፡ አካላቱን ፡ በየመላያያውና ፡ በየጅማቱ ፡ በየደም ፡ ሥሩም ፡ እየመረመሩ ፡ በሽታውን ፡ የሚያውቁበት ፡ መኪና ፡ ያለበትን ፡ አሳየን ። በዚሁም ፡ ቀን ፡ ጊዜ ፡ አጋጥሞን ፡ ያንድ ፡ ሰው ፡ ሬሳ ፡ ለመቅደድ፡አስቀድሞ፡በመድኃኒት፡ውስጥ፡ዘፍዝፈውት፡አየን።

ሬሳውን ፡ ከወዴት ፡ ታገኙታላችሁ ፡ ብዬ ፡ ብጠይቃቸው ፡ አገራቸ ውን ፡ የሚወዱና ፡ እውቀት ፡ ያላቸው ፡ አንዳንድ ፡ ሰዎች ፡ ታመው ፡ በሚሞቱበት ፡ ጊዜ ፡ ሬሳችንን ፡ የዩኒቬርሲቴ ፡ ተማሪዎች ፡ እየቀደዱ ፡ ህክምና ፡ እንዲማሩበት ፡ ፈቅደናል ፡ እያሉ ፡ እየተናዘዙ ፡ ይሞታሉና ፡ ከዚያ ፡ እያመጣን ፡ ነው ። ይህን ፡ በመሰለው ፡ ኑዛዜ ፡ ባመት ፡ ባመት ፡ እስከ ፡ ፴ ፡ ሬሳ ፡ እናገኛለን ፡ ብሎ ፡ ነገረኝ ። እንደዚህም ፡ እየተናዘዙ ፡ የሚሞቱ ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ለሚነሣው ፡ ትውልድ ፡ ጥቅም ፡ ሲሉ ፡ ነውና ፡ እጅግ ፡ ሊመሰገኑ ፡ ይገባቸዋል ።

ጊዜውም ፡ ስለ፡ አጋጠመኝ ፡ በአሜሪካ፡ዩናይትድ ፡ እስቴት ፡ አንዳ ንድ ፡ ሰዎች ፡ የሚያደርጉትን ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ ከዚህ ፡ ቀጥዬ ፡ ልጽ ፈው ፡ ይገባኛል ። ሀኪሞች ፡ አንዳንድ ፡ በሽተኛ ፡ ሲመረምሩ ፡ የ ዚህ ፡ በሽተኛ ፡ ደሙ ፡ ስለ ፡ አነሰ ፡ የሌላ ፡ ሰው ፡ ደም ፡ ካልገባበት ፡ በቶሎ ፡ ይሞታል ፡ ይላሉና ፡ በሽተኛው ፡ ዘመዶች ፡ ያሉት ፡ እንደሆነ ፡ ከዘመዶቹ ፤ ዘመዶችም ፡ ባይኖሩት ፡ ገንዘብ ፡ ያለው ፡ ከሆነ ፡ የድሆች ፡ ደም ፡ እየተገዛ ፡ በበሽተኛው ፡ በደም ፡ ሥሩ ፡ እየገባለት ፡ በጎ ፡ ይሆ ናል ። ዘመድ ፡ ወይም ፡ ገንዘብ ፡ የሌለው ፡ በጭራሽ ፡ ድሀ ፡ የሆነ ፡ እንደ ሆነ ፡ ግን ፡ ደም ፡ የማይገኝለት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በቶሎ ፡ ይሞታል ።

የዚህንም ፡ ወሬ ፡ የሰሙ ፡ አንዳንድ ፤ ደጋግ ፡ ባለጠጎች ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ እንደ ፡ ምጽዋት ፡ ደማቸውን ፡ ለበሽተኞች ፡ ለመስጠት ፡ በሆ ፒታሉ ፡ አጠገብ ፡ ቤት ፡ እየተከራዩ ፡ ይኖራሉ ። ይህንም ፡ በማድረጋ ቸው ፡ እጅግ ፡ ይመሰገናሉ ፡ ብሎ ፡ አንድ ፡ የአሜሪካ ፡ ሰው ፡ ነግሮኝ ፡ ነበርና ፡ ይህን ፡ የጃፓን ፡ ሕዝብ ፡ አደራረግ ፡ ከዚያ ፡ ጋራ ፡ ባመዛዝነው ፡ ሥጋቸው ፡ የሚቀደደው ፡ ምንም ፡ ከሞቱ ፡ በኋላ ፡ ቢሆን ፡ ኑዛዜውን ፡ የሚናገሩት ፡ በሕይወተ ፡ ሥጋ ፡ ሳሉ ፡ ነውና ፡ እንደነዚያው ፡ ሊመሰገኑ ፡

ይገባቸዋል ። ከዚያም ፡ ወጥተን ፡ የጦር ፡ ሚኒሲቴሩን ፡ ጽሕፈት ፡ ቤት ፡ አይተን ፡ በዚያውም ፡ ከጦር ፡ አለቆች ፡ ጋራ ፡ ሻይ ፡ ተጋብዘንና ፡ ፎቶግራፍ ፡ ተነሥተን ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ተመለስን ።

በታኅሣሥ ፡ ፡ ፱ ቀን ፡ ግርማዊ ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የሚኒስትሮች ፡ ሹም ፡ ሽር ፡ አድርገው ፡ ነበርና ፡ በፊት ፡ የተዋወቅኋቸው ፡ ጠቅላይ ፡ ሚኒስትሩና ፡ የውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስትሩ ፡ ስለ ፡ ተሻሩ ፡ ከአዲሱ ፡ ጠቅላይ ፡ ሚኒስትር ፡ ጋራ ፡ ለመገናኘት ፡ ቀጠሮ ፡ ጠይቄ ፡ በታኅሣሥ ፡ ፲ ቀን ፡ ወደ ፡ ጠቅላይ ፡ ሚኒስቴሩ ፡ ጽሕፈት ፡ ቤት ፡ ሔድሁ ።

ከጠቅላይ ፡ ሚኒስትሩም ፡ በቀጥታ ፡ ቀጠሮ ፡ መጠየቄ ፡ ለውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስቴር ፡ የተመረጠው ፡ ፓሪስ ፡ ያለው ፡ አምባሳዶራቸው ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ እርሱ ፡ እስቲመጣ ፡ የውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስቴሩን ፡ ሥራ ፡ የሚሠራው ፡ ጠቅላይ ፡ ሚኒስትሩ ፡ ስለ ፡ መሆኑ ፡ ነው ።

ጠቅላይ ፡ ሚኒስትሩ ፡ በእድሜ ፡ በጣም ፡ የሸመገለ ፡ ነው ። እንደ ፡ ዚህም ፡ ሸምግሎ ፡ ሳለ ፡ ለዚህ ፡ ለትልቅ ፡ ሥራ ፡ የተመረጠበትን ፡ ምክንያቱን ፡ የሚያውቁ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ብቻ ፡ ናቸው ፡ ይባል ፡ ነበር ። ቢሆንም ፡ ከውጭ ፡ አገር ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ የፖለቲካ ፡ ጉዳይ ፡ ሲነጋገር ፡ የፖለቲካውን ፡ ነገር ፡ ተጠባባቂ ፡ አንድ ፡ ልጅ ፡ እግር ፡ ሰው ፡ ባጠገቡ ፡ ይቆምለታል ።

እኔም ፡ በገባሁ ፡ ጊዜ ፡ እስከ ፡ በሩ ፡ መጥቶ ፡ ተቀበለኝ ። ንግግርም ፡ በጀመርን ፡ ጊዜ ፡ ኢትዮጵያና ፡ ጃፓን ፡ በጣም ፡ እንዲቃረቡ ፡ ለማድረግ ፡ ምኞቱና ፡ ፈቃዱ ፡ መሆኑን ፡ ገለጠልኝ ። ወዲያውም ፡ ሻይ ፡ ጋብዞኝ ፡ ነበርና ፡ ከሻይ ፡ ግብዣ ፡ በኋላ ፡ ስለ ፡ ኢትዮጵያ ፡ በተናገረው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ምስጋናዬን ፡ አቅርቤና ፡ ተሰነባብቼ ፡ ወጣሁ ።

---

## የሕግ ፡ መወሰኛና ፡ የሕግ ፡ መምሪያ ፡ ቤት ፡ ስለ ፡ መጎብኘታችን ።

በታኅሣሥ ፡ ፯ ቀን ፡ በጃፓን ፡ ቋንቋ ፡ ጊካይ ፡ የሚባለውን ፡ የሕግ ፡ መወሰኛና ፡ የሕግ ፡ መምሪያ ፡ ቤት ፡ ለማየት ፡ ሔድን ። ይህም ፡ ቤት ፡ ሥራው ፡ ተጀምሮ ፡ ገና ፡ ያልተጨረሰ ፡ ነው ። እስካሁንም ፡ ጉባኤው ፡ የሚሰበሰብበትና ፡ የሚመክርበት ፡ በሌላ ፡ ቤት ፡ ነው ።

ወደ ፡ ስፍራውም ፡ በደረስን ፡ ጊዜ ፡ የዚሁ ፡ ቤት ፡ ሥራ ፡ ዋና ፡ መሐንድስና ፡ የሠራተኞቹ ፡ ሹሞች ፡ ተቀብለው ፡ ወደ ፡ ማረፊያው ፡ ቤት ፡

ወሰዱን ። በዚያም ፡ ጥቂት ፡ ከቆየን ፡ በኋላ ፡ አዲሱን ፡ የምክር ፡ ቤት ፡ ለማየት ፡ ሔድን ። ዋናው ፡ መሐንድስ ፡ ባጠገብ ፡ ባጠገባችን ፡ እየሔደ ፡ በየክፍሉ ፡ እያገባ ፡ የሥራውን ፡ አኳኋን ፡ ሁሉ ፡ ያሳየን ፡ ነበር ።

የምክር ፡ ቤቱ ፡ ከምድር ፡ ቤቱ ፡ በቀር ፡ ሁለት ፡ ደርብ ፡ ነው ።

፩ኛው ፡ ደርብ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ማረፊያና ፡ መጸፊያ ፡ ቤት ። የሕግ ፡ መወሰኛና ፡ ለዚሁም ፡ የሚያስፈልገው ፡ ሁሉ ፡ ቤት ። የሕግ ፡ መምሪያና ፡ ለዚሁም ፡ የሚያስፈልገው ፡ የቤት ፡ ክፍል ፡ ሁሉ ፡ ነው ።

እንደዚህም ፡ ስለ ፡ ተባለ ፡ በሁለቱም ፡ ምክር ፡ ቤት ፡ ለፕሬዚዳው ፡ ማረፊያና ፡ መጻፊያ ። ለምክትሉም ፡ ፕሬዚዳን ፡ ማረፊያና ፡ መጻፊያ ። ለየዋኖቹም ፡ ጸሐፊዎች ፡ ሁሉ ፡ ማረፊያና ፡ መጻፊያ ፤ ለሕግ ፡ ወሳኞችና ፡ ለሕግ ፡ መሪዎችም ፡ ማረፊያና ፡ መጻፊያ ፤ ይህንም ፡ የመሰለው ፡ ሁሉ ፡ በክፍል ፡ በክፍል ፡ ተሠርቷል ።

አሁን ፡ ለጊዜው ፡ ሥራው ፡ የተጨረሰው ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ማረፊያና ፡ የሕግ ፡ መወሰኛ ፡ ቤት ፡ ክፍል ፡ ነው ።

፪ኛው ፡ ደርብ ፤ እንደዚሁ ፡ ለሁለቱም ፡ ወገኖች ፡ ጸሐፊዎችና ፡ ለየዋናው ፡ ወረቀት ፡ ሁሉ ፡ ማኖሪያ ፡ እንዲሆን ፡ የተከፈለ ፡ ነው ።

የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ማረፊያ ፡ ቤት ፡ ጌጡ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ለማለት ፡ አይቻልም ። ግንቡ ፡ የተለበጠው ፡ ባለወርቅ ፡ አበባ ፡ ሐር ፡ አንዱ ፡ ሜትር ፡ ባንድ ፡ ሺ ፡ ብር ፡ የሚገዛ ፡ ነው ። መዝጊያውና ፡ መቃኑ ፡ የበሩም ፡ የመስኮቱም ፡ በወርቅና ፡ በዓሣ ፡ አንበሪ ፡ አጥንት ፡ ሞዛይክ ፡ እየሆነ ፡ የተሠራ ፡ ነው ።

የምክር ፡ ቤቱ ፡ በሚከፈትበትና ፡ በሚዘጋበት ፡ ጊዜ ፡ ዲስኩር ፡ ለማድረግ ፡ ሲመጡ ፡ መጀመሪያ ፡ በዚህ ፡ ቤት ፡ አርፈው ፡ በኋላ ፡ ዲስኩር ፡ ወደ ፡ ሚደረግበት ፡ ወደ ፡ ሕግ ፡ መወሰኛው ፡ ቤት ፡ ይሔዳሉ ።

ዲስኩሩንም ፡ ሲጨርሱ ፡ ተመልሰው ፡ መጥተው ፡ በዚሁ ፡ ቤት ፡ ጥቂት ፡ ካረፉ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ መንግሥታቸው ፤ ይመለሳሉ ።

ይህም ፡ አዲሱ ፡ የምክር ፡ ቤት ፡ ከተጀመረ ፡ አሥር ፡ ዓመቱ ፡ ነው ። አሁንም ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ሥራውን ፡ ለመጨረስ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ያስፈልጋል ፡ ዳሩ ፡ ግን ፡ ዋናው ፡ የሕግ ፡ መወሰኛው ፡ ስለ ፡ ተጨረሰ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ እንዲመርቁት ፡ ፈቅደዋልና ፡ በታኅሣሥ ፡ ፲፮ ፡ ቀን ፡ ይመረቃል ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

የቤቱ ፡ ሥራ ፡ የሚበዛው ፡ በዕብነ ፡ በረድ ፡ ነው ። የበሩና ፡ የየመስኮቱ ፡ ማዕዘን ፡ መመለሻው ፡ ሁሉ ፡ ዕብነ ፡ በረድ ፡ ነው ። መሬ

ቱም ፡ በዕብነ ፡ በረድ ፡ ሞዛይክ ፡ ተሌብጧል ። በየክፍሉም ፡ በግንቡ ፡ ላይ ፡ የተሰቀሉት ፤ የእጅ ፡ ሥራ ፡ ሥዕሎች ፡ የቀድሞ ፡ ጃፓንን ፡ ታሪክ ፡ የሚያመለክቱ ፡ ናቸው ።

በትልቅነትና ፡ በቤት ፡ ክፍል ፡ ብዛት ፡ በሎንዶን ፡ ያለው ፡ የእንግሊዝ ፡ አገር ፡ ፓርላሚንት ፡ ይበልጣል ።

በማማርና ፡ በጥንካሬ ፡ ግን ፡ በቶኪዮ ፡ ያለው ፡ የጃፓን ፡ ጊካይ ፡ ይበልጣል ።

---

## ከልዑል ፡ ችችቡ ፡ ለመገናኘት ፡ ፈቃድ ፡ ስለ ፡ መቀበላችን ።

ልዑል ፡ ችችቡ ፡ የግርማዊ ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ታናሽ ፡ ወንድም ፡ ናቸው ። ወደ ፡ ቶኪዮ ፡ ሔደን ፡ በአፌሴል ፡ ከግርማዊ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ጋራ ፡ በተገናኘንበት ፡ ወራት ፡ ልዑልነታቸው ፡ ወደ ፡ ባላገር ፡ ስለሔዱ ፡ በቶኪዮ ፡ አልነበሩምና ፡ ከግርማዊ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የተላከላቸውን ፡ የሥላሴ ፡ ኒሻንና ፡ ከልዑል ፡ መርድ ፡ አዝማች ፡ አስፋ ፡ ወሰን ፡ የተላከላቸውን፡ ሰገባው ፡ በወርቅ ፡ ያጌጠውን ፡ ሰይፍ ፡ እንደ ፡ ሀገራቸው ፡ ልማድ ፡ በንጉሠ ፡ ነገሥቱና ፡ በቤተ ፡ ዘመዶቻቸው ፡ ለሚሆነው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ተጠያቂው ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ የግቢ ፡ ሚኒስቴር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ኒሻኑንና ፡ ሰይፉን ፡ አስረክበልን ፡ ብለን ፡ ሰጥተነው ፡ ነበር። በኋላ ፡ ግን ፡ በታኅሣሥ ፡ ወር ፡ መጀመሪያ ፡ ወደ ፡ ቶኪዮ ፡ ስለ ፡ ተመለሱ ፡ እንደና ፡ የግቢ ፡ ሚኒስቴር ፡ የቀጠሮ ፡ ቀን ፡ ጠይቆ፡ በታኅሣሥ ፡ ፺ ፡ ቀን ፡ የቀድሞ፡ ባልደረባችንን ፡ ሙሴ ፡ ዋታናቤን ፡ ልከ ፡ ወደ ፡ ልዑል ፡ ችችቡ ፡ ቤት ፡ ሔድን ።

የልዑል ፡ ችችቡ ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ አንድ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ የሚቆጠር ፡ ትልቅ ፡ ቤት ፡ ነው ። እንደ ፡ ደረስንም ፡ አጋፋሪው ፡ እስከ ፡ በሩ ፡ ወጥቶ ፡ ተቀበለን ። አንደኛውንም፡ የቤት ፡ ክፍል ፡ ካለፍን፡ በኋላ ፡ የልዕልት ፡ ችችቡ ፡ የክብር ፡ እመቤት ፡ (ደንገጥር ፡ )ተቀበለችን ። ወደ ፡ ማረፊያው ፡ ቤት ፡ ገብተን ፡ ፫ ደቂቃ ፡ ያህል ፡ ካረፍን ፡ በኋላ ፡ አጋፋሪው ፡ መጥቶ ፡ ወደ ፡ እንግዳ ፡ መገናኛው ፡ ቤት ፡ ይዞን ፡ ገባ ።

ልዑል ፡ ችችቡና ፡ ልዕልት ፡ ችችቡም ፡ በአዳራሹ ፡ መካከል ፡ ቆመው ፡ ይጠብቁን ፡ ነበርና ፡ ለልዑልነታቸው ፡ ማዕርግ ፡ እንደሚገባ ፡ እጅ ፡ ነሥተን ፡ ተገናኘን ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ቀዳማዊ ፡ ኀይለ ፡ ሥላሴ ፡ በሸለሟቸው ፡ ኒሻንና ፡ ልዑል ፡ መርድ ፡ አዝማች ፡ አስፋ ፡ ወሰን ፡ በላኩላቸው ፡ ሰይፍ ፡ ደስታቸውን ፡ እየገለጡ ፡ ነገሩኝ ። ወዲያውም ፡ የኒሻኑን ፡ የምስክር ፡ ወረቀት ፡ አማርኛውን ፡ ከነትርጉሙ ፡ ወስጄ ፡ ሰጥቻቸው ፡ ነበርና ፡ በፊታቸው ፡ በጠረጴዛው ፡ ላይ ፡ ዘርግተው ፡ የአማርኛውን ፡ ጽሕፈት ፡ አጥብቀው ፡ ይመለከቱ ፡ ጀመር ። የፊደሉንም ፡ ቊጥር ፡ ስለ ፡ ጠየቁኝ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሰማንያ ፡ ያህል ፡ ይሆናል ፡ ብላቸው ፡ ብዙ ፡ ነው ፡ በማለት ፡ በጣም ፡ አደነቁ ። እኔም ፡ በመብዛቱ ፡ መደነቃቸውን ፡ አይቼ ፡ ልዑል ፡ ሆይ ፡ ቊጥሩ ፡ ስለ በዛ ፡ የያንዳንዱ ፡ ፊደል ፡ መልኩና ፡ ቅርጹ ፡ ይመሳሰላል ፡ እንጂ ፡ ብዙ ፡ ልዩነት ፡ የለውም ፡ ብዬ ፡ ከሀ ፡ እስከ ፡ ሆ ፡ ከመ ፡ እስከ ፡ ሞ ፡ ጽፌ ፡ አሳየኋቸው ። ስጽፈውም ፡ በስተኋላዬ ፡ ቆመው ፡ ይመለከቱ ፡ ነበር ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ሻይ ፡ ቀረበና ፡ ከተጋበዝን ፡ በኋላ ፡ ለመሔድ ፡ ስነሣ ፡ ስለ ፡ ኒሻኑ ፡ ለግርማዊ፡ንጉሠ ፡ ነገሥት ፤ ስለ ፡ ሰይፉም ፡ ለልዑል ፡ መርድ ፡ አዝማች፡ምስጋና፡እንዳቀርብላቸው፡ለመኑኝና ፡ ተሰናብቼ፡ወጣሁ።

ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

ወደ ፡ ምስተር ፡ ሲሚዮካ ፡ ቤት ፡ ስለ ፡ መሔዳችን ።

ምስተር ፡ ሲሚዮካ ፡ የሚባለው ፡ የኢትዮጵያ ፡ ወዳጅ ፡ ለራት ፡ ጋብዞን ፡ ነበርና ፡ በታኅሣሥ ፡ ስምንት ፡ ቀን ፡ ከማታው ፡ በ፩ ፡ ሰዓት ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሔድን ። ምስተር ፡ ሲሚዮካ ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ የጥብቅና ፡ ሥርዓት ፡ ከተማሩት ፡ አንዱ ፡ ዋነኛው ፡ ነው ። እርሱም ፡ በጀርመን ፡ አገር ፡ ይኖር ፡ ነበርና ፤ ስለ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ብዙ ፡ ነገር ፡ በመስማቱ ፡ ለኢትዮጵያ ፡ እርዳታ ፡ ማጋዜን ፡ በሚባለው ፡ በየሳምንቱ ፡ በሚወጣው ፡ የጋዜታ ፡ መጽሐፍ ፡ ቀድሞ ፡ የግርማዊት ፡ ንግሥት ፡ ዘውዲቱን ፤ አሁንም ፡ የግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ኀይለ ፡ ሥላሴን ፡ የግርማዊት ፡ እቴጌ ፡ መነንን ፡ የሌሎችንም ፡ የኢትዮጵያ ፡ መኳንንት ፡ ፎቶግራፍ ፡ እየጨመረ ፡ ያሳትማል ።

ከዚህም ፡ በቀር ፡ ኢትዮጵያንና ፡ ጃፓንን ፡ የሚያገናኝ ፡ ያገር ፡ ስምና ፡ ቋንቋ ፡ ከየመጽሐፉ ፡ እየፈለገ ፡ ይጽፋል ። በመጀመሪያም ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መላክተኞች ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ ከተማ ፡ ወደ ፡ ቶኪዮ ፡ መግባታችንን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ በደግነቷ ፡ ከታወቀችው ፡ ባለቤቱ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ሆቴላችን ፡ መጥቶ ፡ ተዋወቀን ።

ወዲያውም ፡ የአፈሴል ፡ ቀናችን ፡ ሲጨረስ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሔደን ፡ እራት ፡ እንድንጋበዝለት ፡ ለምኖን ፡ ነበርና ፡ አሁን ፡ የአፈሴሉ ፡ ቀን ፡ መጨረሱን ፡ ጠይቆ ፡ እንደፈተኛው ፡ ከባለቤቱ ፡ ጋራ ፡ መጥቶ ፡ ለእራት ፡ ጋበዘን ።

ከራትም ፡ በፊት ፡ ስለ ፡ መታሰቢያ ፡ እንዲሆነን ፡ ብሎ ፡ የጃፓን ፡ አገር ፡ ልብስ ፡ ለብሰን ፡ ባንድነት ፡ ፎቶግራፍ ፡ እንድንነሣ ፡ ስለ ፡ ለመነን ፡ ደስ ፡ ለማሰኘት ፡ ስንል ፡ የጃፓን ፡ አገር ፡ ልብስ ፡ ለብሰን ፡ ፎቶግራፍ ፡ ተነሣን ። ቀጥሎም ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ጠርቶ ፡ የጃፓን ፡ አገር ፡ ጅግኖች ፡ በጦርነት ፡ ጊዜ ፡ የሚያደርጉትን ፡ ዘፈንና ፡ (ሽለላ ፡ )ጐራዴ ፡ አመዛዘዝ ፡ በጐራዴውም ፡ አመታታቸውንና ፡ አገዳደላቸውን ፡ አሳየን ። አነዛዘሩና ፡ አመታቱ ፡ ጐራዴውንም ፡ ወደ ፡ ሰገባው ፡ አመላለሱ ፡ እጅግ ፡ ያስደንቃል ። ከጐራዴውም ፡ አንዱን ፡ ስለ ፡ መታሰቢያ ፡ ይሁን ፡ ብሎ ፡ ሰጠኝ ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ጃፓኖች ፡ ሥርዓት ፡ ራት ፡ ቀረበና ፡ በፍራሽ ፡ ተቀምጠን ፡ በሁለት ፡ እንጨት ፡ እያጣበቅን ፡ ራታችንን ፡ ተጋበዝን ።

ለራትም ፡ ከተጠሩት ፡ ሰዎች ፡ አንዱ ፡ የተማረና ፡ የጃፓንን ፡ ታሪክ ፡ በጣም ፡ የሚያውቅ ፡ ስለሆነ ፡ የጠየቅሁትን ፡ ጥያቄ ፡ ሁሉ ፡ እያስረዳ ፡ መለሰልኝ ።

ከደስታውም ፡ብዛት ፡ የተነሣ ፡ በእስያ ፡ የጃፓንን ፡ ትልቅነት ። በአፍሪቃም ፡ የኢትዮጵያን ፡ ትልቅነት ፡ እየተናገረ ፡ ጽዋውን ፡ ቶሎ ፡ ቶሎ ፡ ያነሣ ፡ ነበር ።

ከእራትም ፡ በኋላ ፡ የኢትዮጵያና ፡ የጃፓን ፡ ሕዝብ ፡ ጥንታውያንና ፡ ወንድማማቾች ፡ መሆናቸውን ፡ ከታሪኩ ፡ እየጠቀሰ ፡ ይናገር ፡ ጀመር ። እኔም ፡ ይህን ፡ በቃል ፡ የነገርኸንን ፡ ሁሉ ፡ በጽሕፈት ፡ አድርገህ ፡ ስጠንና ፡ እናየዋለን ፡ አልሁትና ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ኢምፔርያል ፡ ተመለስን ።

እርሱም ፡ በጃፓን ፡ ቋንቋ ፡ ከጻፈው ፡ በኋላ ፡ በእንግሊዝ ፡ ቋንቋ ፡ አስተርጕሞ ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ድረስ ፡ አመጣልንና ፡ ወደ ፡ አማርኛ ፡ ቋንቋ ፡ ተረጐምነው ። ቃሉም ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ የተጻፈው ፡ ነው ።

የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ልዩ ፡ መላክተኛ ፡
ክቡር ፡ ብላቴን ፡ ጌታ ፡ ኅሩይ ፡ ሆይ ።

ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ በደስታ ፡ የምጽፍልዎን ፡ ማመልከቻ ፡ እንደ ፡ ታላቅ ፡ ክብር ፡ አድርጌ ፡ እቆጥረዋለሁ ። ይኸውም ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሕዝ



በወዳጃችን ፡ በምስተር ፡ ሲሚዮካ ፡ ቤት ፡ የጃፓን ፡
አገር ፡ ልብስ ፡ ለብሰን ፡ ራት ፡ እንደ ፡ ተጋበዝን ።

ብና ፡ የጃፓን ፡ ሕዝብ ፡ ሁለቱም ፡ ወገኖች ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ ያላቸውን ፡ የመንግሥት ፡ ሕግጋትና ፡ ታሪክ ፤ ደግሞ ፡ ስለ ፡ ጅግንነታቸው ፡ ሊመኩ ፡ የሚገባቸው ፡ መሆናቸውን ፡ መርምሬ ፡ ማግኘቴን ፡ ለመግለጥ ፡ ነው ። በብሉይ ፡ ኪዳንም ፡ እንደ ፡ ተጻፈላቸው ፡ እነዚህ ፡ ሁለቱ ፡ ወንድማማች ፡ ሕዝቦች ፡ የመጡበትን ፡ ፍለጋ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ተመልሰን ፡ ብንመለከት ፡ የትውልዳቸው ፡ ጥንታዊነት ፡ አንድ ፡ ዓይነት ፡ መሆኑ ፡ ይታወቃል ፤ እንደዚህም ፡ ያለው ፡ ስጦታ ፡ በተለየ ፡ የሚሰጠው ፡ ከእግዚአብሔር ብቻ ፡ መሆኑን ፡ ስላመንሁ ፡ እውነተኛውን ፡ ነገር ፡ በቅን ፡ ልቡና ፡ ልነግርዎ ፡ ወደድሁ ።

በብሉይ ፡ ኪዳን ፡ በኦሪት ፡ ዘፍጥረት ፡ በ፲ኛው ፡ ምዕራፍ ፡ ስለ ፡ ሰው ፡ ትውልድ ፡ ሲጽፍ ፡ ስለ ፡ ዝምድና ፡ መቀራረብ ፡ ነገር ፡ ለመመርመር ፡ ብዙ ፡ ጥቅም ፡ ያለው ፡ ሐሳብ ፡ ይሰጣል ። በዚሁም ፡ ምዕራፍ ፡ ውስጥ ፡ ያፌት ፡ የኖኅ ፡ ሶስተኛው ፡ ልጁ ፤ ከልጆቱ ፡ መካከል ፡ ጃባን ፡ የሚባል ፡ አንድ ፡ ልጅ ፡ እንደ ፡ ነበረው ፡ ተጽፎ ፡ እናገኛለን ፤ ከጃባንም ፡ የተወለዱት ፡ ልጆች ፡ ሕዝብ ፡ ሆነው ፡ በየደሴቶቹ ፡ የተከፋፈሉ ፡ ሆኑ ። የአዲሱም ፡ ዘመን ፡ ትምሕርት ፡ ያላቸው ፡ ታሪክ ፡ ጸሐፊዎች ፡ የጃባን ፡ ትውልዶች ፡ እነዚሁ ፡ ጃፓኖች ፡ መሆናቸውን ፡ ያስታውቁናል ። በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ተጉዘው ፡ አገር ፡ የያዙት ፡ የጃባን ፡ ነገዶች ፡ የያዙትን ፡ አገር ፡ በጥንቱ ፡ ስማቸው ፡ ጠሩት ። ስለዚህ ፡ ይኸው ፡ ዛሬ ፡ በማላይ ፡ የደሴት ፡ መንጎችኛ ፡ (አርቺፔላጎ) በሩቁ ፡ በምሥራቅ ፡ ጃፓን ፡ ጃባን ፡ የሚባል ፡ ስም ፡ አለን ። ጃፓን ፡ የሚባለውን ፡ ስም ፡ ማርኮ ፡ ፖሎ ፡ መጀመሪያ ፡ አወጣለት ፡ ብለው ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ እንደሚናገሩት ፡ አይደለም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከብዙ ፡ ዘመናት ፡ በፊት ፡ ይዞ ፡ የኖረችው ፡ ስምዋ ፡ ነው ። ጃፓን ፡ የሚባለው ፡ ስም ፡ የወጣው ፡ ጃባን ፡ ከሚባለው ፡ ስም ፡ ነው ። ይህም ፡ የኒፖን ፡ የጥንት ፡ ስሙ ፡ ነው ፤ የአዲሱ ፡ ዘመን ፡ ታሪከኞችም ፡ ይህንኑ ፡ ያጸናሉ ።

(፩ኛ ፡ ማመልከቻ) የጃባን ፡ የጥንት ፡ ስሙ ፡ ጃባዲ ፡ ነው ፤ ይህም ፡ አነጋገር ፡ ያባዳይ ፡ የሚባለውን ፡ ስም ፡ ያሳስበናል ። ጃፓን ፡ የሚባለውንም ፡ በጥንቱ ፡ በቻይና ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፎ ፡ እናገኛለን ። ከሶስት ፡ ሺህ ፡ ዘመን ፡ በፊት ፡ የይሁዳ ፡ አገር ፡ ንጉሥ ፡ ሰሎሞን ፡ ከፊኒቂ ፡ (ፊንሲያ) ንጉሥ ፡ ጋራ ፡ ባንድነት ፡ እየሠራ ፡ ከቀይ ፡ ባሕር ፡ በጣም ፡ እርቆ ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ዘመቻ ፡ ሔዶ ፡ እንደነበረ ፡ ታሪክ ፡ ይነ

ግረናል ። ደግሞም ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ የነበሩት ፡ የፌንቂ ፡ ሰዎች ፡ የመ
ርከብ ፡ ሥራ ፡ ጥበብ ፡ ያውቁ ፡ እንደነበሩና ፡ በሱማትራ ፡ በኩል ፡ አ
ድርገው ፡ ወደ ፡ ቦርኒዎ ፡ እንደ ፡ ሔዱ ፡ በዚያም ፡ የንግድ ፡ ሥራ ፡
መቀራረቢያ ፡ እንደ ፡ መሠረቱ ፡ ታሪክ ፡ ያስተምረናል ። (ቦርኔዎ ፡ ሱ
ማትራንና ፡ ሲንጋፑርን ፡ አልፎ ፡ በቻይና ፡ የደቡብ ፡ ባሕር ፡ መከከል ፡
ያለ ፡ ደሴት ፡ ነው ። )

ጃባንም ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በደሴቷ ፡ ላይ ፡ ልዩ ፡ የሆነ ፡ ታላቅ ፡
ሥልጣኔ ፡ ነበራት ። ስለዚህ ፡ በሜድትራኒያን ፡ በኤርትራና ፡ (ቀይ ፡
ባሕር ፡)በምሥራቅ ፡ አሲያ ፡ መከከል ፡ ከ፫ ሺ ፡ ዘመን ፡ በፊት ፡ መርከ
ብ ፡ ይመላለስ ፡ ነበርና ፡ በብሉይ ፡ ኪዳን ፡ የተጻፈላቸው ፡ የጃባን ፡ ነገ
ዶች ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ መጥተዋል ፡ ለማለት ፡ ይቻላል ። ይህም ፡ ነገር ፡ ከዚ
ህ ፡ በፊት ፡ ብዙዎቹ ፡ ባለታሪኮች ፡ አባቶቻችን ፡ ከወደ ፡ ደቡብ ፡ ባሕ
ር ፡ ሳይመጡ ፡ አይቀሩም ፡ ብለው ፡ ያምኑ ፡ የነበሩትን ፡ ነገር ፡ ያረጋ
ግጥልናል ። በኦሪት ፡ ዘፍጥረት ፡ በ፲ኛው ፡ ምዕራፍ ፡ የጃባን ፡ ልጆች ፡
ሕዝቦች ፡ ሆነው ፡ የሚኖሩባቸው ፡ የተከፋፈሉ ፡ ደሴቶች ፡ ናቸው ፡
ብሎ ፡ ያመለከተው ፡ ቃል ፡ ለአሳባችን ፡ የበለጠ ፡ ይረዳል ።

(፪ኛ ፡ ማመልከቻ ፡)አንዳንድ ፡ ሰዎችም ፡ ያፌት ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡
ያዋታ ፡ መጥቶ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ ይናገራሉ ። ያዋታ ፡ የተባለውም ፡ ክቡር
ነትዎ ፡ ሔደው ፡ የጐበኙት ፡ በኪዩሹ ፡ ያለው ፡ የብረት ፡ ፋብሪካ ፡ ስፍራ ፡
ነው ። ደግሞም ፡ በኦሪት ፡ ዘፍጥረት ፡ በምዕራፍ ፡ ፲ ፡ ካም ፡ የሚባለው ፡
የኖኅ ፡ ሁለተኛ ፡ ልጁ ፡ ከልጆቹ ፡ መካከል ፡ ኩሽ ፡ የሚባል ፡ ልጅ ፡
እንደነበረው ፡ የዚሁም ፡ የኩሹ ፡ ትውልዶች ፡ እጅግ ፡ ብርቱ ፡ ሰዎች ፡
ሆነው ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ (ቀይ ፡ ባሕር ፡)አጠገብ ፡ ያለውን ፡ አገር ፡
ሁሉ ፡ እንደገዙ ፡ እናገኛለን ። ከሶስት ፡ ሺህ ፡ ዘመን ፡ በፊት ፡ የነበረውን ፡
የምስርን ፡ መንግሥት ፡ ግዛት ፡ በካርታ ፡ ላይ ፡ የተመለከቱት ፡ እንደሆ
ነ ፡ በላይኛው ፡ ጥቁር ፡ ዓባይ ፡ አቅራቢያ ፡ ወደ ፡ ዛሬው ፡ የኢትዮጵ
ያ ፡ አገር ፡ በሚቀርበው ፡ አገር ፡ ኩሽ ፡ ካስ ፡ ኩንሜህ ፡ የሚባሉ ፡ አ
ገሮች ፡ እንደነበሩ ፡ ያስረዳል ። ይኸውም ፡ በጣም ፡ ያልተካከለ ፡ ማስረ
ጃ ፡ የኩሽ ፡ ነገዶች ፡ በዚሁ ፡ አገር ፡ ክፍል ፡ እንደኖሩና ፡ እንደተራቡ ፡
ባጭሩ ፡ አመልክቶ ፡ በኦሪት ፡ ዘፍጥረት ፡ የተጻፈውን ፡ ቃል ፡ ለማጽ
ናት ፡ ነው ። በሎሬንስ ፡ ዩኒበርሲቲም ፡ የኩሽ ፡ ወገኖች ፡ በእብራውያ
ን ፡ ቋንቋ ፡ ኮዋሾ ፡ ወይም ፡ ኩሹ ፡ መልካቸውም ፡ ሴማውያንን ፡ ወይ

ም ፡ ያፌታውያን ፡ (የኤሮፓውያን ፡ ህንዶች ፡ )ይመስላል ፡ የሚል ፡ ታሪክ ፡ አግኝተናል ። ዛሬም ፡ ምስራውያንና ፡ ኢትዮጵያውያን ፡ እንደዚሁም ፡ የመሰሉትን ፡ ሆነዋል ። ይህም ፡ ነገር ፡ ኢትዮጵያውያን ፡ ትውልዳቸው ፡ ከኩሽ ፡ መሆኑን ፡ ያስረዳናል ። የኢትዮጵያም ፡ ሰዎች ፡ በአገራቸው ፡ ከቀሩት ፡ ከሌሎቹ ፡ ዘሮች ፡ በላይ ፡ በመሆናቸው ፡ ሊመኩ ፡ ይገባቸዋል ። ባለፈው ፡ ማመልከቻዬ ፡ እንዳስረዳሁ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሰዎች ፡ ትውልዳቸው ፡ የኖኅ ፡ ሁለተኛ ፡ ልጅ ፡ ከሚሆን ፡ ከካም ፡ ልጅ ፡ ከኩሽ ፡ ከሆነ ፡ ጃፓኖች ፡ የኖኅ ፡ የሶስተኛው ፡ ልጁ ፡ የያፌት ፡ ልጅ ፡ የጃባን ፡ ትውልዶች ፡ ከሆኑ ፡ አወጣጣቸው ፡ ከአንድ ፡ ሥር ፡ ስለሆነ ፡ ወንድማማች ፡ ናቸው ። ይኸውም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ምስጢር ፡ ነው ። ክቡርነትዎን ፡ በተቀበልሁበት ፡ ጊዜያት ፡ በአሪት ፡ ዘፍጥረት ፡ ከብዙ ፡ ሺህ ፡ ዘመናት ፡ በፊት ፡ የተጻፈውን ፡ የሁለቱን ፡ ሕዝቦች ፡ ወንድማማችነት ፡ ማግኘቴ ፡ ትልቅ ፡ ድንቅ ፡ ነው ።

እኔ ፡ ለመናገር ፡ የምፈልገው ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ብቻ ፡ አይደለም ። ነገር፡ ግን ፡ እጅግ ፡ ተገልጦ ፡ በመታየቱ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘውን ፡ ነገር ፡ የኩሽ ፡ ወገኖች ፡ (ነገዶች ፡ )ጉዞዋቸውን ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ እየቀጠሉ ፡ መጥተው ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ መግባታቸውንም ፡ እናገራለሁ ። በዛሬው ፡ ጊዜ ፡ ጃፓኖች ፡ የኩሽ ፡ ትውልዶች ፡ መሆናቸውን ፡ ብንናገር፡ምንም ፡ አያስነቅፈንም ። ስለምን ፡ የኩሽ ፡ ነገዶች ፡ በምሥራቅ፡በኩል፡ስለ ፡ መሔዳቸው ፡ ነገርና ፡ ስለ ፡ ጃፓን ፡ ነገዶች ፡ ተመርምሮ ፡ በዶክቶር፡ ኮማኖስኪ ፡ ቶጋሚ፡ አስቀድሞ ፡ በሙሉ ፡ ተጽፈዋል ። ይህንም ፡ ብዙ ፡ ጥቅም ፡ ያለበትን ፡ የመጽሐፍ ፡ ግልባጭ ፡ ለክቡርነትዎ ፡ ሰጥተዎታል ። ክቡርነትዎም ፡ ምቹ፡ ጊዜ ፡ በተገኘ ፡ ጊዜ ፡ ይህንኑ ፡ መጽሐፍ ፡ አስተርጒመው ፡ እንዲመለከቱት ፡ ተስፋ ፡ አለኝ ።

ደግሞ ፡ የኩሽ ፡ ነገዶች ፡ ወደዚህ ፡ ወደ ፡ ሀገራችን ፡ የመግባታቸውን ፡ ነገር ፡ በጥቂቱ ፡ ልገልጽልዎ ፡ እወዳለሁ ። ኩሻውያን ፡ በዱሮ ፡ ዘመን ፡ የተቀመጡበት ፡ ስፍራ ፡ ነው ፡ የተባለው ፡ በስተ ፡ ሰሜን ፡ በኩል ፡ በጃፓን ፡ ባሕር ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ያለው ፡ ኮሺ ፡ ኖ ፡ ኩኒ ፡ ወይም ፡ የኮሺ ፡ አውራጃ ፡ የሚባለው ፡ አገር ፡ በመጀመሪያ ፡ ኩሻውያን ፡ የተቀመጡበት ፡ አገር ፡ ነው ።

ይኸውም ፡ ኩሺ ፡ ኖ ፡ ኩኒ ፡ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ በሶስት ፡ ክፍል ፡ ተከፋፈለ ። የዛሬውም ፡ ሶስቱ ፡ አውራጃዎች ፡ ኤቼዝን ፤ ኤቹ ፤ ኤቺጎ ።

የተባሉት ፡ በያንዳንዳቸው ፡ ቃል ፡ አነጋገር ፡ የሚሰማው ፡ የኢትዮጵያ ፡ አነጋገር ፡ (አገባብ ፡ )ያለባቸው ፡ ይመስላል ፡ እግዚአብሔር ፡ ሕዝብን ፡ የመረጠበት ፡ ስፍራ ፡ (የቀድሞዎቹ ፡ አባቶቻችን ፡ እንደሚሉት ፡ ) በመጀመሪያ ፡ ገብተው ፡ ሠርተው ፡ በተቀመጡበት ፡ ስፍራ ፡ ኩሺ ፡ ፉሩ ፡ ታኬ ፡ ተባሉ ። ይኸውም ፡ ቃል ፡ ፈልሰው ፡ የመጡት ፡ የኩሺ ፡ ነገዶች ፡ መሆናቸውን ፡ ያመለክታል ፤ ትሱ ፡ ኩሺ ፡ የሚባለው ፡ ቃል ፡ ኩሹን ፡ ይመስላልና ፡ ኩሻውያን ፡ ጥንት ፡ በኪዩሹ ፡ ተቀምጠው ፡ በዘመን ፡ ብዛት ፡ እየተባዙ ፡ እንደ ፡ ሔዱ ፡ ያስረዳል ፡ ኩሺ ፡ ሮ ፡ ማለት ፡ በሆካይዶ ፡ ምናልባት ፡ ኩሻውያን ፡ የገቡበት ፡ መንገድ ፡ ማለት ፡ ሳይሆን ፡ አይቀርም ። እንዲሁም ፡ ባለፉት ፡ በጃፓንና ፡ በኮሪያ ፡ ታሪክ ፡ ከኩሺ ፡ የወጣ ፡ ኪሺ ፡ ወይም ፡ ኮሺ ፡ ተብለው ፡ የሚጠሩ ፡ ብዙ ፡ ቃሎች ፡ እናገኛለን ። ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ የተጻፈው ፡ ምሳሌ ፡ ዘመዶቻችን ፡ ከሚናገሩት ፡ ቃል ፡ ተለቅሞ ፡ የተጻፈ ፡ ስም ፡ ነው ።

ኩሺ ፡ ሞቶ ፡
ኩሺ ፡ ዳ ፡
ኪሺ ፡
ኪሺ ፡ ሞቶ ፡
ኪሺ ፡ ኢ ፡
ኪሺ ፡ ዳ ፡
ኩሱ ፡ ዳ ፡
ኩሱ ፡ ኖ ፡ ኪ ፡
ኩሱ ፡ ሞቶ ፡
ኮሺ ፡ ያማ ፡
ኮሺ ፡ ዳ ፡
ኮሺ ፡ ታኒ ፡

እነዚህን ፡ ስሞች ፡ የያዙ ፡ ሰዎች ፡ የኩሻውን ፡ ትውልዶች ፡ ናቸው ። ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ያለውም ፡ ተጨማሪ ፡ ማመልከቻ ፡ የጃፓኖች ፡ ስም ፡ ከኢትዮጵያ ፡ ጂዎግራፊ ፡ ከአፍሪቃ ፡ ካርታ ፡ ላይ ፡ የለቀምኳቸው ፡ ናቸው ። (እስኪል ፡ 1 15,000.000) ይህም ፡ ከጃፓኖች ፡ ቃል ፡ ጋራ ፡ ይገጥማል ።

## ኢትዮጵያ ፡

አምሀራ ፡ አም ፡ ሀራ ፡
(ልብ ፡ አድርጉ ፡) በእንግሊዝ ፡ ምስር ፡ ሱዳን ፤ በኢትዮጵያ ፡ በአምሀራ ፡ አውራጃ ፡ በስተ ፡ ሰሜን ፡ ታካ ፡ (ታዕካ)የሚባል ፡ አገር ፡ አለ። ታካ ፡ አምሀራ ፡ ይሆናል ፡ ወይም ፡ ታካ ፡ አምሀራ ፡ ይኸውም ፡ እነጋገር ፡ ታካ ፡ ማጋ ፡ ሀራን ፡ ይመስላል ። በታካ ፡ አጠገብ ፡ ያለው ፡ ካሠላ ፡ ካሺዋሀራን ፡ የመጀመሪያው ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ጅሙ ፡ ወደ ፡ ዙፋን ፡ የወጣበትን ፡ የጃፓንን ፡ የጥንት ፡ ከተማ ፡ ያሳስባል ።

አክሱም ፡

አድዋ ፡

ትግሬ ፡

ኖጋራ ፡ (ወገራ ፡)

ስሜን ፡

መቀላ ፡ (መከላ ፡)

ጎንዳ ፡ (ጐንደር) ጎንዳጕዲ ፡

ተከዚ ፡ (ፈሳሽ ፡ ወንዝ ፡)

ጣና ፡

ከረን ፡ (ኪሬን ፡)

## ጃፓን ።

(ታካ ፡) ማጋ ፡ ሀራ ፡

አክትሱ ፡ ሺማ ፡
(የጥንቱ ፡ የደሴታችን ፡ መንግሥት ፡ ስም ነው ፡)

አድሱማ ፡
(የጥንቱ ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ያለው ፡ ግዛታችን ፤ ከዛሬው ፡ ቶኪዮ ፡ ጋራ ፡ የሚቆጠር ፡)

ሺግሬ ፡
(በመከር ፡ ጊዜ ፡ ወይም ፡ በክረምት ፡ የሚነሣ ፡ ብርድ ፡ ያለበት ፡ ነፋስ ፡)

ናጋራ ፡
(የከተማ ፡ ስም ፡)

ሲሚ ፡ (ትል)

መገራ ፡ (የሰው ፡ ስም ፡

ጐንደ ፡ (የሰው ፡ ስም ፡

ተከዚ ፡
(በኪዮቶ ፡ አጠገብ ፡ ያለው ፡ ያንድ ፡ ትል ፡ ወንዝ ፡ ስም ፡

ታና ፡
(ሼልፍ ፡)የቁም ፡ ሣጥን ፡)

ኪረን ፡ (ቀጭኔ ፡)

| ኢትዮጵያ ፡ | ጃፓን ፡ |
|---|---|
| አዋሽ ፡(አዋሲ፡ ባሕር ፡ ተራራ፡) | አዋዲ ፡ የአንድ ፡ ደሴት ፡ ስም ፡ |
| አሞ ፡ (ወንዝ ፡) | አም ፡ በኪዮቶ ፡ አውራጃ ፡ ውስጥ ፡ የትልቅ ፡ ወንዝ ፡ ስም ፡ ነው ። |
| ሣቃ ፡ | ሠቃ ፡(ተራራ ፡) |
| ተርተላ ፡ (ተርተሌ ፡) | ታታላ ፡ (የሰው ፡ ስም ፡) |
| አሱብ ፡ | አሰቡ ፡ |
| አቤ ፡ | አቤ ፡ የሰው ፡ ስም ፡ |
| አህማረ ፡ | አማ ፡ የጥንት ፡ ስም ፡ (ሰማይ ፡ ማለት ፡ ) |
| ሐረር ፡ | ሐራ ፡ (ደጋ ፡ አገር ፡) |

እንዚህ ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ የተጻፉት ፡ ቃሎች ፡ ኩብሉይ ፡ ኪዳንና ፡ ከሌሎቹ ፡ መጻሕፍቶች ፡ በአጭር ፡ ጊዜ ፡ ምርመራ ፡ የተገኙ ፡ በመሆናቸው ፡ እርግጠኛ ፡ ከመሆን ፡ የራቁ ፡ ይሆናሉ ፡ ብዬ ፡ እፈራለሁ ። ነገር ፡ ግን ፡ እነዚሁ ፡ ሁለቱ ፡ ወንድማማች ፡ ሕዝቦች ፡ የመዛመዳቸው ፡ አኳኋን ፡ እንዴት ፡ እንደሆነ ፡ ለማስረዳት ፡ የፍቅር ፡ ቅናት ፡ ስላነሳሣኝ ፡ መርምሬ ፡ በጥቂቱ ፡ ለመግለጽና ፡ ይህን ፡ መንፈሳዊ ፡ ስጦታ ፡ ከሩቅ ፡ አገር ፡ ለመጡት ፡ ለተከበሩ ፡ እንግዳችን ፡ ለክቡርነትዎ ፡ ለማበርከት ፡ የተመኘሁበት ፡ ዋናው ፡ ምክንያት ፡ በአገርዎና ፡ በጃፓን ፡ መከከል ፡ ያለውን ፡ የወዳጅነት ፡ መገናኛ ፡ በጣሙን ፡ ለማበረታት ፡ መሣሪያ ፡ እንዲሆን ፡ ብዬ ፡ ነው ። አስቀድሜ ፡ እንዳመለከትሁ ፡ በአሬት ፡ ዘፍጥረት ፡ የተጻፈውን ፡ ቃል ፡ መሠረት ፡ አድርጌ ፡ ሁለቱም ፡ ወገኖች ፡ አስቀድሞም ፡ መሠረታቸው ፡ ከአንድ ፡ ግንድ ፡ መሆኑን ፡ ስለ ፡ ተረዳሁ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ ብሎኛል ።

አሁን ፡ ይህን ፡ በችኮላ ፡ የተጻፈውን ፡ የምርመራ ፡ ቃል ፡ ለክቡርነትዎ ፡ በማክበር ፡ ካቀረብሁ ፡ በኋላ ፡ የተማሩት ፡ የአገርዎ ፡ ልጆች ፡ ነገሩን ፡ አስተካክለው ፡ እየመረመሩ ፡ ሁለቱ ፡ ሕዝቦች ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ከሥር ፡ ጀምሮ ፡ ወንድማማቾች ፡ መሆናቸውን ፡ ተረድተው ፤ በሁለቱ ፡ አገሮች ፡ መከከል ፡ ያለውን ፡ የልብ ፡ ወዳጅነት ፡ እያጸኑ ፡ እንዲሔዱ ፡ ፍጹም ፡ ምኞቴ ፡ ነው ። ታኅሣሥ ፡ ፳፩ ቀን ፡ ፲፱፻፳፪ ፡ በጃፓን ፡ ዘመን ፡ ቍጥር ።

ለዘላለም ፡ ታማኝዎ ።

ቶሞዮሺ ፡ ሲሚዮካ ።




በቶኪዮ ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

### የንጉሠ ፡ ነገሥቱን ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ማየት ።

የንጉሠ ፡ ነገሥቱን ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ በአፈሴሉ ፡ ቀን ፡ ያየነው ፡ የእንግዳ ፡ ማረፊያውንና ፡ የእንግዳ ፡ መቀበያውን፤ የሙብል ፡ ቤቱንና፤ ከሙብል ፡ በኋላ ፡ የሚታረፍበትን ፡ ክፍል ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በሙሉ ፡ ለማየት ፡ ጊዜው ፡ አልነበረምና ፡ ግርማዊነታቸው ፡ ቢፈቅዱ ፡ የቤተ ፡ መንግሥቱን ፡ ክፍል ፡ ሁሉ ፡ በሙሉ ፡ እንድናይ ፡ በግቢ ፡ ሚኒስትሩ ፡ በኩል ፡ ፈቃድ ፡ ጠይቀን ፡ ነበርና ፡ ባልደረባችን ፡ ምስተር ፡ ዋታናቢ ፡ መፈቀዱን ፡ ስለ ፡ አስታወቀን ፡ በታኅሣሥ ፡ ፱ ቀን ፡ በ፫ ሰዓት ፡ መጥቶ ፡ ወደ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ወሰደን ።

በመጀመሪያም ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ የሚመጣ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ፊርማውን ፡ ወደሚፈርምበት ፡ ቤት ፡ ገብተን ፡ ወደ ፡ ግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥትና ፡ ወደ ፡ ግርማዊት ፡ እቴጌ ፡ በሚቀርበው ፡ በሁለቱ ፡ ደብተር ፡ ላይ ፡ ፊርማችንን ፡ ፈረምን ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የቤት ፡ ጠባቂዎች ፡ ሹምና ፡ ምስተር ፡ ዋታናቢ ፡ ሆነው ፡ በየክፍሉ ፡ እያገቡ ፡ ቤተ ፡ መንግሥቱን ፡ አሳዩን ። ነገር ፡ ግን ፡ የቤቱን ፡ ማማር ፤ በየግንቡና ፡ በየጣራው ፡ ያለውን ፡ ጌጥ ፡ ይህን ፡ ይመስላል ፡ ብዬ ፡ ለመጻፍና ፡ ለማስረዳት ፡ ምሳሌው ፡ ይቸግረኛልና ፡ ምሳሌውን ፡ ሳልጽፈው ፡ በመቅረቴ ፡ የዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ አንባቢዎች ፡ ሳያዝኑ ፡ አይቀሩም ።

የቤቱም ፡ ክፍል ፡ ብዙ ፡ ነው ። የእንግዳ ፡ መቀበያው ፡ ሁለት ፡ ክፍል ፡ ነው ። ፩ኛው ፡ ክፍል ፡ በጣም ፡ ሰፊ ፡ የሆነ ፡ ሁለት ፡ የወርቅ ፡ ወንበር ፡ የተዘረጋበት ፡ በታላላቅ ፡ በዓል ፡ ቀን ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ አምባሳዶሮችንና ፡ ሚኒስትሮችን ፡ ያገር ፡ መሳፍንቶችንና ፡ መኳንንቶችን ፡ የሚቀበሉበት ፡ ነው ።

፪ኛው ፡ ክፍል ፡ ጥቂት ፡ አነስ ፡ ያለ ፡ አንዳንድ ፡ ልዩ ፡ መላክተኛና ፡ ያገር ፡ መኳንንቶች ፡ የሚቀበሉበት ፡ ነው ።

የሙብል ፡ ቤቱም ፡ ሁለት ፡ ክፍል ፡ ነው ። ፩ኛው ፡ በታላላቅ ፡ በዓል ፤ ቀን ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ አምባሳዶሮችና ፡ ሚኒስትሮች ፡ ያገርም ፡ ሚኒስትሮችና ፡ ባላባቶች ፡ የሚጋብዙበት ፡ ትልቅ ፡ ሰፊ ፡ ነው ። ፪ኛው ፡ አንዳንድ ፡ ልዩ ፡ መላክተኛ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ከቤተ ፡ ዘመዶቻቸው ፡ ጋራ ፡ ሆነው ፡ የሚጋብዙበት ፡ ነው ።

ደግሞ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ልዩ ፡ አማካሪዎች ፡ የሚመክሩበት ፡ አንድ ፡ ትልቅ ፡ ክፍል ፡ ቤት ፡ አለ ። በዚህም ፡ ቤት ፡ ትልቅ ፡ ጠረጴዛ ፡ ተዘርግቶ ፡ በየወንበሩ ፡ ላይ ፡ የአማካሪዎቹ ፡ ቍጥርና ፡ ስም ፡ ተጽፎበታል ። ለንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ሁለት ፡ ሜትር ፡ ያህል ፡ ለየት ፡ ብሎ ፡ ፩ ወንበርና ፡ ፩ ጠረጴዛ ፡ ተዘርግቶበታል ።

ልዩ ፡ አማካሪዎች ፡ በሚሰበሰቡበት ፡ ጊዜ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ቤተ ፡ ዘመዶች ፡ አይለዩምና ፡ ወንበራቸው ፡ ከአማካሪዎቹ ፡ ጋራ ፡ ሆኖ ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ወንበር ፡ አቅራቢያ ፡ ነው ።

ለእቴጌይቱም ፡ እንደዚሁ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ እንግዳ ፡ መቀበያ ፤ ያገር ፡ ባላባቶችና ፡ ወይዛዝሮች ፡ መቀበያ ፡ ለየብቻው ፡ የተለየ ፡ የቤት ፡ ክፍል ፡ አላቸው ።

የንጉሠ ፡ ነገሥቱም ፡ ቤተ ፡ ዘመዶች ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ የማረፊያ ፡ ቤት ፡ ተለይቶላቸዋል ።

ይህንም ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ እየዞርን ፡ ስናይ ፡ ባንደኛው ፡ ቤት ፡ መተላለፊያ ስንደርስ ፡ ሳናስበው ፡ በድንገት ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ሁለተኛ ፡ ወንድማቸው ፡ ልዑል ፡ ታካማሱ ፡ ከባለቤታቸው ፡ ከልዕልት ፡ ታካማሱ ፡ ጋራ ፡ ሆነው ፡ የጦር ፡ አለቆች ፡ ልብስ ፡ ለብሰው ፡ ኒሻን ፡ አድርገው ፡ ከወደ ፡ ውስጥ ፡ ሲመጡ ፡ ተጋጠምንና ፡ ሰላምታ ፡ ሰጥተን ፡ ቆምን ። ልዑል ነታቸውም ፡ በማክበርና ፡ በትሕትና ፡ ቃል ፡ ሰላምታ ፡ ሰጥተውን ፡ ካለፉ ፡ በኋላ ፡ ባልደረባችንን ፡ ሙሴ ፡ ዋታናቢን ፡ ጠርተው ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ ልዩ ፡ መላክተኛ ፡ ዛሬ ፡ ወደ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ግቢ ፡ የመጡት ፡ በምን ፡ ምክንያት ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ጠየቁትና ፡ ቤተ ፡ መንግሥቱን ፡ ግቢውንም ፡ ውጭውንም ፡ ለማየት ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ መለሰላቸው ።

እኔም ፡ ዛሬ ፡ ኒሻን ፡ ማድረጋቸው ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ነው ፡ በዓል ፡ ነውን ፡ ብዬ ፡ ሙሴ ፡ ዋታናቢን ፡ ብጠይቀው ፡ የወታደር ፡ አለቅነት ፡ ያለው ፡ ማንም ፡ ቢሆን ፡ ወደ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ሲገባና ፡ ሲገናኝ ፡ ኒሻን ፡ ሳያደርግ ለመግባት ፡ አይፈቀድለትም ። ልዑል ፡ ታካማሱም ፡ አሁን ፡ ሹመታቸው ፡ በወታደር ፡ አለቅነት ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ከግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ጋራ ፡ ለመገናኘት ፡ ሲመጡ ፡ ኒሻን ፡ አደረጉ ፡ ብሎ ፡ መለሰልኝ ።

እንግዲህ ፡ በቶኪዮ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱን ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ለማየት ፡ ምክንያት ፡ ካገኘሁ ፡ የስፍራውንና ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ የሆነበትን ምክንያት ፡ ባጭሩ ፡ እጽፋለሁ ።

የቀድሞዎቹ ፡ የጃፓን ፡ ነገሥታት ፡ ከተማቸውን ፡ ካንዱ ፡ ስፍራ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ስፍራ ፡ ያዘዋውሩ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ ባንድ ፡ ከተማ ፡ ጸንተው ፡ አልኖሩም ። ቢሆንም ፡ አንዳንድ ፡ ብርቱ ፡ ምክንያት ፡ እያገኙ ፡ ነበር ።

ኪዮቶ ፡ በሚባለው ፡ ከተማ ፡ ብቻ ፡ አንድ ፡ ሺ ፡ ዓመት ፡ ያህል ፡ ቆይተውበታል ።

ቶኪዮም ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ለመሆን ፡ የተመረጠበት ፡ ምክንያቱ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈው ፡ ነው ።

የጃፓን ፡ ነገሥታት ፡ ከመጀመሪያው ፡ ንጉሥ ፡ ከጂሙ ፡ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ፹፪ተኛው ፡ ንጉሥ ፡ እስከ ፡ ጎ—ቶባ ፡ ድረስ ፡ ራሳቸውን ፡ ችለው ፡ እንደ ፡ ፈቃዳቸው ፡ ይገዙ ፡ ነበር ። ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ባላባቶቹ ፡ ጉልበት ፡ እያበጁ ፡ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡ ከንጉሡም ፡ ጋራ ፡ ይዋጉ ፡ ነበርና ፡ ሚናሞቶ ፡ ዮሪቶሞ ፡ የሚባለው ፡ ባላባት ፡ ከንጉሡ ፡ ጋራ ፡ ሆኖ ፡ ሌሎቹን ፡ ባላባቶች ፡ እየወጋ ፡ ድል ፡ ስለ ፡ አደረገ ፡ ንጉሡን ፡ ለስሙ ፡ ብቻ ፡ በዙፋን ፡ አስቀምጦ ፡ አገሩን ፡ እርሱ ፡ ይገዛ ፡ ጀመር ። ከእርሱም ፡ ቀጥሎ ፡ የእርሱ ፡ ወራሽ ፡ የሆነው ፡ እንደዚሁ ፡ እንደ ፡ ሚናሞቶ ፡ ኃይለኛ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የሁለቱም ፡ የግዛት ፡ ዘመን ፡ ፴ዓመት ፡ ሆነ ።

ቀጥሎም ፡ ፉጂዋራ ፡ ዮሪትሱኒ ፡ የሚባለው ፡ ባላባት ፡ በሚናሞቶ ፡ ትውልድ ፡ እግር ፡ ገብቶ ፡ እስከ ፡ ፰ ፡ ትውልድ ፡ ፻፲፭ ፡ ዓመት ፡ ገዝተው ፡ ካለፉ ፡ በኋላ ፡ አሽካባ ፡ ታካጂ ፡ የሚባል ፡ ሌላ ፡ ባላባት ፡ ተነሥቶ ፡ እስከ ፡ ፲፭ ፡ ትውልድ ፡ ፪፻፴፬ ፡ ዓመት ፡ ገዝተው ፡ አለፉ ።

በእርሳቸውም ፡ እግር ፡ ታዮራ ፡ ኖቡናጋ ፡ የሚባለው ፡ ባላባት ፡ ተነሥቶ ፡ እስከ ፡ ሁለት ፡ ትውልድ ፡ ፳፭ ፡ ዓመት ፡ ከገዙ ፡ በኋላ ፡ ኢዬያሹ ፡ ቶኩጋዋ ፡ የሚባል ፡ ሌላ ፡ ባላባት ፡ ተነሥቶ ፡ እስከ ፡ ፲፭ ፡ ትውልድ ፡ ፪፻፷፭ ፡ ዓመት ፡ አገሩን ፡ ገዙ ። ንጉሡን ፡ ለስም ፡ ብቻ ፡ በዙፋን ፡ እያስቀመጡ ፡ የጃፓንን ፡ አገር ፡ የገዙት ፡ ባላባቶች ፡ ቍጥራቸው ፡ ፴፱ ፤ ዘመናቸውም ፡ ፯፻፷፱ ፡ መሆኑ ፡ ነው ።

እነዚህም ፡ የመንግሥት ፡ እንደራሴዎች ፡ የሆኑት ፡ ባላባቶች ፡ ምንም ፡ ንጉሥ ፡ ባይባሉ ፡ የመንግሥቱን ፡ ሥራና ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡ በእጃቸው ፡ እያደረጉ ፤ ከተማቸውን ፡ እየለዩ ፡ ነዋሪዎች ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ ነገሥታቱ ፡ ለሕይወታቸው ፡ እንኳ ፡ የሚበቃ ፡ ገንዘብ ፡ እየተቸገሩ ፡ ይኖሩ ፡ ነበር ። ከቤተ ፡ መንግሥቱም ፡ ውጭ ፡ እንዳይወጡ ፡ እናንተ ፡ የ

አምላክ ፡ ልጆች ፡ ናችሁና ፡ በግልጥ ፡ ብዙ ፡ ሰው ፡ ሊያያችሁ ፡ አይገ ባም ፡ እያሉ ፡ ያታልሏቸው ፡ ነበር ።

ይልቁንም ፡ የአሽካጋ ፡ ትውልድ ፡ ፡ የነበሩት ፡ ባላባቶች ፡ የመንግ ሥት ፡ እንደራሴዎች ፡ በሆኑበት ፡ ዘመን ፡ በሺ፩፻ ፡ ዓመ ፡ ምሕ ፡ የነገ ሠው ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ትሱቺ ፡ ሲሞት ፡ እንደ ፡ ነገሥታት ፡ ሥርዓት ፡ በክብር ፡ ለማስቀበር ፡ ለማጥኑና ፡ ለሠረገላው ፡ ማሰናጃ ፡ ገንዘብ ፡ ታጥቶ ፡ ሬሳው ፡ ፵ቀን ፡ ሙሉ ፡ ሳይቀበር ፡ ቆየ ፡ ይባላል ።

ደግሞ ፡ ጎ—ናራ ፡ የሚባለው ፡ ንጉሥ ፡ ለእለት ፡ ምግብ ፡ እንኳ ፡ እየተቸገረ ፡ መጽሐፍ ፡ እየጻፈ ፡ ይሼጥ ፡ ነበር ፡ ይባላል ። በገራችን ፡ በ ኢትዮጵያ ፡ በዘመነ ፡ መሳፍንት ፡ ጊዜ ፡ ነገሥታቱ ፡ በጎንደር ፡ ቤተ ፡ መ ንግሥት ፡ እየተዘጋባቸው ፡ የእለት ፡ ምግብ ፡ እንኳ ፡ እየተቸገሩ ፡ ሰሌን ፡ እየሠሩ ፡ አሽከር ፡ እያወጣ ፡ ይሸጥላቸው ፡ ነበረ ፡ እንደሚባለው ፡ ነው ።

እነዚህም ፡ የአሽካጋ ፡ ወገኖች ፡ የመንግሥት ፡ እንደራሴ ፡ እየሆኑ ፡ የገዙት ፡ እስከ ፡ ፲፭ ፡ ትውልድ ፡ ነው ። ስለ ፡ ሆነም ፡ በሌላው ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ የሠራ ፡ ሰው ፡ ፍዳውን ፡ መቀበሉ ፡ አይቀርምና ፡ ከ ሰባቱ ፡ በቀር ፡ ስምንቱ ፡ ፍዳቸውን ፡ እየተቀበሉ ፡ ሞተዋል ።

ሁለቱን ፡ የገዛ ፡ አሽከሮቻቸው ፡ ገደሏቸው ። አምስቱ ፡ ከእንደራ ሴነታቸው ፡ ተሽረው ፡ በስደት ፡ ሲዞሩ ፡ ሞቱ ።

ሁለቱ ፡ በገዛ ፡ እጃቸው ፡ ራሳቸውን ፡ ገደሉ ።

(አውት ፡ ላይን ፡ ሂስቶሪ ፡ አፍ ፡ ጃፓን ፡ ፲፰፻፺፫ና ፡ ፲፱፻፲ ፡ ገጽ ፡ እይ)

ከነዚህም ፡ ሁሉ ፡ ኢዬያሹ ፡ ቶኩጋዋ ፡ የሚባለው ፡ ይበልጥ ፡ ነበር ። የበለጠበትም ፡ ምክንያቱ ፡ ከእርሱ ፡ አስቀድሞ ፡ የነበሩት ፡ የመንግሥቱ ፡ እንደራሴዎች ፡ ከሲብል ፡ ወገን ፡ ነበሩ ። ቶኩጋዋ ፡ ግን ፡ ከሚሊታሪ ፡ (ከ ጦር ፡ አለቆች ፡)ወገን ፡ ነበረና ፡ ኃይሉ ፡ ስለ ፡ በረታ ፡ የንጉሡንም ፡ የባላ ባቶችንም ፡ ሥልጣን ፡ ጠቅልሎ ፡ በእጁ ፡ በማድረጉ ፡ ነበር ።

ይህንም ፡ የሚያስረዳ ፡ ነገር ፡ በኒኮና ፡ በናጎያ ፡ በኪዋቁም ፡ እጅግ ፡ የተዋበ ፡ ቤቶችና ፡ ብርቱ ፡ ብርቱ ፡ ምሽግ ፡ ሠርቶባቸው ፡ ነበር ። ዋና ፡ መ ኖሪያውን ፡ ግን ፡ ዛሬ ፡ ቶኪዮ ፡ በተባለው ፡ በዮዶ ፡ አድርጎ ፡ ነበር ።

ቶኪዮ ፡ ከዚያ ፡ አስቀድሞ ፡ የዓሣ ፡ አጥማጆች ፡ መንደር ፡ ነበረች ። ቶኩጋዋ ፡ ከተማ ፡ ካደረጋት ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ነጋዴዎችንም ፡ ሌሎችንም ፡ ት ልልቆች ፡ ሰዎች ፡ ባላባቶችንም ፡ ወደ ፡ ቶኪዮ ፡ እየመጣችሁ ፡ ቤት ፡ ሥሩ ፡ ብሎ ፡ ስለ ፡ አዘዛቸው ፡ የቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ እየሰፋች ፡ ሔደች ።

ቶኩጋዋ ፡ ምንም ፡ ኃይሉ ፡ ቢበረታና ፡ ጃፓንን ፡ በሙሉም ፡ ቢገዛ ፡ የንገሥታቱን ፡ ክብር ፡ እየጠበቀ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ እንኳ ፡ ን ጉሥንት ፡ አስበ ፡ አያውቅም ፡ ነበር ። አስቦ ፡ በነበረ ፡ ግን ፡ ባንድ ፡ ሰዓት ፡ እጅ ፡ ለማድረግ ፡ ይችል ፡ ነበር ፡ ይባላል ።

ይልቁንም ፡ እርሱ ፡ ለጃፓን ፡ የሠራው ፡ ትልቅ ፡ ሥራ ፡ በዘመኑ ፡ የ ነበሩ ፡ ባላባቶቹ ፡ ሁሉ ፡ በየግዛታቸው ፡ ሙሉ ፡ ሥልጣንና ፡ ወታደር ፡ ነ በራቸውና ፡ ይህን ፡ ሥልጣናቸውን ፡ ለመውሰድ ፡ ሲል ፡ ባላባቶችን ፡ ሁሉ ፡ ቆጥሮ ፡ ዓመቱን ፡ አካፍሎ ፡ በየተራ ፡ ወደ ፡ ቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ እየ መጡ ፡ እንዲቀመጡ ፡ (እንዲቸክሉ ፡)አደረጋቸው ። ባላባቶቹም ፡ ሚስታ ቸውን ፡ ልጆቻቸውን ፡ በያገራቸው ፡ እየተዉ ፡ ብዙ ፡ ወታደር ፡ እየያዙ ፡ በቶኪዮ ፡ ሲቀመጡ ፡ ጊዜ ፡ ገንዘባቸውን ፡ ሁሉ ፡ ለወታደር ፡ ቀለብ ፡ በ መስጠትና ፡ በሴቶች ፡ ፍትወት ፤ በሌላውም ፡ በከተማ ፡ ችግር ፡ ሁሉ ፡ ጨርሰው ፡ ባዶ ፡ እጃቸውን ፡ ሲቀሩ ፡ ወታደራቸው ፡ እየተዋቸው ፡ ስለ ፡ ሔደ ፡ ኃይላቸው ፡ ሁሉ ፡ ደከመና ፡ እንደ ፡ ፈቃዱ ፡ ይገዛቸው ፡ ጀመር ።

ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ ልጆቹና ፤ የልጅ ፡ ልጆቹ ፡ እስከ ፡ ፲፬ ፡ ትው ልድ ፡ እንደዚህ ፡ እያደረጉ ፡ ከገዙ ፡ በኋላ ፡ ከ፲፭ኛው ፡ ትውልድ ፡ ሲደርስ ፡ ሚጂ ፡ ነገሡና ፡ የመንግሥቱ ፡ አኳኋን ፡ እየተለወጠ ፡ ስለ ፡ ሔደ ፡ የቶኩጋዋ ፡ ትውልድ ፡ ግዛትና ፡ ሥልጣን ፡ ወደ ፡ መውደቅ ፡ ደረሰ ።

የመንግሥቱም ፡ አኳኋን ፡ የተለወጠበት ፡ ምክንያቱ ፡ በሀገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ ተፍጻሜተ ፡ መንግሥት ፡ አጼ ፡ ተክለ ፡ ጊዮርጊስ ፡ ከሞቱ በት ፡ ከሺ፯፻፸፪ ፡ ዓመ ፡ ም ፡ ጀምሮ ፡ ሰባ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ሙሉ ፡ መሳፍንቱ ፡ የንገሥታቱን ፡ ዘር ፡ ሳያጠፉ ፡ በየተራ ፡ በዙፋን ፡ እያስቀመጡ ፡ አገሩን ፡ ይገዙት ፡ እንደ ፡ ነበረው ፡ ነው ።

በኢትዮጵያ ፡ በስም ፡ ብቻ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ እየተባሉ ፡ በዙፋን ፡ የተቀመጡ ፡ ነገሥታት ፡ አሥራ ፡ ሶስት ፡ ናቸው ።

ስማቸውም ፡ ከዚህ ፡ እንደሚከተለው ፡ ነው ።

፩ኛ ። አጼ ፡ ሕዝቅያስ ።

፪ኛ ። አጼ ፡ በእደ ፡ ማርያም ።

፫ኛ ። አጼ ፡ ሰሎሞን ።

፬ኛ ። አጼ ፡ ዮናስ ።

፭ኛ ። አጼ ፡ ዲሙ ።

፮ኛ ። አጼ ፡ ጓሉ ፡ (እጓለ ፡ ጽዮን ፡)

፯ኛ ። አጼ ፡ ኢዮአስ ።
፰ኛ ። አጼ ፡ ጊጋር ።
፱ኛ ። አጼ ፡ በእደ ፡ ማርያም ።
፲ኛ ። አጼ ፡ ኢያሱ ።
፲፩ኛ ። አጼ ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስ ።
፲፪ኛ ። አጼ ፡ ሣህሉ ።
፲፫ኛ ። አጼ ፡ ዮሐንስ ።

የመሳፍንቱም ፡ ቍጥር ፡ ስምንት ፡ ነው ።

፩ኛ ። ራስ ፡ አሊጋዝ ። ( ትልቁ ፡ አሊ )
፪ኛ ። ራስ ፡ አሥራት ።
፫ኛ ። ራስ ፡ ወልደ ፡ ገብርኤል ።
፬ኛ ። ራስ ፡ ጉግሣ ።
፭ኛ ። ራስ ፡ ይማም ።
፮ኛ ። ራስ ፡ ማርየ ።
፯ኛ ። ራስ ፡ ዶሪ ።
፰ኛ ። ራስ ፡ አሊ ። ( ትንሹ ፡ አሊ )

ቢሆንም ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ የተቆጠሩት ፡ መሳፍንት ፡ ይገዙት ፡ የነበረው ፡ በጌምድርንና ፡ በበጌምድር ፡ ዙሪያ ፡ ያሉትን ፡ አገሮች ፡ ብቻ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ ሸዋን ፡ ትግሬን ፤ ጎጃምን ፤ ወሎን ፡ በጭራሽ ፡ ጠቅልለው ፡ አልገዙም ፡ ነበርና ፡ የኢትዮጵያ ፡ መሳፍንትና ፡ የጃፓን ፡ መሳፍንት ፡ ልዩነታቸው ፡ በዚህ ፡ ብቻ ፡ ነበር ።

ስለዚህ ፡ የዘመን ፡ ብዛትና ፡ የትውልድ ፡ ማለፍ ፡ ሁሉንም ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ ያስመስለዋል ፡ እንጂ ፡ ከፀሐይ ፡ በታች ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ የለም ፡ ያለውን ፡ የሰሎሞንን ፡ ቃል ፡ መመልከት ፡ ይገባል ። መክ ፡ ፩ ፡ ፱—፲፩ ።

---

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ።

እንግዲህ ፡ በሚጂ ፡ ዘመን ፡ የከተማውና ፡ የመንግሥቱ ፡ አኳኋን ፡ የተለዋወጠበትን ፡ ምክንያቱን ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ በተጻፈው ፡ ቃል ፡ እናስረዳለን ።

በ፲፰፻፷፯ ፡ ዓ ፡ ም ፡ ነግሦ ፡ የነበረው ፡ የሚጂ ፡ አባት ፡ ከሜይ ፡ ከውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ አይገናኝም ፡ ነበር ። በዘመኑም ፡ የነበረው ፡ የጃፓን ፡ መንግሥት ፡ እንደራሴ ፡ የነበረው ፡ ኢዬሞቼ ፡ ቶኩጋዋ ፡ የሚባለው ፡



በቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ በጦር ፡ ሚኒስቴር ፡ ጽሕፈት ፡ ቤት ፡ ከጦር ፡ አለቆች ፡ ጋራ ፡ ስንገናኝ ።

የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎችን ፡ አይወድም ፡ ነበር ። ስለዚህ ፡ ከወታደር ፡ አለቆችና ፡ ካገረ ፡ ገዥዎችም ፡ ወገን ፡ ኃይል ፡ የተሰማው ፡ አንዳንዱ ፡ በውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ፈቃዱ ፡ ይሠራ ፡ ነበር ።

የሳትሱማ ፡ አውራጃ ፡ ገዥ ፡ የነበረው ፡ ፰፻ ፡ ወታደር ፡ አስከትሎ ፡ ከዮዶ ፡ ወደ ፡ ዮኮሃማ ፡ ሲሔድ ፡ ሶስት ፡ የእንግሊዝ ፡ ነጋዴዎች ፡ ካንዲት ፡ ሴት ፡ ጋራ ፡ በፈረሶች ፡ ተቀምጠው ፡ ሲሔዱ ፡ በመንገድ ፡ ላይ ፡ ቢገናኙ ፡ ነጋዴዎቹ ፡ ከፈረሶቻቸው ፡ ላይ ፡ ሳይወርዱ ፡ መንገዱን ፡ ብቻ ፡ ለቀው ፡ ዘወር ፡ አሉ ። በዚያ ፡ ዘመን ፡ ትልቅ ፡ ጌታ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ በመንገድ ፡ ሲያልፍ ፡ እግረኛ ፡ እያጎነበሰ ፤ ፈረሰኛ ፡ ከፈረስ ፡ እየወረደ ፡ እጅ ፡ ይነሣ ፡ ነበርና ፡ እነዚህ ፡ የእንግሊዝ ፡ ነጋዴዎች ፡ በሳትሱማ ፡ ገዥ ፡ አጠገብ ፡ ከፈረሶቻቸው ፡ ሳይወርዱ ፡ ስለ ፡ አለፉ ፡ ያዙዋቸው ፡ ብሎ ፡ አንዱ ፡ ብቻ ፡ ጋልቦ ፡ ሲያመልጥ ፡ ሁሉንም ፡ አስገደላቸው ።

በዚህም ፡ ምክንያት ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ መርከቦች ፡ ሁሉ ፡ ባንድነት ፡ ሆነው ፡ ሺሞኖስኪ ፡ በሚባለው ፡ በባሕር ፡ ዳር ፡ ከተማ ፡ ይተኩሱበት ፡ ጀመር ።

በኋላ ፡ ግን ፡ ፫ ሚሊዮን ፡ የአሜሪካ ፡ ብር ፡ እንዲክሱና ፡ እርቅ ፡ እንዲሆን ፡ ስምምነት ፡ አደረጉ ። ይህንንም ፡ ካሣውን ፡ የሳትሱማን ፡ ገዥ ፡ ክፈል ፡ ቢሉት ፡ እምቢ ፡ ስላለ ፡ የመንግሥቱም ፡ እንደራሴ ፡ በኃይል ፡ ለማስከፈል ፡ ስላልቻለ ፡ ከመንግሥት ፡ ግምጃ ፡ ቤት ፡ ተከፈለ ።

ቢሆንም ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ከውጭ ፡ አገር ፡ መንግሥቶች ፡ ጋራ ፡ የተወሰነ ፡ የንግድ ፡ ውል ፡ አልተደረገም ፡ ነበርና ፡ ከውጭ ፡ አገር ፡ በሚገባው ፡ የንግድ ፡ ዕቃ ፡ ላይ ፡ ቀረጥ ፡ አብዝተው ፡ ጨምረው ፡ ከሣራቸውን ፡ መለሱ ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በሺ፰፻፷፯ ፡ ዓ ፡ ም ፡ የመንግሥቱ ፡ እንደራሴ ፡ የነበረው ፡ ኢዬሞቹ ፡ ቶኩጋዋ ፡ ሞተና ፡ ልጁ ፡ ኪይኪ ፡ ቶኩጋዋ ፡ ባባቱ ፡ ስፍራ ፡ ተተካ ። ቀጥሎም ፡ ባመቱ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ጠላት ፡ የነበረው ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ኮሜይ ፡ ሞተና ፡ ልጁ ፡ ሚጂ ፡ ነገሠ ።

ነገር ፡ ግን ፡ ከሁለት ፡ ዓመት ፡ በፊት ፡ በኮሜይ ፡ ዘመን ፡ ሳይጎታካምሪና ፡ አኩቦ ፡ ቶሺሚቼ ፡ የሚባሉ ፡ ትልልቅ ፡ ባላባቶች ፡ በእንደራሴ ፡ የምንገዛው ፡ ለምንድነው ፤ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ እንደ ፡ ጥንቱ ፡ ዋና ፡ ሆኖ ፡ የመንግሥቱን ፡ ሥራ ፡ ለያንዳንዳችን ፡ እያከፋፈለ ፡ እየ

ሰጠን ፡ እንሠራዋለን ፡ እያሉ ፡ በምስጢር ፡ ከየትልልቁ ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ ተነጋግረው ፡ ጨርሰው ፡ ነበርና ፡ አሁን ፡ የፊተኛው ፡ እንደራሴና ፡ የፊተኛው ፡ ንጉሥ ፡ ሞተው ፡ ልጆቻቸው ፡ በየስፍራቸው ፡ መተካታቸውን ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡ ከዛሬ ፡ የተሻለ ፡ ጊዜ ፡ አናገኝም ፡ በማለት ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ባለበት ፡ በኪዮቶ ፡ የመንግሥቱን ፡ ሥራ ፡ ተከፋፍለው ፡ ይዘው ፡ ይሠሩ ፡ ጀመር ።

ለመንግሥቱም ፡ ሥራ ፡ አንድ ፡ ጠቅላይ ፡ ሚኒስትርና ፡ ምክትል ፡ ሚኒስትር ፡ ሰባት ፡ አማካሪዎች ፡ ተመርጠው ፡ ከንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ እየተማከሩ ፡ የመንግሥቱን ፡ ሥራ ፡ እንዲጨርሱ ፡ ተደረገ ።

ኪይኪም ፡ ለጊዜው ፡ ሥራውን ፡ ለመሥራት ፡ ጀምሮ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ እጁን ፡ የሚያገባበት ፡ አንድ ፡ ሥራ ፡ እንኳ ፡ አላገኘምና ፡ በዚያ ፡ ዘመን ፡ የነበሩትን ፡ የፊዎዳል ፡ ጌቶች ፡ ሁሉ ፡ ሰብስቦ ፡ ምክር ፡ ቢጠይቃቸው ፡ እንደ ፡ አባቶቹ ፡ የመንግሥቱን ፡ ሥራ ፡ እንድሠራ ፡ሙሉ ፡ ሥልጣን ፡ ስጠኝ ፡ ብለህ ፡ ለንጉሡ ፡ ጻፍለት ፡ ብለው ፡ መከሩት ።

መቸውንም ፡ ቢሆን ፡ በእንደራሴ ፡ መግዛትን ፡ የማይወዱ ፡ ባላባቶች ፡ ናቸው ፡ እንጂ ፡ ፊዎዳሎች ፡ እጅግ ፡ ጉዳት ፡ የለባቸውምና ፡ ከእንደራሴው ፡ ጋራ ፡ ናቸው ።

ኪይኪም ፡ ለማናቸውም ፡ ነገር ፡ እንዲቀርበው ፡ ዛሬ ፡ ቶኪዮ ፡ ከተባለው ፡ ከአባቶቹ ፡ ከተማ ፡ ከዬዶ ፡ ተነሥቶ ፡ በመርከብ ፡ ሆኖ ፡ ወደ ፡ኦሳካ ፡ ሔዶ ፡ ነበርና ፡ በኦሳካ ፡ ሆኖ ፡ እንደ ፡ አባቶቹ ፡ ሙሉ ፡ ሥልጣን ፡ ስጠኝ ፤ ብሎ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ቢጽፍ ፡ ንጉሡ ፡ አማካሪዎቹ ፡ ምላሽ ፡ አትስጥ ፡ ብለው ፡ ስለ ፡ መከሩት ፡ ዝም ፡ አለው ። ኪይኪም ፡ ለደብዳቤው ፡ ምላሽ ፡ አለማግኘቱንና ፡ ከእንደራሴነቱ ፡ ሥራ ፡ በጭራሽ ፡ መውጣቱን ፡ አይቶ ፡ ፲ሺ ፡ ወታደሮች ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ኪዮቶ ፡ ተጓዘ ። ከንጉሡም ፡ ጋራ ፡ የሆኑት ፡ ትልልቆቹ ፡ ባላባቶች ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱን ፡ ዘበኞች ፡ ይዘው ፡ በጥር ፡ ወር ፡ ፉሲሚ ፡ በሚባል ፡ ስፍራ ፡ ላይ ፡ ተጋጥመው ፡ ፭፻ ፡ ቀን ፡ ሙሉ ፡ ከተዋጉ ፡ በኋላ ፡ ድል ፡ አደረጉት ፤ እርሱም ፡ ወደ ፡ ኦሳካ ፡ ሸሽቶ ፡ በምሽጉ ፡ ውስጥ ፡ ገባ ፤ ጠላቶቹም ፡ ተከታትለው ፡ ሔደው ፡ ነበርና ፡ ምሽጉን ፡ ለመስበር ፡ የማይቻላቸው ፡ ቢሆን ፡ እሳት ፡ ለቀቁበት ። ኪይኪ ፡ ግን ፡ ባንድ ፡ ወገን ፡ ሾልኮ ፡ ወጥቶ ፡ በመርከብ ፡ ገብቶ ፡ ወደ ፡ ዬዶ ፡ ተመለሰ ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ጦርነት ፡ ለማድረግ ፡ የማይቻለው ፡ መሆኑን ፡ አይቶ ፡ የዬዶን ፡ ከተማና ፡ እንደራሴነቱን ፡ ስላስረከበ ፡ ሚቶና ፡ ሱራ

ጋ ፡ በሚባሉት ፡ ርስቶቹ ፡ ላይ ፡ እንዲቀመጥ ፡ ተፈቀደለት ። የሚጂም ፡ አማካሪዎች ፡ ለማናቸውም ፡ ለውጭ ፡ አገር ፡ መንግሥቶች ፡ መገናኛና ፡ ወዲያውም ፡ የቶኩጋዋን ፡ ዘር ፡ ለማድከም ፤ ለምሥራቁና ፡ ለምዕራቡም ፡ አገር ፡ አማካይ ፡ ነውና ፡ ዋናው ፡ ከተማ ፡ ኪዮቶ ፡ መሆኑ ፡ ቀርቶ ፡ ዬዶ ፡ ይሁን ፡ ብለው ፡ ስለመከሩት ፡ ከተማውን ፡ ከኪዮቶ ፡ ወደ ፡ ዬዶ ፡ አዛወረ ። ስሙንም ፡ ቶኪዮ ፡ ብሎ ፡ ሰየመው ።

ትርጓሜውም ፤ የምሥራቅ ፡ ከተማ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ይህንም ፡ የመሰለው ፡ አደራረግ ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ ከቀድሞ ፡ ጀምሮ ፡ እስካሁን ፡ ሲደረግ ፡ ይኖራል ። የቀድሞውም ፡ ይቅርና ፡ አሁን ፡ በቅርቡ ፡ በአፄ ፡ ሚኒልክ ፡ ዘመን ፡ እንኳ ፡ ፊንፊኒ ፡ ሲባል ፡ የኖረው ፡ አዲስ ፡ አበባ ። ሜታ ፡ ሲባል ፡ የኖረው ፡ አዲስ ፡ ዓለም ። ሆሎታ ፡ ሲባል ፡ የኖረው ፡ ገነት ፡ ተብሏል ።

አሁን ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ የተሠራው ፡ የመስፍኑ ፡ የቶኩጋዋ ፡ ቤት ፡ በነበረበት ፡ ስፍራ ፡ ላይ ፡ ነው ። ከተሠራም ፡ ፵፫ ፡ ዓመቱ ፡ ነው ።

የስፍራው ፡ አቀማመጥ ፡ እንደ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ስፍራ ፡ ትንሽ ፡ ከፍታ ፡ ያለው ፡ ነው ። የዛፉም ፡ ዓይነት ፡ ልዩ ፡ ይሁን ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ዙሪያውን ፡ በዱር ፡ የተሸፈነ ፡ ነው ። በመጀመሪያው ፡ ቶኩጋዋ ፡ ዘመን ፡ የተተከሉት ፡ ዛፎች ፡ እስካሁንም ፡ አምረውና ፡ ለምልመው ፡ ይታያሉ ።

ከቀድሞው ፡ እድሞ ፡ በስተ ፡ ግንባር ፡ ያለውን ፡ ቦታ ፡ ለሕዝብ ፡ መመላለሻና ፡ መናፈሻ ፡ ይሁን ፡ ብለው ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ከፍለው ፡ አስቀርተውለታል ። ምሽጉ ፡ ብርቱና ፡ ጠንካራ ፡ ነው ።

በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ የጃፓን ፡ አገር ፡ መሳፍንትና ፡ ሌሎችም ፡ ባላባቶች ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ይዋጉ ፡ ነበርና ፡ እየፈሩ ፡ ቤታቸውን ፡ ሲሠሩ ፡ ዙሪያውን ፡ በትልልቅ ፡ ድንጋይ ፡ ርዝመቱ ፡ ከ፩ ሜትር ፡ እስከ ፡ ፯ ፡ ሜትር ፡ ስፋቱ ፡ (አርመኑ ፡)ከ፪ ሜትር ፡ እስከ ፡ ፫ ሜትር ፡ የሆነ ፡ እድሞ ፡ (ቅጥር) እየሠሩ ፡ ከቅጥሩ ፡ ውጭ ፡ ጉድባ ፡ እየተቆፈረ ፡ ወሀ ፡ በቦይ ፡ እያመጡ ፡ ባሕር ፡ ያደርጉት ፡ ነበር ። ምክንያቱም ፡ በዚያ ፡ ዘመን ፡ ጦርነታቸው ፡ በቀስትና ፡ በጦር ፡ በጐራዴ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ፈረሰኛም ፡ እግረኛም ፡ በሌላ ፡ በኩል ፡ እንዳይገባባቸው ፡ በሩን ፡ ብቻ ፡ ይዘው ፡ ለመዋጋት ፡ ነበር ። በኢትዮጵያም ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ እንጦጦ ፡ ራጉ

ኤል ፡ ላይ ፡ በነበረ ፡ ጊዜ ፡ አጼ ፡ ምኒልክ ፡ ዙሪያውን ፡ ጉድባ ፡ አስቆፍረ ውት ፡ ነበርና ፡ ጉድባው ፡ ዛሬውኑ ፡ ይታያል ። ስለዚህ ፡ በያገሩ ፡ ያለው ፡ የቀድሞው ፡ ልማድ ፡ ይመስላል ።

በቶኪዮ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ዙሪያ ፡ ያለው ፡ ጉድባና ፡ ባሕር ፡ ምን ም ፡ ዛሬ ፡ ከመድፍና ፡ ከመትረየስ ፡ ባያድን ፡ የሚያስፈራም ፡ ነገር ፡ ባይ ኖር ፡ እንደ ፡ ቀድሞው ፡ ይኑር ፡ ተብሎ ፡ ቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ በባሕር ፡ ተ ከበ ፡ ይታያል ።

የቤተ ፡ መንግሥቱም ፡ ዋናው ፡ በር ፡ ሁለት ፡ ድልድይ ፡ ይባላል ። በ አፊሴል ፡ ወደ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ የሚገባ ፡ ሁሉ ፡ በ ዚህ ፡ በር ፡ ነው ።

በቶኪዮ ፡ ወደ ፡ ሁለት ፡ ድልድይ ፡ ሔዱል ፡ ሲባል ፡ በአፊሴል ፡ መ ግባቱ ፡ ይታወቃል ።

ሁለት ፡ ድልድይም ፡ የተባለበት ፡ ምክንያት ፡ የጉድባው ፡ ውሀ ፡ ዙ ሪያውን ፡ ከዞረ ፡ በኋላ ፡ በዋናው ፡ በር ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ጥቂት ፡ ወጣ ፡ አድርገው ፡ ለዘበኞች ፡ ማደሪያ ፡ ቤት ፡ ሠርተው ፡ የዘበኞቹ ፡ ቤት ፡ የተ ሠራበት ፡ ቦታ ፡ እንደ ፡ ደሴት ፡ ሆኗል ። ስለዚህ ፡ ከውጭ ፡ የሚመጣ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ዘበኞቹ ፡ መቆሚያ ፡ ቤት ፡ የሚወስደውን ፡ መን ገድ ፡ ይዞ ፡ ሲገባ ፡ አንዱን ፡ ድልድይ ፡ ይሻገራል ። ያንንም ፡ አልፎ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ሲገባ ፡ ሁለተኛውን ፡ ድልድይ ፡ ይሻገራል ። ወደ ፡ ቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ በአፊሴል ፡ የማይገባ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱንና ፡ የእቴጌይቱን ፡ ጤና ፡ ለመጠየቅ ፡ በ፪ኛው ፡ በር ፡ እየገባ ፡ የእን ግዳ ፡ ማረፊያ ፡ በተባለው ፡ ቤት ፡ ስሙን ፡ በመዝገብ ፡ እየጻፈ ፡ ይወጣል ።

ለዚሁም ፡ ሥራ ፡ የታዘዘው ፡ ሹም ፡ በቀን ፡ በቀኑ ፡ የመጡት ፡ እ ንግዶች ፡ ስማቸውን ፡ የጻፉበትን ፡ መዝገብ ፡ ለንጉሡና ፡ ለንግሥቲቱ ፡ እያቀረበ ፡ ያሳያል ። እኛም ፡ ቤተ ፡ መንግሥቱን ፡ አይተን ፡ ስንወጣ ፡ በዚሁ ፡ መዝገብ ፡ ላይ ፡ ስማችንን ፡ ጽፈናል ።

---

## ምዕራፍ ፡ ፳፯ ።

## ወደ ፡ ዮኮሃማና ፡ ወደ ፡ ካማኩራ ፡ ስለ ፡ መሔዳችን ።

ዮኮሃማ ፡ ያለው ፡ የፈረንሳዊ ፡ ቆንስል ፡ ሙሴ ፡ ቤልፎን ፡ የሚባለ ው ፡ ለራት ፡ ጋብዞን ፡ ነበርና ፡ በታኅሣሥ ፡ ፱ቀን ፡ በ፲ ፡ ሰዓት ፡ ወደ ፡ ዮኮሃማ ፡ ሔድን ።



በቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ በባልደረባችን ፡ በምስተር ፡ ዋታናቢ ፡ ቤት ፡ ሻይ ፡ ተጋብዘን ፡ ስንወጣ ።




ዮኮሐማ ፡ የሚባለው ፡ የጃፓን ፡ የባሕር ፡ ወደብ ፡ ከተማ ።

ሙሴ ፡ ቤልፎን ፡ ፓሪስ ፡ ላይ ፡ በውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስቴር ፡ በ ኢትዮጵያ ፡ አገር ፡ ለሚሆነው ፡ ጉዳይ ፡ ጸሐፊ ፡ ነበርና ፡ ወደ ፡ ፓሪስ ፡ በተመላለስሁበት ፡ ጊዜ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስቴር ፡ ስሔድ ፡ የሚያነጋግረኝና ፡ ጉዳዬን ፡ የሚፈጽምልኝ ፡ እርሱ ፡ ነበር ።

ደግሞ ፡ ጊዜ ፡ አጋጥሞት ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ መጥቶ ፡ ከጃንሆይ ፡ ቀዳሚዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ጋራ ፡ ተገናኝቶ ፡ ሲሔድ ፡ በወዳጅነት ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ ስለ ፡ መጣ ፡ በጣም ፡ ተላምደን ፡ ነበር ።

እርሱም ፡ ከኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ተልከን ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ መምጣታችንኝ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ዮኮሃማ ፡ ሔደን ፡ ራት ፡ እንድንጋበዝ ፡ ቢጽፍልኝ ፡ የኦፊሴሉ ፡ ቀን ፡ ሳይጨረስ ፡ አይመቸኝም ፡ ብዬው ፡ ነበርና ፤ አሁን ፡ የኦፊሴሉ ፡ ቀን ፡ መጨረሱን ፡ ሰምቶ ፡ እንደገና ፡ ስለ ፡ ጻፈልኝ ፡ ወደ ፡ ዮኮሃማ ፡ ሔድን ።

በዚሁም ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ አጋጣሚ ፡ ሙሴ ፡ ቤልፎን ፡ የዮኮሃማ ፡ ቆንስልነቱን ፡ ለቆ ፡ በአሜሪካ ፡ ሳን ፡ ፍራንሲስኮ ፡ ወደ ፡ ሚባለው ፡ ተሾሞ ፡ መሔዱ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ አምባሳዶሩንና ፡ ሌሎቹንም ፡ በዮኮሃማ ፡ ያሉትን ፡ የፈረንሳዊንና ፡ የጃፓንን ፡ ትልልቅ ፡ ሰዎች ፡ ጠርቶ ፡ ኖሮ ፡ በታላቅ ፡ ደስታ ፡ አመሸን ። በቤቱም ፡ ሳሎን ፡ ( አዳራሽ )የጃንሆይ ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴን ፡ ፎቶግራፍና ፡ ሌላውንም ፤ ወደ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ የወሰደውን ፡ ማለፊያ ፡ ማለፊያ ፡ መታሰቢያ ፡ አስቀምጦ ፡ ለመጡት ፡ እንግዶች ፡ ሁሉ ፡ ያሳይ ፡ ነበር ።

ከአዲሱም ፡ ቆንስል ፡ ጋራ ፡ ሁላችንንም ፡ አስተዋወቀን ።

ወደ ፡ ቶኪዮም ፡ ለመመለስ ፡ ጊዜው ፡ ስለ ፡ መሸ ፡ በዮኮሃማ ፡ ኺው ፡ ግራንድ ፡ ሆቴል ፡ በሚባለው ፡ አድረን ፡ በማግሥቱ ፡ ጧት ፡ መርከቦች ፡ የሚቆሙበትን ፡ የባሕሩን ፡ ወደብ ፡ ስናይ ፡ አረፈድን ።

አራት ፡ ሰዓት ፡ ሲሆን ፡ ከዮኮሃማ ፡ ተነሥተን ፡ ወደ ፡ ካማኩራ ፡ ሔድን ። ካማኩራ ፡ ከዮኮሃማ ፡ በኤሌክትሪክ ፡ ባቡር ፡ ፴ደቂቃ ፡ ያስሔዳል ። የካማኩራ ፡ ከተማ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ዓይነት ፡ ዛፎች ፡ የተሸፈነ ፡ በባሕር ፡ ዳር ፡ የተሠራ ፡ ነው ። በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ ሹጎን ፡ የሚባሉት ፡ የነገሥታቱ ፡ እንደራሴዎች ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ እየሔዱ ፡ የሚያርፉበት ፡ ነው ። ስለ ፡ ሀገሩ ፡ መልካምነትና ፡ ስለ ፡ ከተማው ፡ ማማር ፡ ስለ ፡ ፀጥታውም ፡ ቢሆን ፡ ዛሬውኑ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ቤተ ፡ ዘመዶች ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ እየሔዱ ፡ ይናፈሱበታል ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

የውጭ ፡ አገርም ፡ ሰዎች ፡ ለመናፈስ ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ ሲመጡ ፡ ካማኩራ ፡ ሳይደርሱና ፡ የሀገሩን ፡ መልካምነት ፡ የከተማውን ፡ ውበት ፡ ሳያዩ ፡ አይሔዱም ፤ ይልቁንም ፡ እጅግ ፡ የሚያስደንቀው ፡ ከመዳብና ፡ ከነሐስ ፡ የተሠራው ፡ የቡዳሃ ፡ ምስል ፡ አለና ፡ ያንን ፡ ለማየት ፡ ሲሉ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ካማኩራ ፡ ይሔዳሉ ። እኛም ፡ ካማኩራ ፡ በደረስን ፡ ጊዜ ፡ መጀመሪያ ፡ የቡዳሃ ፡ ምስል ፡ ወደ ፡ ቆመበት ፡ ስፍራ ፡ ሔድን ፤ ምስሉ ፡ የቆመው ፡ በብዙ ፡ ዛፍ ፡ መካከል ፡ በሜዳ ፡ ላይ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በቤት ፡ ውስጥ ፡ አይደለም ።

ይህንም ፡ ምስል ፡ የሠራው ፡ በ፯፻፵፯ ፡ ዓ ፡ ም ፡ ነግሦ፡ የነበረው ፡ ሾሙ ፡ የሚባለው ፡ ነው ። እርሱ ፡ የቡዳሃን ፡ ሃይማኖትና ፡ ካህናት ፡ ይወድ ፡ ነበርና ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ በብዙ ፡ ስፍራ ፡ የቡዳሃን ፡ ምስል ፡ አቁሟል ። ግን ፡ ከሁሉ ፡ የሚበልጠው ፡ በካማኩራ ፡ ያቆመው ፡ ምስል ፡ ነው ።

ወደ ፡ ላይ ፡ ርዝመቱ ፡ ፲፪ ፡ ሜትር ፡ ከ፹፱ ሳንቲ ። ዙሪያው ፡ ውፍረቱ ፡ ፳፱ ፡ ሜትር ፡ ከ፳፱ ፡ ሳንቲ ። የፊቱ ፡ ስፋት ፡ ፪ሜትር ፡ ከ፴፫ ፡ ሳንቲ ። ከዓይኑ ፡ እስከ ፡ ዓይኑ ፡ ፩ሜትር ። ከጆሮው ፡ እስከ ፡ ጆሮው ፡ ፪ ፡ ሜትር ፡ ከ፩ ፡ ሳንቲ ። አፍንጫው ፡ ፹፭ ፡ ሳንቲ ። አፉ ፡ ፹፩ ፡ ሳንቲ ። ከጉልበቱ ፡ እስከ ፡ ጉልበቱ ፡ ፱ ፡ ሜትር ፡ ከ፱ ፡ ሳንቲ ፡ ነው ።

ውስጡ ፡ ክፍት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ገንዘብ ፡ እየተከፈለ ፡ ውስጥ ፡ ለውስጥ ፡ በመሰላል ፡ ይወጣና ፡ ከወገቡ ፡ ላይ ፡ ማረፊያ ፡ እርከን ፡ አለው ። በእርከኑ ፡ ላይ ፡ ሁለት ፡ ሰፋፊ ፡ መስኮት ፡ ተደርጎለታል ፤ በስተ ፡ ውስጥ ፡ በጀርባው ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ጠረጴዛ ፡ ሆኖ ፡ ተሠርቶ ፡ ቁመቱ ፡ ፳ሳንቲም ፡ የሚሆን ፡ ከጥሩ ፡ ወርቅ ፡ ብቻ ፡ የተሠራ ፡ የቡዳሃ ፡ ምስል ፡ ቆሞ ፡ ይታያል ። ትልቁ ፡ ምስል ፡ ታቹም ፡ ላዩም ፤ ግቢውም ፡ ውጭውም ፡ ከመዳብ ፡ የተሠራ ፡ ነው ።

የቀድሞ ፡ ዘመን ፡ የጃፓን ፡ ነገሥታት ፡ ለዚህ ፡ ለማይረባ ፡ ምስል ፡ ገንዘባቸውን ፡ መጨረሳቸው ፤ የሕዝባቸውን ፡ ጉልበት ፡ ማድከማቸው ፤ ለዛሬ ፡ ዘመን ፡ ልጆች ፡ በጣም ፡ ያሳዝናል። ለመታሰቢያ ፡ ያህል ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ ወይም ፡ አንድ ፡ ሜትር ፡ ቢሠሩ ፡ ይበቃቸው ፡ ነበር ። ራሱ ፡ ቡዳሃም ፡ ለድሀ ፡ እንዲራሩ ፤ ምጽዋት ፡ እንዲመጸውቱ ፡ አስተምሮ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ ተራራ ፡ የሚያህል ፡ ምስል ፡ አቁሙልኝ ፡ ብሎ ፡ አላስተማረም ፡ ነበር ።

ዐ ወን ፖ ባ ፆ

## ምዕራፍ ፡ ፳፯ ።

## የኢትዮጵያን ፡ መንግሥት ፡ ቀደምትነትና ፡ የነገሥታቱን ፡ ትውልድ ፤ የሕዝቡንም ፡ ክርስቲያንነት ፡ ስለ ፡ ማስረዳት ።

መጀመሪያ ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ እንደ ፡ ደረስን ፡ ጋዚጠኞች ፡ መጥተው ፡ የኢትዮጵያን ፡ መንግሥትና ፡ የነገሥታቱን ፡ አኳኋን ፡ የሕዝቡንም ፡ ሃይማኖት ፡ ስለ ፡ ጠየቁን ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ ከተመሠረተ ፡ ከሶስት ፡ ሺ ፡ ዘመን ፡ ይበልጣል ፤ የነገሥታቱም ፡ ትውልድ ፡ ከቀዳማዊ ፡ ምኒልክ ፡ ጀምሮ ፡ እስካሁን ፡ ድረስ ፡ ሳያቋርጥ ፡ ተያይዞ ፡ የመጣ ፡ ነው ። የሕዝቡም ፡ ሃይማኖት ፡ ከእስክንድርያ ፡ የግብጽ ፡ ኦርቶዶክስ ፡ የመጣ ፡ የክርስቲያን ፡ ሃይማኖት ፡ ነው ፡ ብለን ፡ ነግረናቸው ፡ ነበርና ፡ ይህንኑ ፡ በጋዜጣ ፡ ስለ ፡ አወጡት ፡ ጋዜጣውን ፡ ያነበቡ ፡ አንዳንድ ፡ የጃፓንና ፡ የአሜሪካ ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ እኛ ፡ እየመጡ ፡ ይህ ፡ በጋዜጣ ፡ የወጣው ፡ ቃል ፡ እውነት ፡ መሆኑን ፡ እየጠየቁን ፡ እውነት ፡ ነው ፡ ብለን ፡ ስንመልስላቸው ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሰዎች ፡ መንግሥታችሁ ፡ አዲስ ፡ ሃይማኖታችሁም ፡ የእስላሞች ፡ ወይም ፡ የአረመኔዎች ፡ ይመስለን ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ መንግሥታችሁ ፡ ጥንታዊ ፡ ሃይማኖታችሁ ፡ የክርስቲያን ፡ መሆኑን ፡ አናውቅም ፡ ነበር ፡ እያሉ ፡ እየተደነቁ ፡ ይመለሱ ፡ ነበር ።

ከነዚሁም ፡ ያንድ ፡ የአሜሪካ ፡ ትምሕርት ፡ ቤት ፡ አለቃ ፡ የሚባለው ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ መጥቶ ፡ የኢትዮጵያን ፡ መንግሥት ፡ ቀደምትነትና ፡ የነገሥታቱንም ፡ አኳኋን ፤ የሕዝቡንም ፡ ሃይማኖት ፡ ለማስረዳት ፡ ይችሉ ፡ እንደሆነ ፡ ትልቅ ፡ ጉባኤ ፡ እናድርግና፡ በንግግርዎ ፡ ያስረዱን ፤ ከጃፓኖችም ፡ ወገን ፡ ወደ ፡ ክርስቲያንነት ፡ የተመለሱት ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ከቃልዎ ፡ ለመስማት ፡ ብዙ ፡ ምኞት ፡ አላቸውና ፡ ይህን ፡ ቢያደርጉልን ፡ ሁላችንም ፡ ደስ ፡ ይለናል ፡ ብሎ ፡ ነገረኝ ።

እኔም ፡ የአፌሴሉ ፡ ቀን ፡ እስከ ፡ አንድ ፡ ወር ፡ ነውና ፡ የአፌሴሉ ፡ ቀን ፡ ሳይፈጸም ፡ ይህን ፡ ለማድረግ ፡ ጊዜ ፡ የለኝም ። የአፌሴሉ ፡ ቀን ፡ ከተፈጸመ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ምንም ፡ በረጅሙ ፡ እንኳ ፡ ባይሆን ፡ ባጭሩ ፡ እየተናገርሁ ፡ አስረዳችኋለሁ ፡ ብዬ ፡ ቀኑን ፡ ቀጥሬ ፡ መለስሁት ።

በቀጠሮውም ፡ ቀን ፡ ጉባዔው ፡ ወደ ፡ ተሰበሰበበት ፡ ስፍራ ፡ ከማታው ፡ ባንድ ፡ ሰዓት ፡ ሔድን ። የመንገዱ ፡ ርቀት ፡ እኛ ፡ ካለንበት ፡ ሆቴል ፡ በአውቶሞቢል ፡ ፺ ደቂቃ ፡ ያስሔዳል ።

የተሰበሰቡትም ፡ ሰዎች ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ነበሩ ። ከዮክሃማ ፡ ድረስ ፡ ብዙ ፡ ጃፓኖችና ፡ አሜሪካኖች ፡ መጥተው ፡ ነበር ። ስለ ፡ ሰዎቹም ፡ ብዛት ፡ ባንድነት ፡ ራት ፡ ለመጋበዝ ፡ ቤቱ ፡ የማይበቃ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ቢፌ ፡ የሚባለው ፡ ራት ፡ ተዘጋጅቶ ፡ ነበር ።

ቢፌ ፡ ማለት ፡ ምግቡና ፡ መጠጡ ፡ በያይነቱ ፡ ተዘጋጅቶ ፡ ባንድ ፡ ክፍል ፡ ቤት ፡ በሰፊ ፡ ጠረጴዛ ፡ ላይ ይቀመጥና ፡ ወንዱም ፡ ሴቱም ፡ ሰሐኑን ፡ እየያዘ ፡ እየቀረበ ፡ ባይኑ ፡ ካየውና ፡ ከወደደው ፡ ዓይነት ፡ እያነሣ ፡ በየቤቱ ፡ ክፍል ፡ እየቆመ ፡ ለየብቻው ፡ መብላትና ፡ መጠጣት ፡ ነው ።

ቢፌውም ፡ ከተበላና ፡ ከተጠጣ ፡ በኋላ ፡ ሁሉም ፡ በመካከለኛው ፡ በትልቁ ፡ አዳራሽ ፡ በተቀመጡ ፡ ጊዜ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ባለው ፡ ስፍራ ፡ ቆሜ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ያለውን ፡ ቃል ፡ በእንግሊዝ ፡ ቋንቋ ፡ አነበብሁላቸው ።

ወይዛዝርና ፡ ትልልቆች ፡ ሰዎች ፡ ሆይ ።

እኛ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መላክተኞች ፡ ዛሬ ፡ በመካከላችሁ ፡ እንድናመሽ ፡ ፈቅዳችሁ ፡ ስለ ፡ ጠራችሁን ፡ አመሰግናችኋለሁ ።

አሜሪካና ፡ ጃፓን ፡ ለኢትዮጵያ ፡ በጣም ፡ የራቁ ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ ምናልባት ፡ ከመካከላችሁ ፡ የኢትዮጵያን ፡ ታሪክና ፡ የክርስቲያን ፡ ሃይማኖቷን ፡ ነገር ፡ የማያውቁ ፡ ይኖራሉና ፡ አሁን ፡ በጭሩ ፡ አድርጌ ፡ ለማስረዳት ፡ የተመቸ ፡ ጊዜ ፡ በማግኘቴ ፡ ደስ ፡ ብሎኛል ።

የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ ከተመሠረተ ፡ አራት ፡ ሺ ፡ ዘመን ፡ ይሆናል ። ነገር ፡ ግን ፡ የመጀመሪያው ፡ ሺው ፡ ዓመት ፡ አንዱ ፡ ንጉሥ ፡ ተነሥቶ ፡ ከገዛ ፡ በኋላ ፡ ሌላው ፡ ንጉሥ ፡ እየተነሣ ፡ የፊተኛውን ፡ ዘር ፡ እያጠፋ ፡ የራሱን ፡ ዘር ፡ ለማቆም ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ሲዋጉ ፡ የኖሩበት፡ ዘመን ፡ ነውና ፡ የዚያን ፡ ታሪክ ፡ ለመናገር ፡ አያስፈልግም ።

ይህ ፡ የመጀመሪያው ፡ ሺህ ፡ ዓመት ፡ ካለፈ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ንግሥተ ፡ ሳባ ፡ የተባለችው ፡ ንግሥታችን ፡ በነገሠች ፡ ጊዜ፡ኢትዮጵያን ፡ በሙሉ ፡ ገዝታ ፡ ግዛቷን ፡ እስከ ፡ ዓረብና ፡ እስከ ፡ ግብጽ ፡ ወሰን ፡ እያሰፋች ፡ ስለሔደች ፡ ስሟ ፡ በዓለም ፡ የታወቀ ፡ ሆነ። ሳባም ፡ የተባለው፡በኢትዮጵያ፡ ሰሜን ፡ ያለው ፡ ዛሬ ፡ አክሱም ፡ የሚባለው ፡ ከተማዋ ፡ ነው ።

በእርስዋም ፡ ዘመን ፡ የኢትዮጵያ ፡ ነጋዴዎች ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እየተመላለሱ ፡ ይነግዱ ፡ ነበርና ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ንጉሥ ፡ ከሰሎሞን ፡ ጋራ ፡ መላላክ ፡ ስለ ፡ ጀመረች፡ጥበቡን፡ሁሉ ፡ ሰማችና ፡ በጆሮ ፡ ከመስማት ፡ ባይን ፡ ማየት ፡ ይሻላል ፡ ብላ ፡ ብዙ ፡ ገጸ ፡ በረከት ፡ ይዛ ፡ ወደ ፡

ኢየሩሳሌም ፡ ወረደች ። ሰሎሞንም ፡ ንግሥተ ፡ ሳባን ፡ ባያት ፡ ጊዜ በዚያ ፡ ዘመን ፡ የጐብዝናው ፡ ወራት ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ በሴቶች ፡ ፍትወት ፡ ልቡ ፡ ተበላሽቶ ፡ ነበርና ፡ ለዚሁ ፡ ፈቃድዋን ፡ ቢጠይቃት ፡ እስካሁን ፡ አገሬን ፡ የምገዛው ፡ በድንግልና ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ፈቃድህን ፡ ለመፈጸም ፡ አይሆንልኝም ፡ ብትለው ፡ ወንድ ፡ ነውና ፡ በኃይል ፡ አሸንፎ ፡ ስለ ፡ ተገናኛት ፡ ፀንሳ ፡ ወደ ፡ ሀገርዋ ፡ ተመለሰች ። ሳባም ፡ ወደ ፡ ሚባለው ፡ ከተማዋ ፡ ለመድረስ ፡ የስምንት ፡ ቀን ፡ መንገድ ፡ ሲቀራት ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ወለደችና ፡ ስሙን ፡ እምኔ ፡ መለክ ፡ (ምኒልክ)አለችው ። ትርጓሜውም ፡ የብልህ ፡ ልጅ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ምኒልክም ፡ ካደገ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወርዶ ፡ ከአባቱ ፡ ከሰሎሞን ፡ ጋራ ፡ ተዋውቆ ፡ ተመለሰ ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ እናቱ ፡ ንግሥተ ፡ ሳባ ፡ በሕይወቷ ፡ መንግሥቷን ፡ ሰጥታ ፡ በሙሉ ፡ ኢትዮጵያ ፡ አነገሠችው ።

ከዚያም ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ እስካሁን ፡ ድረስ ፡ የቀዳማዊ ፡ ምኒልክ ፡ ዘር ፡ ሳያቋርጥ ፡ መጥቶ ፡ አሁን ፡ በኢትዮጵያ ፡ የነገሡት ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ለቀዳማዊ ፡ ምኒልክ ፡ ፻፳፭ኛ ፡ ንጉሥ ፡ ናቸው ።

ነገር ፡ ግን ፡ የትውልድ ፡ ነገር ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ በቀጥታ ፡ በልጁ ፡ ይወርዳል ። አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ በወንድሙ ፤ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ በአኅቱ ፤ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ በወንድሙና ፡ በእህቱ ፤ በአኅቱና ፡ በአክስቱ ፡ ልጅ ፡ ይወርዳልና ፡ ይህን ፡ በመሰለው ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ አንድ ፡ ጊዜም ፡ ቢሆን ፡ ከቀዳማዊ ፡ ምኒልክ ፡ ዘር ፡ አላቋረጠም ። ለጊዜውም ፡ አንዳንድ ፡ ኃይለኛ ፡ ተነሥቶ ፡ በኃይል ፡ በነገሠ ፡ ጊዜ ፡ የነገሥታቱ ፡ ዘር ፡ ባንድ ፡ አውራጃ ፡ እየሆነ ፡ እየቆየ ፡ ጊዜ ፡ ሲመቸው ፡ ተመልሶ ፡ ባባቱ ፡ ዙፋን ፡ ይቀመጥ ፡ ነበር ። የነገሥታቱ ፡ ትውልድ ፡ የተመሠረተው ፡ በዚህ ፡ ዓይነት ፡ ነው ።

ስለ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ ክርስቲያንነት ።

ቀዳማዊ ፡ ምኒልክ ፡ ከአባቱ ፡ ከሰሎሞን ፡ ጋራ ፡ ለመተዋወቅ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወርዶ ፡ ሲመለስ ፡ የሊቀ ፡ ካህናቱ ፡ የሳዶቅ ፡ ልጅ ፡ አዛርያስ ፡ መጽሐፈ ፡ ኦሪት ፡ ይዞ ፡ ከብዙ ፡ ካህናት ፡ ጋራ ፡ ሆኖ ፡ ቀዳማዊ ፡ ምኒልክን ፡ ተከትሎ ፡ ወደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ መጥቶ ፡ ነበርና ፡ ሕዝቡ ፡ በመጽሐፈ ፡ ኦሪት ፡ እየተማሩ ፡ እውነተኛውን ፡ አምላክ ፡ ማምለክ ፡ ጀመሩ ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ፳፫ኛው ፡ ንጉሥ ፡ ባዝኬን ፡ የሚባለው ፡ በነገሠ ፡ በ፰ኛው ፡ ዓመት ፡ ጌታችን ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በቤተ ፡ ልሔም ፡ ተወለደ ። ጌታችንም ፡ እኛን ፡ ስለ ፡ ማዳን ፡ ሞቶና ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ከረገ ፡ በኋላ ፡ በ፩ኛው ፡ ዓመት ፡ ህንደኬ ፡ የተባለችው ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንግሥት ፡ በጋዛ ፡ ርስትዋ ፡ የሾመችው ፡ አንድ ፡ ጃንደረባ ፡ ነበርና ፡ እርሱ ፡ ለበዓል ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ሊሰግድ ፡ ወጥቶ ፡ በዓለ ፡ ፋሲካ ፡ ካለፈ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ጋዛ ፡ በሠረገላ ፡ ሆኖ ፡ ሲመለስ ፡ ከሰባቱ ፡ ዲያቆናት ፡ አንደኛው ፡ የሚሆን ፡ ፊልጶስ ፡ የሚባለው ፡ በመንገድ ፡ አግኝቶ ፡ በክርስቶስ ፡ አሳምኖ ፡ አጠመቀው ። ስለዚህ ፡ በዚያ ፡ ዘመን ፡ የክርስትና ፡ ወሬ ፡ በኢትዮጵያ ፡ ተሰምቶ ፡ ነበር ።

በኋላም ፡ በ፫ተኛው ፡ መቶ ፡ ዓመ ፡ ምሕ ፡ መጨረሻ ፡ ነግሦ ፡ የነበረው ፡ አብርሃ ፡ የሚባለው ፡ የክርስትናን ፡ ወሬ ፡ ስለ ፡ ሰማ ፡ ፍሬምናጦስ ፡ የሚባል ፡ የግሪክ ፡ አገር ፡ ተወላጅ ፡ ጸሐፊ ፡ ነበረውና ፡ እርሱን ፡ ወደ ፡ እስክንድርያ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ወደ ፡ ቅዱስ ፡ አትናቴዎስ ፡ ላከው ። አትናቴዎስም፡ፍሬምናጦስን ፡ ደግነትና ፡ አዋቂነት ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ አገሩንም ፡ ቋንቋውንም ፡ በማወቅ ፡ ካንተ ፡ የሚሻል ፡ የለም ፡ ብሎ ፡ ፍሬምናጦስን ፡ ጳጳስ ፡ አድርጎ ፡ ሾሞ ፡ ወደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ መለሰው ።

ፍሬምናጦስም ፡ ወደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ተመልሶ ፡ ከንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ጀምሮ ፡ መኳንንቱንና ፡ የቤተ ፡ መንግሥቱን ፡ ትልልቅ ፡ ሰዎች ፡ በክርስቶስ ፡ እያሳመነ ፡ አጠመቃቸው ። ስሙም ፡ ሰላማ ፡ ተባለ ። ትርጓሜውም ፡ የኢትዮጵያን ፡ ሕዝብ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋራ ፡ ያስታረቀ ፡ ሰላማዊ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ከዚያም ፡ ጀምሮ ፡ በየጊዜው ፡ አንዳንድ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አገር ፡ እየሔዱ ፤ ከውጭ ፡ አገርም ፡ አንዳንድ ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ እየመጡ ፡ የኢትዮጵያን ፡ ቋንቋ ፡ ግዕዝ ፡ የሚባለውን ፡ እየተማሩ ፡ የብሉይ ፡ ኪዳንና ፡ የሐዲስ ፡ ኪዳን ፡ መጻሕፍት ፡ በግዕዝ ፡ ቋንቋ ፡ እየተተረጐሙ ፡ ተጻፉ ። ይህም ፡ ግዕዝ ፡ የሚባለው ፡ ቋንቋ ፡ እንደ ፡ ላቲን ፡ (ሮማይስጥ) ቋንቋ ፡ ሆኖ ፡ እስካሁን ፡ በየቤተ ፡ ክርስቲያናችን ፡ የሚቀደስበትና ፡ የሚጸለይበት ፡ ነው ።

ከዚያም ፡ ወዲህ ፡ አንዳንድ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሰዎች ፤ የውጭ ፡ አገርም ፡ ሰዎች ፡ መጻሕፍተ ፡ ብሉይንና ፡ መጻሕፍተ ፡ ሐዲስን ፡ ባማርኛ ፡ ቋንቋ ፤ እየተረጐሙ ፡ ስለ ፡ አሳተሙ ፡ ዛሬ ፡ ብዙዎቹ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ ባማርኛ ፡ ቅዱስ ፡ መጽሐፍ ፡ ያነባሉ ።

በጠቅላላው ፡ የእኛ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሰዎች ፡ ከአባቶቻችን ፡ የቆየን ፡ ሃይማኖታችን ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ያለው ፡ ነው ።

፩ኛ ። ምስጢረ ፡ ሥላሴን ፡ እናምናለን ።

ምስጢረ ፡ ሥላሴ ፡ ማለት ፡ እግዚአብሔር ፡ በባሕርይ ፡ አንድ ፤ በአካላት ፡ ሶስት ፡ ነው ፡ ማለት ፡ ነው ። ይኸውም ፡ ባንድነቱ ፡ አምላክ ፤ በሶስትነቱ ፡ አብ ፤ ወልድ ፤ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ተብሎ ፡ ይጠራል ።

፪ኛ ። ምስጢረ ፡ ሥጋዌን ፡ እናምናለን ።

ምስጢረ ፡ ሥጋዌ ፡ ማለት ፡ ከሶስቱ ፡ አካላት ፡ አንዱ ፡ አካል ፡ ወልድ ፡ እኛን ፡ ሰዎችን ፡ ከፍዳ ፡ ከመርገም ፤ ከኵነኔ ፡ ለማዳን ፡ በኋለኛው ፡ ዘመን ፡ ሰው ፡ ሆኖ ፡ ከድንግል ፡ ማርያም ፡ መወለዱን ፡ መሞቱንና ፡ መነሣቱን ፤ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ማረጉንና ፡ ዓለሙን ፡ ለማሳለፍ ፡ ሁለተኛ ፡ ተመልሶ ፡ መምጣቱን ፡ ማመን ፡ ነው ።

፫ኛ ። ምስጢረ ፡ ጥምቀትን ፡ እናምናለን ።

ምስጢረ ፡ ጥምቀት ፡ ማለት ፡ ቄሱ ፡ በስመ ፡ አብ ፡ ወወልድ ፡ ወመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ብሎ ፡ ባጠመቀን ፡ ጊዜ ፡ ከፍዳ ፡ ከመርገም ፡ ከኃጢአት ፡ ንጹሐን ፡ ሆነን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ መባላችንን ፡ ማመን ፡ ነው ።

፬ኛ ። ምስጢረ ፡ ቍርባንን ፡ እናምናለን ።

ምስጢረ ፡ ቍርባን ፡ ማለት ፡ በቅዳሴ ፡ ጊዜ ፡ ቄሱ ፡ የሚባርከውን ፡ ኅብስቱን ፡ የክርስቶስ ፡ ሥጋ ፡ ነው ፤ ወይኑን ፡ የክርስቶስ ፡ ደም ፡ ነው ፡ ብለን ፡ ማመን ፡ ነው ።

፭ኛ ። ምስጢረ ፡ ትንሣኤ ፡ ሙታንን ፡ እናምናለን ።

ምስጢረ ፡ ትንሣኤ ፡ ሙታን ፡ ማለት ፡ ሰው ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ ፍሱ ፡ እንደ ፡ ሥራዋ ፡ መጠን ፡ እግዚአብሔር ፡ በወሰነላት ፡ ስፍራ ፡ ቆ ታ ፡ በኋላ ፡ በእለተ ፡ ምጽአት ፡ ከሥጋዋ ፡ ጋራ ፡ ተዋህዳ ፡ እን ገና ፡ አካል ፡ አግኝታ ፡ እንድትነሣ ፡ ማመን ፡ ነው ።

ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ መኖሩን ፡ እናምናለን ።

የኢትዮጵያ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ የተመሠረተችውና ፡ ጸንታ የችው ፡ ይህን ፡ በመሰለ ፡ ነገር ፡ መሆኑን ፡ ሳስረዳችሁ ፡ እጅግ ፡ ይለኛል ፡ ብዬ ፡ ንግግሩን ፡ ስጨርስ ፡ ሁሉም ፡ በደስታ ፡ አጨ

## ምዕራፍ ፡ ፳፱ ።

በታኅሣሥ ፡ ፲፩ ፡ ቀን ፡ ዋይስ ፡ አድሚራል ፡ ሳይዞ ፡ ሴኮንጂ ፡ የሚባለው ፡ ለመሰናበት ፡ እመጣለሁ ፡ ብሎ ፡ አስቀድሞ ፡ በስልክ ፡ አስታውቆኝ ፡ ነበርና ፡ ከጧቱ ፡ በ፰ ሰዓት ፡ የማዕርግ ፡ ልብሱን ፡ ለብሶ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ የሸለሙትን ፡ ኒሻን ፡ አድርጎ ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ኤፔርያል ፡ መጣ ።

ዋይስ ፡ አድሚራል ፡ ሴኮንጂ ፡ በሰኔ ፡ ወር ፡ በ፲፱፻፳፫ ፡ ዓ ፡ ም ፡ አዝሞና ፡ አጉሞ ፡ የሚባሉትን ፡ ሁለት ፡ ትልልቅ ፡ የጃፓንን ፡ የጦር ፡ መርከቦች ፡ ይዞ ፡ በህንድ ፡ ውቅያኖስና ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ ሲዛወር ፡ ጂቡቲ ፡ ይደርሳልና ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ አንድ ፡ ዋና ፡ የጦር ፡ አለቃ፡ ልከው ፡ የጦር ፡ መርከቦችን ፡ እንዲያሳዩለት ፡ የጃፓን ፡ መንግሥት ፡ ስለ፡ ለመነ ፡ ክቡር ፡ ደጃዝማች ፡ ደስታ ፡ ዳምጠው ፡ ወደ ፡ ጂቡቲ ፡ ወርደው፡ የጦር ፡ መርከቦችን ፡ አይተው ፡ ተመልሰው ፡ ነበር ።

አሁን ፡ ግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ ንጉሠ፡ነገሥት፡ መላክተኞች ፡ ሲልኩ ፡ ለመንግሥቱ ፡ ትልልቅ ፡ ሰዎች ፡ ኒሻን ፡ ሸልመው ፡ ነበርና ፡ ለዋይስ ፡ አድሚራል ፡ ሴኮንጂም ፡ የኢትዮጵያን፡የክብር ፡ ኮከብ፡ ኒሻን ፡ ባለ ፡ ኮርዶኑን ፡ ሸለሙት ። ስለዚህ ፡ እኛን ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱን ፡ መላክተኞች ፡ ለመሰናበት ፡ ሲመጣ ፡ ብዙ ፡ ታሪክ ፡ ያለው ፡ የቀድሞ ፡ ዘመን ፡ ጎራዴ ፡ ለመታሰቢያ ፡ ብሎ ፡ ሰጠኝ ። ጐራዴውንም ፡ ሲሰጠኝ ፡ የጦር ፡ መርከብ ፡ ፎቶግራፍ ፡ አንሺ ፡ ተከትሎት ፡ መጥቶ ፡ ነበርና ፡ ፎቶግራፍ ፡ እንዲአነሣ ፡ ስለ ፡ ጠየቀ ፡ ባንድነት ፡ ሆነን ፡ ተነሣን ።

ለልጅ ፡ ተፈራና ፡ ለልጅ ፡ አርአያ ፡ ላቶ ፡ ዳባም ፡ ጩቤ ፡ የሚመስሉ ፡ አጫጭር ፡ ጐራዴዎች ፡ ሰጣቸው ።

በዚሁም ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ማታ ፡ የጃፓን ፡ አገር ፡ ሀኪሞች ፡ ኤክስሬ ፡ አፓሬቱር ፡ በሚባል ፡ በኤሌክትሪክ ፡ ኃይል ፡ በሽተኞች፡የሚያክሙበትን ፡ ሆስፒታል ፡ ለማየት ፡ ሔድን ። ይህም ፡ ኤክስሬ ፡ የሚባለው ፡ የኤሌክትሪክ ፡ መኪና ፡ የሰውን ፡ አካል ፡ ሌላውንም ፡ ዕቃ ፡ ቢሆን ፡ አቅርበው ፡ ሲያሳዩት ፡ የውስጡን ፡ ገልጦ ፡ የሚያሳይ ፡ ነው ። ሰው ፡ ልብሱን ፡ እንደ ፡ ለበሰ ፡ ቢቀርብ ፡ የሆድ ፡ ዕቃው ፡ አንጀቱ ፡ ጉበቱ፡ ሳምባው ፡ በሙሉ ፡ ተገልጦ ፡ ይታያል ። ራሱንም ፡ ቢያቀርብ ፡ አንጎና ፡ አጥንቱ ፡ ሥሩ ፡ ተለይቶ ፡ ይታያል ። እጁንና ፡ እግሩንም ፡ ቢ



ዋይስ ፡ አድሚራል ፡ ሳይዞ ፡ ሴኮንጂ ፡ ለክቡር ፡ ብላቴን ፡ ጌታ ፡
ኅሩይ ፡ የቀድሞ ፡ ዘመን ፡ የጃፓን ፡ አገር ፡ ጐራዴ ፡ ሲሸልሙ ።

ያቀርብ ፡ ጅማቱና ፡ አጥንቱ ፤ የደም ፡ ሥሩ ፡ ተለይቶ ፡ ይታያል ። የገንዘብ ፡ መያዣ ፡ (በርሳ ፡)ቢያቀርብ ፡ በውስጡ ፡ ያለው ፡ ገንዘብ ፡ በ ውጭ ፡ ታይቶ ፡ ይቈጠራል ።

በዚህም ፡ መኪና ፡ ማናቸውንም ፡ ዓይነት ፡ በሽታ ፡ እየመረመሩ፡ በያይነቱ ፡ በማሞቅ ፡ በማሸት ፤ በማጠብ ፤ በመቁረጥ ፤ በመቅደድ ፤ ይ ህንም ፡ በመሰለው ፡ የሚሆነውን ፡ በሽተኛ ፡ ሁሉ ፡ መድኃኒት ፡ ሳያጠ ጡና ፡ ሳያቀምሱ ፡ በኤሌክትሪክ ፡ ኃይል ፡ ብቻ፡ እያከሙ ፡ ያድኑበታ ል ። ዲረክተሩም ፡ ይህን ፡ የመሰለው ፡ የኤሌክትሪክ ፡ ኃይል ፡ አዲስ፡ የወጣ ፡ ብልሃት ፡ ነውና ፡ ወደ ፡ ሀገራችሁ ፡ እንዲገባ ፡ ብታደርጉ፡ መ ልካም ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ነገረኝ ።

እኔም ፡ እንደዚህ ፡ የሚታከምበት ፡ አይደለም ፡ እንጂ ፡ በሽታውን፡ ብቻ ፡ ለመመርመሪያ ፡ ያህል ፡ ጃንሆይ ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ባቆ ሙት ፡ ቤተ ፡ ሣይዳ ፡ በሚባለው ፡ ሆስፒታል ፡ አለ ፡ ብዬ ፡ ነገርሁት ።

ይህንም ፡ የመሰለውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ባይን ፡ ከማየት ፡ በቀር ፡ እንደ ዚህ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ለመጻፍና ፡ ለማስረዳት ፡ አይቻልም ፡ እንጂ ፡ በዚሁ ፡ በኤሌክትሪክ ፡ ኃይል ፡ የሚያደርጉት ፡ የህክምና ፡ ሥራ ፡ ያየነው ፡ ብቻ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ነው ።

በዚሁም ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ማታ ፡ በቶኪዮ ፡ የሻይ ፡ ማኅበረተኞች ፡ የሚባሉት ፡ ትልልቅ ፡ ሰዎች ፡ ለሻይ ፡ ጊዜ ፡ ሔደን ፡ ወዲያው ፡ የመሰነ ባበቻ ፡ እራት ፡ እንድንጋበዝላቸው ፡ ጠርተውን ፡ ነበርና ፡ በ፲ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ወደዚያው ፡ ሔድን ።

የሻዩ ፡ አፈላልና ፡ አቀዳዱ ፡ የፍንጃሉም ፡ አያያዝ ፡ ሥርዓቱ ፡ እንደ ቀድሞ ፡ ዘመን ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡ አዲሱ ፡ ዘመን ፡ አይደለም ። የሚ ቀዳውም ፡ በእድሜ ፡ የሸመገለና ፡ በተለየ ፡ ለዚሁ ፡ ሥራ ፡ እውቀት ፡ ያለ ው ፡ ነው ። ለያንዳንዱ ፡ ሰዎች ፡ የምታድለው ፡ ግን ፡ ቆንጆ ፡ ልጃገረድ ፡ ተመርጣ ፡ ነው ። ፍንጃሉንም ፡ በሁለት ፡ እጅ ፡ ተቀብሎ ፡ በግራ ፡ እጅ ፡ በመዳፍ ፡ ላይ ፡ አድርጎ ፡ በቀኝ ፡ እጅ ፡ ደግፎ ፡ ይጠጣል ። አንዱ ፡ በጠጣ በት ፡ ፍንጃል ፡ ሳይታጠብ ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ እንዳይጠጣበት ፡ በጣም ፡ ይጠነ ቀቃሉ ።

እንደዚህም ፡ እያደረጉ ፡ ሻይ ፡ ሲጋብዙን ፡ ቆይተው ፡ ወደ ፡ እራት፡ መጋበዣው ፡ ቤት ፡ ወሰዱን ። ምግቡም ፡ ሁሉ ፡ የተሰናዳው ፡ እንደ ፡ ጃ ፓኖች ፡ ምግብ ፡ ስለሆነ ፡ አቀማመጡም ፡ በፍራሽ ፡ ላይ፡ነበር።እራትም፡

ሲጀመር ፡ የማኅበሩ ፡ ዲሬክተር ፡ ተነሥቶ ፡ ሻይ ፡ መጠጣት ፡ የተጀመረ ው ፡ አስቀድሞ ፡ በሺን ፡ አገር ፡ መሆኑንና ፡ የሚጠጣውም ፡ ለመድኃኒ ት ፡ እየተባለ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፤ በኋላ ፡ ግን ፡ መድኃኒት ፡ መባሉ ፡ ቀርቶ ፡ በ ልማድ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ መጠጣቱን ፡ አስቀድሞም ፡ የሚጠጣው ፡ እርጥ ቡ ፡ ቅጠል ፡ በሙቀጫ ፡ እየተወቀጠ ፡ ሲደርቅ ፡ እንደ ፡ ዱቄት ፡ እየ ተበጠበጠና ፡ እየተፈላ ፡ መሆኑን ፡ ከተናገረ ፡ በኋላ ፡ የሻይ ፡ መጠጣት ፡ ፍሬ ፡ ነገሩ ፡ ወዳጅና ፡ ወዳጅ ፡ ማገናኘቱ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ እውነተኛው ን ፡ ነገር ፡ ተናገረ ። ቀጥሎም ፡ በኢትዮጵያ ፡ ቡን ፡ እንጂ ፡ ሻይ ፡ የለ ም ፡ ሲሉ ፡ ሰምቻለሁና ፡ ከጃፓን ፡ አገር ፡ ብዙ ፡ የሻይ ፡ ንግድ ፡ እ ንዲሔድ ፡ ተስፋ ፡ አደርጋለሁ ፡ ብሎ ፡ ጨረሰ ።

እኔም ፡ ስለ ፡ መሰነባበቻ ፡ ሻይና ፡ እራት ፡ በመጋበዛቸው ፡ ካመሰ ገንሁ ፡ በኋላ ፡ በኢትዮጵያ ፡ ሻይ ፡ የለም ፡ ስለ ፡ ማለትዎ ፡ በቀድሞ ፡ ዘ መን ፡ በኢትዮጵያ ፡ ሻይ ፡ አለመኖሩ ፡ እርግጥ ፡ ነው ። አሁን ፡ ግን ፡ ከአራት ፡ ዓመት ፡ አስቀድሞ ፡ ግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ሻይ ፡ በኢትዮጵያ ፡ መሆኑን ፡ ለመፈተን ፡ ሲሉ ፡ ቡና ፡ በሚያበቅለው ፡ ከፋ ፡ በሚባለው ፡ አገር ፡ እንዲተከል ፡ ላንድ ፡ ሰው ፡ ፈ ቃድ ፡ ሰጥተው ፡ ነበርና ፡ ፫ ሺ ፡ እግር ፡ ያህል ፡ በቅሎ ፡ እጅግ ፡ ማለፊያ ፡ ሆኗል ። ቢሆንም ፡ ለ፲፫ ፡ ሚሊዮን ፡ ሕዝብ ፡ ፫ ሺ ፡ እግር ፡ ሻይ ፡ ይበቃዋ ል ፡ ለማለት ፡ አይቻልምና ፡ የሻይ ፡ ተክል ፡ ባገራችን ፡ እየሰፋ ፡ እስ ኪሔድ ፡ ድረስ ፡ ከጃፓን ፡ አገር ፡ የሻይ ፡ ንግድ ፡ ቢሔድ ፡ ሕዝባችን ፡ ደስ ፡ ሳይለው ፡ አይቀርም ።

ደግሞ ፡ የሻይ ፡ ፍሬ ፡ ነገሩ ፡ ወዳጅና ፡ ወዳጅ ፡ ማገናኘቱ ፡ ነው ፡ ስለ ፡ ማለትዎ ፡ በዚህ ፡ አሳብ ፡ እኔም ፡ ከእርሰዎ ፡ ጋራ ፡ ነኝ ።

ይልቁንም ፡ የዛሬው ፡ ሻይ ፡ ግብዣ ፡ ኢትዮጵያውያንንና ፡ ጃፓኖ ችን ፡ የሚያገናኝ ፡ በመሆኑ ፡ የተናገሩት ፡ ነገር ፡ እርግጥ ፡ ነው ፡ ለማ ለት ፡ እችላለሁ ፡ ብዬ ፡ መለስሁላቸው ። በዚሁም ፡ ግብዣ ፡ እስከ ፡ ፬ ሰዓት ፡ አምሽተን ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ኤምፔሪያል ፡ ተመለስን ።

---

## ምዕራፍ ፡ ፴ ።

ወደ ፡ ከጁንሻ ፡ ክለብና ፡ ወደ ፡ ኅበዛዝት ፡ ማኅበር ፡ ስለ ፡ መሔዳችን ።

በታኅሣሥ ፡ ፲፬ ቀን ፡ የከጁንሻ ፡ ክለብ ፡ ማኅበር ፡ በፎርሞሳ ፡ ደሴት ፡ አገረ፡ ገዥ ፡ አማካይነት ፡ ለምሳ ፡ ጋብዘውን ፡ ነበርና ፡ በ፮ሰዓት ፡ ወደ ፡ ክለቡ ፡ ሔድን ።

የዚህም ፡ የኮጇንሻ ፡ ክለብ ፡ ማኅበረተኞች ፡ ቊጥራቸው ፡ ፫፻ ፡ ነው ። ክለቡም ፡ ከቆመ ፡ ፶ዓመቱ ፡ ነው ። ለምሳም ፡ የተጋበዝንበት፡ ምክንያቱ፡እኔ፡የኢትዮጵያ፡ንጉሠ ፡ ነገሥት፡መላክተኛ ፡ ሆኜ ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ ስለ ፡ ሔድሁ፡ የክብር ፡ ማኅበረተኛ፡ሆኜ፡ እንድቆጠርላቸው፡ አስቀድመው ፡ ለምነውኝ ፡ እሺ ፡ ብያቸው ፡ ነበርና ፡ ማኅበሩን ፡ ሰብ ስበው ፡ ለማስተዋወቅ ፡ ነው ።

በዚህም ፡ ቀን ፡ ከማኅበረተኞቹ ፡ ወገን ፡ የተሰበሰቡት ፡ መቶ ፡ ያ ህል ፡ ነበሩ ። በደረስንም ፡ ጊዜ ፡ ፕሬዚዳኑ ፡ ዋና ፡ ዋናዎቹን ፡ እያቀ ረበ ፡ አስተዋወቀኝ ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ መብል ፡ ቤት ፡ ገባንና ፡ የማኅበሩ ፡ ዲሬክተር ፡ ተነሥቶ ፡ ብላቴን ፡ ጌታ ፡ ኅሩይ ፡ ምንም ፡ በ ጃፓን ፡ አገር ፡ ነዋሪ ፡ ባይሆኑ ፡ የኢትዮጵያና ፡ የጃፓን ፡ ሕዝብ ፡ ለ መቃረባችን ፡ ምልክት ፡ እንዲሆኑ ፡ የክብር ፡ ማኅበረተኛ ፡ አድርገን ፡ መርጠናቸዋልና ፡ እንድታውቋቸው ፡ ይሁን ፡ ብሎ፡ ተናግሮ ፡ ወዲያው ፡ ዲፕሎሙን ፡ በፊታቸው ፡ ፈርሞ ፡ ሰጠኝ ።

እኔም ፡ በማኅበሩ ፡ ፊት ፡ ቆሜ ፡ ለዚህ ፡ ለትልቅ ፡ ክብር ፡ ስለመ ረጡኝ ፡ ምስጋናዬን ፡ አቀረብሁ ።

ከምግብም ፡ በኋላ ፡ የክለቡን ፡ ቤት ፡ በየክፍሉ ፡ እያገቡ ፡ አሳዩንና ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ኢምፔሪያል ፡ ተመለስን ።

በዚሁም ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ማታ ፡ በ፲ሰዓት ፡ የጃፓን ፡ ጎበዛዝት ፡ የ ሚማሩበትን ፡ ቤት ፡ እንድናይ ፡ ዲሬክተሩ ፡ አስታውቆን ፡ ነበርና ፡ ወደዚያ ፡ ሔድን ።

ስሙም ፡ ዋይ ፡ ኤም ፡ ሲ ፡ ኢ ፡ ይባላል ። ትርጓሜውም ፡ የጎበዛ ዝት ፡ ክርስቲያኖች ፡ ሰዎች፡ማኅበር ፡ ማለት ፡ ነው ። ይህንም ፡ የትም ህርት ፡ ቤት ፡ ያቆሙት ፡ የአሜሪካ ፡ ማኅበር ፡ ናቸው ። ቊጥራቸውም ፡ ሶስት ፡ ሺ ፡ ይሆናል ። ከጃፓኖችም ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ወደዚሁ ፡ ማኅበ ር ፡ ገብተዋል ።

በዚህም ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ እድሜያቸው ፡ ከሕፃንነት ፡ ያለፈው፡ ጎበዛዝትና ፡ ሌላም ፡ የዘወትር፡ ሥራ ፡ ያለባቸው ፡ ሰዎች ፡ ሥራቸውን ፡ ሲሠሩ ፡ እየዋሉ ፡ ማታ ፡ ማታ ፡ እየተሰበሰቡ ፡ ይማራሉ ።

የትምህርቱም ፡ ዓይነት ፡ ጅምናስቲክ ፡ በያይነቱ ፡ የወሀ ፡ ዋና ፡ ቋንቋም ፡ ጽሕፈትም ፡ ሌላም ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ሁሉ ፡ ነው ።

ማኅበሩ ፡ በየወሩ ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ ገንዘብ ፡ እያዋጡ ፡ ይሰጣሉ ። ተማሪዎቹም ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ ገንዘብ ፡ ይከፍላሉ ። በዚህም ፡ አደራረግ ፡ አራት ፡ ጥቅም ፡ ይገኝበታል ።

፩ኛው ፡ ጥቅም ። ትምህርት ፡ የሚፈልግ ፡ ሰው ፡ ትልቅ ፡ ቢሆን ፡ ዘመንህ ፡ አልፏልና ፡ አትማርም ፡ ሳይባል ፡ ለመማር ፡ ይችላል ።

፪ኛው ፡ ጥቅም ። ገንዘብ ፡ የሚያገኝበትን ፡ ሌላውን ፡ ሥራውን ፡ ሲሠራ ፡ ውሎ፡ማታ ፡ ማታ ፡ እውቀት ፡ የሚያገኝበትን፡ትምህርት፡ይማራል።

፫ኛው ፡ ጥቅም ። ለትምህርት ፡ ቤቱ ፡ ብዙ ፡ ገንዘብ ፡ መክፈሉ ፡ ቀርቶ ፡ በጥቂት ፡ ገንዘብ ፡ ይማራል ።

፬ኛው ፡ ጥቅም ። የገንዘቡ ፡ አወጣጥ ፡ ሳይበዛ ፡ የሕዝቡ ፡ ጥቅምና ፡ ያገር ፡ ሥልጣኔ ፡ ይገኝበታል ። ስለዚህ ፡ በሀገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ ይህ ፡ አደራረግ ፡ ቢለመድ ፡ እጅግ ፡ መልካም ፡ ነው ።

በጭሩ ፡ ለማስረዳት ። ያገር ፡ ፍቅር ፡ ያላቸው ፡ መቶ ፡ ትልልቅ ፡ ሰዎች ፡ በየወሩ ፡ አምስት ፡ አምስት፡ብር፡እያወጡ ፡ ቢሰጡ ፡ ፭፻ብር ፡ ይሆናል ። ደግሞ ፡ መቶ ፡ ተማሪዎች ፡ በየወሩ ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ ብር ፡ ቢከፍሉ ፡ ፪፻ ፡ ብር ፡ ይሆናል ። በድምሩ ፡ ፯፻ብር ፡ መሆኑ ፡ ነው ። ሌላውን ፡ ሥራቸውን ፡ ሳይተዉ ፡ ማታ ፡ ማታ ፡ ብቻ ፡ ለማስተማር ፡ በሁለት ፡ መቶ ፡ ብር ፡ አራት ፡ አስተማሪዎች ፡ ለመቅጠርና ፡ በመቶ ፡ አምሳ ፡ ብር ፡ አንድ ፤ የትምህርት ፡ ቤት ፡ ለመከራየት ፡ ይቻላል ።

ከዚህም፡ የሚተርፈው ፡ ሶስት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ብር ፡ መጽሐፍና፡ ወረቀት ፤ ቀለምና ፡ እርሳስ ፤ ወረቀትና ፡ ደብተር ፡ ለመግዣ ፡ ይበቃልና ፡ በአዲስ ፡ አበባ ፡ ከተማችን ፡ በቶሎ ፡ እንዲጀመር ፡ ተስፋ ፡ አደርጋለሁ ።

የማኅበሩም ፡ ዲሬክተር ፡ ቤቱን ፡ ሁሉ ፡ በየክፍሉ ፡ እያዞረ ፡ ካሳየን ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ኤምፔሪያል ፡ ተመለስን ።

---

## እንበሶቻችን ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ ስለ ፡ መድረሳቸው ።

እንደ ፡ ዓለም ፡ ነገሥታት ፡ ደንብ ፡ ያንዱ ፡ አገር ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ሌላው ፡ አገር ፡ ንጉሥ ፡ መላክተኞች ፡ በሚልክበት ፡ ጊዜ ፡ በገሩ ፡ ውስጥ ፡ ከሚገኘው ፡ ዕቃ ፡ አንድ ፡ ዓይነት ፡ ገጸ ፡ በረከት፡ ጨምሮ፡ መላክ፡ ልማድ፡ ነውና ፡ ጃንሆይ ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ እኛን ፡ ልዩ ፡ መላክተኞች ፡

አድርገው ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ ሲልኩ ፡ ከሌላው ፡ ዕቃ ፡ በቀር ፡ ሁለት ፡ የአንበሶች ፡ ገጸ ፡ በረከት ፡ ይዘን ፡ እንድንሔድ ፡ አዘውን ፡ ነበር ።

ነገር ፡ ግን ፡ እኛ ፡ የተሳፈርንበት ፡ አንድሬሊበን ፡ የሚባለው ፡ መርከብ ፡ ከሰዎችና ፡ ከፖስታ ፡ በቀር ፡ የንግድ ፡ ዕቃና ፡ አራዊት ፡ የማይሳፈርበት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ጂቡቲ ፡ ያለው ፡ የቆንስላችን ፡ ጸሐፊ ፡ በንግድ ፡ ዕቃ ፡ መርከብ ፡ አሳፍሮ ፡ እንዲሰዳቸው ፡ ብለን ፡ ጂቡቲ ፡ ላይ ፡ ትተናቸው ፡ ሔደን ፡ ነበርና ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ ደርሰን ፡ አንድ ፡ ወር ፡ ያህል ፡ ከቆየን ፡ በኋላ ፡ አንበሶቹ ፡ ዮክሃማ ፡ በሚባለው ፡ የባሕር ፡ ወደብ ፡ ከተማ ፡ መድረሳቸው ፡ በተሰማ ፡ ጊዜ ፡ በንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ የግቢ ፡ ሚኒስቴር ፡ ትእዛዝ ፡ አንበሶቹን ፡ ወደ ፡ ቶኪዮ ፡ ወስደው ፡ በቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ቅጥር ፡ ግቢ ፡ በሰፊውና ፡ በገላጣው ፡ ስፍራ ፡ አኑረዋቸው ፡ ነበርና ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱና ፡ እቴጌይቱ ፤ ቢተ ፡ ዘመዶቻቸውና ፡ ባለሟሎቻቸው ፡ ሁሉ ፡ በደስታና ፡ በማድነቅ ፡ ካዩዋቸው ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ዙሎጅካል ፡ ጋርድን ፡ ሰደዱዋቸው ። ያዚህም ፡ ወሬ ፡ በጋዜጣ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ የከተማው ፡ ሕዝብ ፡ ትልቁም ፡ ትንሹም ፡ ወደዚያው ፡ እየሔደ ፡ ስምንት ፡ ቀን ፡ ያህል ፡ ሲያይ ፡ ሰነበተ ።

ዙሎጅካል ፡ ጋርድን ፡ ማለት ፡ የዱር ፡ አራዊትን ፤ የአየር ፡ አእዋፍን ፤ የምድር ፡ ተንቀሳቃሽን ፤ በያይነታቸው ፡ እየሰበሰቡና ፡ እያለመዱ ፡ የሚያኖሩበት ፡ ሥፍራ ፡ ነው ። ይህንም ፡ በማድረጋቸው ፡ ሶስት ፡ ጥቅም ፡ ይገኝበታል ።

፩ኛው ፡ ጥቅም ። ዓይን ፡ እለት ፡ እለት ፡ አዲስ ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ ሲያይ ፡ ይታደሳል ፡ ይባላልና ፡ ሽማግሌዎችና ፡ ባልቴቶች ፡ ሕፃናትም ፡ ወደ ዚያ ፡ ስፍራ ፡ እየሔዱ ፡ አራዊቱንና ፡ አእዋፉን ፡ ተንቀሳቃሹንም ፡ በማየት ፡ ደስ ፡ እያላቸው ፡ ሰውነታቸው ፡ ይታደሳል ።

፪ኛው ፡ ጥቅም ። ሕዝቡ ፡ በሀገራቸው ፡ ሆነው ፡ ከሌላው ፡ አገር ፡ የመጡትን ፡ አራዊትና ፡ አእዋፍ ፤ ተንቀሳቃሹንም ፡ በማየታቸው ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ። ይልቁንም ፡ አንበሳ ፤ ነብር ፤ ዳልጋ ፡ አንበሳ ፤ ድብ ፤ ጅብ ፡ ይህን ፡ የመሰለውን ፡ ክፉ ፡ አርዌ ፡ ከሀገራቸው ፡ አጥፍተውታልና ፡ የኋላ ፡ ትውልድ ፡ አንበሳ ፡ ነብር ፤ ዳልጋ ፡ አንበሳ ፤ ድብ ፤ ጅብ ፡ የሚባለው ፡ እንዴት ፡ ያለ ፡ ይሆን ፡ እንዳይል ፡ እየሔደ ፡ እነዚህን ፡ ለማዶቹን ፡ ያያል ።

፫ኛው ፡ ጥቅም ። እነዚህን ፡ ለማዶች ፡ አራዊትና ፡ አእዋፍ ፡ የምድር ፡ ተንቀሳቃሽ ፡ ለማየት ፡ የሚሔድ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡

ዋጋ ፡ ይከፍላልና ፡ ትርፍ ገንዘብ ፡ እንኳ ፡ ቢቀር ፡ ለአራዊቱ ፡ ምግብና ፡ ለጠባቂዎቹ ፡ ቀለብ ፡ ሳይበቃ ፤ አይቀርም ።

በዚህም ፡ ስፍራ ፡ ያየናቸው ፡ ከያገሩ ፡ የመጡ ፡ አራዊትና ፡ አእዋፍ ፤ ተንቀሳቃሽም ፡ ዓይነታቸውና ፡ ቊጥራቸው ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ነው ።

እኛም ፡ እነዚህኑ ፡ ለማዶች ፡ አራዊት ፡ ለማየት ፡ ሔደን ፡ ሳለን ፡ ከጠባቂዎቹ ፡ አንዱ ፡ ወደ ፡ እኛ ፡ መጥቶ ፡ ከሀገራችሁ ፡ ከኢትዮጵያ ፡ የመጡት ፡ አንበሶች ፡ ያሉበትን ፡ ላሳያችሁ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ስፍራው ፡ ወሰደን ።

ወንዱ ፡ አንበሳ ፡ ወደ ፡ ማደሪያው ፡ ዋሻ ፡ ውስጥ ፡ ገብቶ ፡ ነበር ። ሴቲቱ ፡ አንበሳ ፡ ግን ፡ በደጃፉ ፡ ላይ ፡ ተኝታ ፡ ነበር ። በዋነኛው ፡ በር ፡ ላይ ፡ ግርማዊ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ለግርማዊ ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የላኩላቸው ፡ አንበሶች ፡ የሚል ፡ በጃፓንና ፡ በፈረንሳዊ ፡ ቋንቋ ፡ በጉልህ ፡ ተጽፎ ፡ ይታያል ።

ደግሞ ፡ ከአዲስ ፡ አበባ ፡ ጀምሮ ፡ በመሬትም ፡ በባሕርም ፡ የሔዱበት ፡ መንገድ ፡ ከርታው ፡ ተስሎ ፡ ባጠገቡ ፡ ተሰቅሏል ።

ይህንም ፡ ሁሉ ፡ ካየን ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ተመለስን ።

በዚህም ፡ ቀን ፡ በቶኪዮ ፡ ዩንቢርስቲ ፡ ያሉት ፡ ፲፫ሺ ፡ የሚያህሉ ፡ ተማሪዎች ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ጨዋታ ፡ ለማሳየት ፡ ወደ ፡ ዩንቢርስቲው ፡ ቢጠሩን ፡ በሥራ ፡ ብዛት ፡ ሰዓቱ ፡ የማያደርሰን ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ለመሔድና ፡ ለማየት ፡ አለመቻላችንን ፡ አስታውቀናቸው ፡ ነበርና ፡ ዋና ፡ ዋኖቹ ፡ ብቻ ፡ ስማቸውን ፡ ባንድ ፡ ደብተር ፡ ውስጥ ፡ ፈርመው ፡ አገርዎ ፡ ሲገቡ ፡ ለመታሰቢያ ፡ ይሁንዎ ፡ ብለው ፡ አምሳ ፡ የሚያህሉ ፡ ተማሪዎች ፡ ተመርጠው ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ድረስ ፡ መጥተው ፡ አጭር ፡ ዲስኩር ፡ ተናግረው ፡ ስማቸው ፡ የተፈረመበትን ፡ ደብተር ፡ በእጄ ፡ ሰጥተውኝ ፡ ተመለሱ ።

## ስድስተኛ ፡ ትልቅ ፡ ክፍል ።

የጃፓን ፡ አገር ፡ የመሬት ፡ ስጉድ ። የነገሥታቱ ፡ ትውልድ ። የነገሥታቱ ፡ ክብር ። የነገሥታቱ ፡ በግልጥ ፡ መታየት ። ነገሥታቱ ፡ በውጭ ፡ አገር ፡ ቋንቋ ፡ አለመናገር ። የነገሥታቱ ፡ ግብዣ ። የነገሥታቱ ፡ ልዩ ፡ ግብዣ ። የጃፓን ፡ አገር ፡ በዓላት ።

### ምዕራፍ ፡ ፴፩ ።

እጅግ ፡ ከፍ ፡ ካሉት ፡ ገዥዎቹ ፡ ከኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ተልኬ ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ የሔድሁበትን ፡ ጉዳይ ፡ ከጨረስሁ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሀገሬ ፡ ወደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ለመመለስ ፡ ቁርጥ ፡ አሳብ ፡ ስለ ፡ አደረግሁ ፡ በኮቤ ፡ ወደ ፡ አለው ፡ ወደ ፡ ማሳጂረ ፡ ማረቲም ፡ ኩምፓኒያ ፡ ተላልኬ ፡ ወደ ፡ ጂቡቲ ፡ ለመሔድ ፡ በታኅሣሥ ፡ ፲፰ ቀን ፡ የሚነሣ ፡ እስፊንክስ ፡ የሚባል ፡ መርከብ ፡ መኖሩን ፡ ባስታወቀኝ ፡ ጊዜ ፡ ለራሴ ፡ መታሰቢያ ፡ ወደ ፡ ጃፓንም ፡ አገር ፡ ለሚሔዱ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሰዎች ፡ መሪ ፡ እንዲሆን ፡ ብዬ ፡ ከሀገሩ ፡ አኳኋንና ፤ ከነገሥታቱ፡ጥንታዊነት ፤ ከሕዝቡም ፡ ልማድና ፡ ሥልጣኔ ፡ ያየሁትንና፡የሰማሁትን ፤ በብዙ ፡ ሳይሆን፡ በጥቂቱ ። በረጅሙ ፡ ሳይሆን ፡ ባጭሩ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ለመጻፍ ፡ አሰብሁ ።

### ስለ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ የመሬት ፡ ስጉድ ።

የጃፓን ፡ አገር ፡ ቀስት ፡ መስሎ ፡ ከምሥራቅ ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ምዕራብ፡ በቀጭኑ ፡ የተዘረጋና ፡ የተከፋፈለ ፡ ደሴት ፡ ነው ።

አሁን ፡ እኛ ፡ እየዞርን ፡ ያየናቸው ፡ አውራጆች ፡ ሁሉ ፡ የሚበዙት ፡ ተራራሞች ፡ ናቸው ። በየተራሮቹም ፡ ሴደር ፡ (ቄድሮስ ፡ ) የሚባለው ፡ ዛፍና ፡ ሌላም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ዛፎች ፡ በብዙ ፡ ይታያሉ ። ስለ ፡ ተራሮችም ፡ ብዛት ፡ ትልልቆች ፡ ወንዞች ፡ ሞልተዋል ። ስለዚህም ፡ በየዞብጡ ፡ መሬት ፡ ሩዝ ፡ ለመዝራትና ፡ ለምግብ ፡ የሚሆኑ ፡ አትክልቶች ፡ ለመትከል ፡ ይመቻቸዋል ።

አሁን ፡ እኛ ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ በደረስንበት ፡ ወራት ፡ የሩዝ ፡ አጨዳ ፡ ነበር ። ስለ ፡ መሬቱም ፡ እርጥባምነት ፡ የታጨደው ፡ ሩዝ ፡ እንዳይበሰብስ ፡ በየነዶው ፡ እያሠሩ ፡ ረጃጅም ፡ እንጨት ፡ በባላ ፡ እያጋደሙ ፡ እንደ ፡ ሥጋ ፡ ቋንጣ፡ ይሰቅሉታል ፡ እንጂ፡በመሬት ፡ ላይ ፡ አይከምሩትም ።

አንዳንዱም ፡ በገመድ ፡ እያሠሩ ፡ በየዛፉ ‥ ላይ ፡ ያንጠለጥሉታል ፡ እኛ ፡ በዘርንበት ፡ በጃፓን ፡ ምዕራብና ፡ ደቡብ ፡ በግና ፡ ፍየል ፡ ሌላም ፡ የቀንድ ፡ ከብት ፡ በዱር ፡ ተሰማርቶ ፡ የሚበላ ፡ አላየንም ። ምናልባት ፡ እነዚህን ፡ የመሰሉት ፡ እንስሶች ፡ የሚረቡት ፡ በጃፓን ፡ ምሥራቅና ፡ ሰሜን ፡ ይሆናል ፡ እንጂ ፡ ባገሩ ፡ ወ ስጥ ፡ በግና፡የቀንድ ፡ ፡ ከብት ፡ የለም፡ ለማለት ፡ አይቻልም ።

## ስለ ፡ ጃፓን፡ነገሥታት ፡ አጭር ፡ ታሪክ ።

የጃፓን ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ በጣም ፡ የሚያስደንቅ ፡ ነው ።

ከጌታችን ፡ ከክርስቶስ ፡ ልደት ፡ አስቀድሞ ፡ በ፮፻፷ ፡ ዓመት ፡ መጀመሪያ ፡ በጃፓን ፡ የነገሠው ፡ ጂሙ ፡ ቴኖ ፡ ይባል ፡ ነበር ። ቴኖ ፡ ማለት ፡ በቋንቋቸው ፡ ንጉሠ፡ነገሥት ፡ ማለት ፡ ነው ። ከእርሱ ፡ አስቀድሞ ፡ የነበሩትን ፡ የነገሥታቱን ፡ ስም ፡ ሲጠይቋቸው ፡ አማልክት ፡ ይገዙን ፡ ነበር ፡ ይላሉ ። ትርጓሜው ፡ ግን ፡ ታሪኩ ፡ አልተገኘም ፡ አልታወቀም ፡ ማለት ፡ ይመስላል ።

የጂሙ ፡ ቴኖ ፡ ዘር ፡ ከወዴት ፡ የመጣ ፡ ነው ፡ ሲሏቸው ፡ ለፀሐይ፡ አማቴራሱ ፡ የተባለች ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ነበረቻትና ፡ ከአማቴራሱ ፡ ዘር ፡ የመጣ ፡ ሰባተኛ ፡ ትውልድ ፡ ነው ። ፀሐይም ፡ አምላክ ፡ ናትና ፡ ነገሥታቶቻችን ፡ የአምላክ ፡ ልጆች ፡ ስለ ፡ መሆናቸውና ፡ ሰውነታቸው ፡ የተቀደሰ ፡ ስለ ፡ መሆኑ ፡ እንሰግድላቸዋለን ፡ ይላሉ ፡ (ምናልባት ፡ ይህች ፡ አማቴራሱ ፡ ያሏት ፡ እኛ ፡ ሔዋን ፡ የምንላትን ፡ ይሆናል።)

ይህም ፡ ልማድ ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ ብቻ ፡ አይደለም ።ነገር ፡ ግን ፡ በቀድሞ ፡ ዘመን፡ በምሥራቅ ፡ አገር ፡ በባቢሎንና ፡ በፋርስ ፡ በከላውዴዎንም ፡ በህንድም ፡ በሽንም ፡ የነበሩ ፡ ሰዎች ፡ የፈጠራቸውን ፡ አምላክ ፡ ባይናቸው ፡ ካለማየታቸው ፡ የተነሣ ፡ እየተቸገሩ ፡ ከፍጥረቱ ፡ ሁሉ፡ የሚበልጥ ፡ ፀሐይ ፡ መሆኑን ፡ እያዩ ፡ አምላካችን ፡ ፀሐይ ፡ ነው ፡ እያሉ ፡ ለፀሐይ ፡ ይሰግዱ ፡ ነበር ። ይኸውም ፡ በአብርሃም ፡ አባቶች ፡ በነታራ ፡ ይታወቃል ። ምንም ፡ እንኳ ፡ በብሉይ ፡ ኪዳን ፡ ተጽፎ ፡ ባናገኘው ፡ ካባቶቻትን ፡ ቃል ፡ ለቃል ፡ ተያይዘልን ፡ እንደመጣው ፡ ታሪክ ፡ አብርሃም ፡ እንደ ፡ አባቶቹ ፡ በፀሐይ ፡ ለማምለክ ፡ ሕሊናው ፡ እምቢ ፡ ቢለው ፡ አምላክ ፡ ፀሐይ ፡ ተናበበኒ ፡ አለ ፡ ይባላል ።

የጃፓንም ፡ የቀድሞ ፡ ነገሥታት ፡ የፀሐይ ፡ ልጆች ፡ ነን ፡ እስከ ፡ ማለት ፡ የደረሱበት ፡ እንደዚሁ ፡ ፈጣሪያቸው ፡ ያለበትን ፡ መርምረው ፡ ለማወቅ ፡ ስለ ፡ ቸገራቸው ፡ ይመስላል ። ደግሞም ፡ ፀሐይን ፡ አምላክ ፡ ማለታቸው ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ አዳም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ተብ ሏልና ፡ መጀመሪያው ፡ ንጉሣችን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ነበር ፡ ቢሉ ፡ ከስሕተት ፡ አይቆጠርባቸውም ፡ ነበር ። ሉቃ ፡ ፫ ፡ ፴፰ ።

እንግዴህ ፡ በማናቸውም ፡ ወገን ፡ ቢሆን ፡ የጃፓን ፡ ነገሥታት ፡ ስምና ፡ ቍጥር ፡ ከታሪከ ፡ ነገሥታቸው ፡ ያገኘሁት ፡ ከዚህ ፡ የሚከተለው ፡ ነው ።

### የጃፓን ፡ ነገሥታት ።

፩ ጂሙ ፤
፪ ሱዋዚይ ፤
፫ አኒይ ፤
፬ ኢቶኩ ፤
፭ ኮሾ ፤
፮ ኮዋን ፤
፯ ኮሬይ ፤
፰ ኮጂን ፤
፱ ካይኳ ፤
፲ ሱጂን ፤
፲፩ ሱዊኒን ፤
፲፪ ካይኮ ፤
፲፫ ሳይሙ ፤
፲፬ ቹዋይ ፤
፲፭ ጂንጎ ፡ (በእንደራሴነት ፡)
፲፮ ኦጂን ፤
፲፯ ኒንቶኩ ፤
፲፰ ሪቹ ፤
፲፱ ሆንዚይ ፤
፳ ኢንክዮ ፤
፳፩ አንኮ ፤
፳፪ ዩሪያኩ ፤

### የጃፓን ፡ ነገሥታት ።

፳፫ ሴይኔይ ፤
፳፬ ኪንዞ ፤
፳፭ ኒንኪን ፤
፳፮ ማሬትሱ ፤
፳፯ ካይታይ ፤
፳፰ አንካን ፤
፳፱ ሲንኳ ፤
፴ ኪሜይ ፤
፴፩ ቢዳትሱ ፤
፴፪ ዩሜይ ፤
፴፫ ሱጁን ።
፴፬ ሱይኮ(ንግሥት)
፴፭ ጆሜይ ።
፴፮ ኮክዩኩ(ንግሥት)
፴፯ ኮቶኩ ።
፴፰ ሳይሜይ ።
፴፱ ቲንቺ ።
፵ ኮቡን ።
፵፩ ቴሙ ።
፵፪ ጂቶ(ንግሥት)
፵፫ ሞሙ ።
፵፬ ጌምዩ(ንግሥት) ።

## የጃፓን ፡ ነገሥታት ።

፺፭ ጌንሾ(ንግሥት)
፺፮ ሾሙ ።
፺፯ ኮኪን(ንግሥት)
፺፰ ጁኒን ።
፺፱ ኮኪን(ታደሰላት)
፻ ኮኒን ።
፻፩ ከዋሙ ።
፻፪ ሄይጆ ።
፻፫ ሣጋ ።
፻፬ ኒና ።
፻፭ ኒምዮ ።
፻፮ ሞንቶኩ ።
፻፯ ሲይዋ ።
፻፰ የዚይ ።
፻፱ ኮኮ ።
፻፲ ኡዳ ።
፻፲፩ ዳይጎ ።
፻፲፪ ሱጃኩ ።
፻፲፫ ሙራጋሚ ።
፻፲፬ ሬይዜይ ።
፻፲፭ ኢንዩ ፤
፻፲፮ ኳዛን ፤
፻፲፯ ኢችዮ ፤
፻፲፰ ሳንጆ ፤
፻፲፱ ጎ—ኢቺጆ ፤
፻፳ ጎ—ሹጃኩ ፤
፻፳፩ ጎ—ሬያዜይ ፤
፻፳፪ ጎ—ሳንጆ ፤
፻፳፫ ሺራካዋ ፤
፻፳፬ ሆሮካዋ ፤
፻፳፭ ቶባ ፤

## የጃፓን ፡ ነገሥታት ።

፻፳፮ ሹቶኩ ፤
፻፳፯ ኮኖዬ ፤
፻፳፰ ጎ ፡ ሺራካዋ ፤
፻፳፱ ኒጆ
፻፴ ሮኩጆ ፤
፻፴፩ ታካኩራ ፤
፻፴፪ አንቶኩ ፤
፻፴፫ ጎ ፡ ቶባ ፤
፻፴፬ ትሱቺ ፡ ሚካዶ ፤
፻፴፭ ጁንቶኩ ፤
፻፴፮ ቹክዮ ፤
፻፴፯ ጎ—ሆሪካዋ ፤
፻፴፰ ዮጆ ፤
፻፴፱ ጎ ፡ ሣጋ ፤
፻፵ ጎ ፡ ፉካኩስ ፤
፻፵፩ ካሚያማ ፤
፻፵፪ ጎ—ኡዳ ፤
፻፵፫ ፉሺሚ ፤
፻፵፬ ጎ—ፉሺሚ ፤
፻፵፭ ጎ ፡ ኒጆዮ ፤
፻፵፮ ሆኖዘኖ ፤
፻፵፯ ጎ ፡ ዳይጎ ፤
፻፵፰ ጎ ፡ ሙራካሚ ።
፻፵፱ ጎ ፡ ካማያማ ፤
፻፶ ጎ ፡ ካማትሱ ።
፻፶፩ ሾኮ ።
፻፶፪ ጎ ፡ ሀናዘኖ ።
፻፶፫ ጎ ፡ ትሱቺ ፡ ሚካዶ ።
፻፶፬ ጎ ፡ ካሺዋበራ ።
፻፶፭ ጎ ፡ ናራ ።
፻፶፮ ኦጊማቺ ።

| የጃፓን ፡ ነገሥታት ። | |
|---|---|
| ፻ ፯ | ጎ ፡ ዮጆ ። |
| ፻ ፰ | ጎ ፡ ሚዙኦ ። |
| ፻ ፱ | መዩሾ ፡ (ንግሥት ፡) |
| ፻፲ | ጎ ፡ ኮመዩ ። |
| ፻፲፩ | ጎ ፡ ኒሺዩ ። |
| ፻፲፪ | ሬይጂን ። |
| ፻፲፫ | ሂጋሺያማ ። |
| ፻፲፬ | ናካ ፡ ሚካዶ ። |
| ፻፲፭ | ሳኩራማቺ ። |

| የጃፓን ፡ ነገሥታት ። | |
|---|---|
| ፻፲፮ | ሞሞዞኖ ። |
| ፻፲፯ | ጎ ፡ ሳኩራማቺ ። (ንግሥት) |
| ፻፲፰ | ጎ ፡ ሞሞዞኖ ። |
| ፻፲፱ | ኮኩ ። |
| ፻፳ | ኒንኮ ። |
| ፻፳፩ | ኮሜይ ። |
| ፻፳፪ | ሚጂ ። |
| ፻፳፫ | ቴይሾ ። |
| ፻፳፬ | ሒሮሂቶ፡ያሁኑ፡ን፡ንጉሥ፡ |

በ፰፻፶፩(፰፻፶፰)ዓ ፡ ም ፡ ነግሦ ፡ የነበረው ፡ ሞንቶኩ ፡ ኮሬሽቶና ፡ ኮሬታካ ፡ የሚባሉ ፡ ሁለት ፡ ልጆች ፡ ነበሩትና ፡ እርሱ ፡ ሲሞት ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ ነግሠው ፡ ሁለቱም ፡ በኃይል ፡ እየተዋጉ ፡ ፲ ዓመት ፡ ያህል ፡ ከቆዩ ፡ በኋላ ፡ ኮሬሽቶ ፡ ድል ፡ አድርጎ ፡ ሲያዋ ፡ ተብሎ ፡ ብቻውን ፡ ነግሦ ፡ ገዝቷል ። ይኸውም ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ አብርሃና ፡ አጽብሐ ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ ነግሠው ፡ እንደ ፡ ነበሩ ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ አብርሃና ፡ አጽብሐ ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ የነገሡት ፡ በፍቅርና ፡ በመስማማት ፡ ነበረ ፡ እንጂ ፡ እንደነዚያ ፡ በ ጠብ ፡ አልነበረምና ፡ ልዩነቱ ፡ በዚህ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

እንግዲህ ፡ እነዚህን ፡ ሁለቱን ፡ ወንድማማቾች ፡ ለየብቻ ፡ የቈጠርና ቸው ፡ እንደሆነ ፡ የዛሬው ፡ ንጉሥ ፡ ግርማዊ ፡ ሒሮሂቶ ፡ ፻፳፬ኛ ፡ ይ ሆናሉ ። አንድ ፡ አድርገን ፡ የቈጠርናቸው ፡ እንደሆነ ፡ ግን ፡ ፻፳፫ኛ ፡ ይ ሆናሉ ። ስለ ፡ ሆነም ፡ አሁን ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ የነገሥታቱ ፡ ትውልድ ፡ በኦፊሴል ፡ ሲቈጠር ፡ የዛሬው ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ፻፳፬ኛ ፡ እየተባሉ ፡ ነ ውና ፡ ይህንኑ ፡ መከተል ፡ ይገባናል ።

ግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሒሮሂቶ ፡ በማዚያ ፡ ፳፪ ፡ በ፲፰፻፺፫ (ማ ዚያ ፡ ፳፱ ፡ ፲፱፻፩ )ዓመ ፡ ምሕ ፡ ተወለዱ ። ባመቱ ፡ የጃፓን ፡ መንግሥት ፡ አልጋ ፡ ወራሽ ፡ መሆናቸው ፡ ታወጀላቸው ። ከ፲፭ ፡ ዓመታቸው ፡ እ ስከ ፡ ፳፭ ፡ ዓመታቸው ፡ የወታደርነት ፡ ትምሕርት ፡ እየተማሩ ፡ ስለ ፡ አ ደጉ ፡ ሌፍትናንት ፤ ኮሎኒል ፤ ኮማንደር ፤ ካፒቴን ፡ የሚባለውን ፡ የወ ታደር ፡ አለቃነት ፡ ሹመት ፡ በየደረጃው ፡ ተሾሙ ።

በ፲፱፻፲፫ ፡ (በ፲፱፻፳፩)ዓመ ፡ ምሕ ፡ አውሮጳን ፡ ጎበኙ። በዚሁም ፡ ዓመት ፡ አባታቸው ፡ ግርማዊ ፡ ቴይሹ ፡ ስለ ፡ ታመመ ፡ የጃፓን ፡ መንግሥት ፡ ባለሙሉ ፡ ሥልጣን ፡ እንደራሴ ፡ ሆኑ ። በጥር ፡ ፲፱ ፡ ፲፱፻፲፰ ፡ (፲፱፻፳፮)የፕረንስ ፡ ኩኒን ፡ ልጅ ፡ ፕሪንሲስ ፡ ናጋኮ ፡ ኩኒን ፡ አገቡ ።

በታኅሣሥ ፡ ፲፱ ፡ ፲፱፻፳ ፡ (፲፱፻፳፯)ዓመ ፡ ምሕ ፡ አባታቸው ፡ ስለ ፡ አረፉ ፡ በንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ዙፋን ፡ ተቀምጠው ፡ ባመቱ ፡ በኅዳር ፡ ወር ፡ በ፲፱፻፳፩ ፡ (፲፱፻፳፰)ዓመ ፡ ምሕ ፡ በኪዮቶ ፡ ከተማ ፡ ሥርዓተ ፡ ንግሥ ፡ አደረሱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፪ ።

## ስለ ፡ ጃፓን ፡ ነገሥታት ፡ ክብር ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ ነገሥታቱ ፡ የፀሐይ ፡ ልጆች ፡ ናቸው ፡ እየተባሉ ፡ በታላቅ ፡ ክብር ፡ እየተከበሩ ፡ ይሰገድላቸዋል ።

ከቀድሞ ፡ ካባቶቻቸው ፡ ጀምሮ ፡ እንደ ፡ ዘውድ ፡ እየተወራረሰ ፡ የመጣላቸው ፡ ያልማዝ ፡ ቀለበታቸውና ፡ ሰይፋቸው ፡ መስተዋታቸውም ፡ እንደ ፡ ንዋየ ፡ ቅድሳት ፡ ይቆጠራል ። የሰውነታቸውም ፡ መከበር ፡ ይቅርና ፡ ፎቶግራፋቸው ፡ በታየ ፡ ጊዜ ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ይሰግዳሉ ።

ስለ ፡ ክብሩም ፡ ማንም ፡ ቢሆን ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱን ፡ ፎተግራፍ ፡ ደፍሮ ፡ በቤቱ ፡ የሚሰቅል ፡ አይገኝም ። ለየትልልቅ ፡ ሰዎችም ፡ እንደ ፡ መታሰቢያ ፡ ሆኖ ፡ የተሰጠ ፡ እንደሆነ ፡ በትልቅ ፡ የብረት ፡ ሣጥን ፡ ውስጥ ፡ እያገቡ ፡ ቆልፈው ፡ ያስቀምጡታል ። አንዳንዱም ፡ ሽራይን ፡ እየሠሩ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱን ፡ ፎቶግራፍ ፡ በዚያ ፡ እያኖሩ ፡ ይሰግዱበታል ።

በውጭ ፡ አገርም ፡ ለተሾሙት ፡ የጃፓን ፡ አምባሳደሮችና ፡ ሚኒስትሮች ፡ የተሰጠ ፡ እንደሆነ ፡ ነፋስ ፡ እንዳይነፍስበት ፡ ትቢያ ፡ እንዳይበንበት ፡ የእሳትም ፡ አደጋ ፡ እንዳያገኘው ፡ እየተባለ ፡ በብረት ፡ ሣጥን ፡ ውስጥ ፡ ይቀመጣል ፡ እንጂ ፡ በሌጋሲዮኑ ፡ አይሰቀልም ።

ያለፈቃድም ፡ ፎቶግራፉን ፡ ኮፒ ፡ ለማንሳት ፡ አይቻልም ። ይህም ፡ በእኔ ፡ በራሴ ፡ ደርሶብኛል ። የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መላክተኛ ፡ ስለ ፡ መሆኔ ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥትና ፡ እቴጌይቱ ፡ ፎተግራፋቸውን ፡ እየፈረሙ ፡ ሰጥተውኝ ፡ ነበርና ፡ ያገሩን ፡ ሕግ ፡ ሳላውቅ ፡ ወደ ፡ አንድ ፡ ሠራተኛ ፡ ወስጄ ፡ ይኸን ፡ ፎቶግራፍ ፡ ኮፒ ፡ አንሥተህ ፡ በመጽሐፍ ፡ የሚገባ ፡ ክሊሼ ፡ ሥራልኝ ፡ ብለው ፡ ፎቶግራፉን ፡ ተቀብሎ ፡ አይቶ ፡ የተቀደ

ሰውን ፡ የንጉሣችንን ፡ ፎተግራፍ ፡ ክልሼ ፡ ለመሥራት ፡ ከግርማዊነታቸ ቸው ፡ ልዩ ፡ ፈቃድ ፡ ካላገኘሁ ፡ አይሆንልኝም ፡ ብሎ ፡ ፎተግራፉን ፡ መ ልሶ ፡ ሰጠኝ ።

## በግልጥ ፡ ስለመታየት ።

የጃፓን ፡ ነገሥታት ፡ እንደ ፡ ሕጋቸው ፡ በከተማ ፡ ዑደት ፡ የሚደረግ በት ፡ ትልልቅ ፡ በዓል ፡ ለማክበርና ፡ የወታደር ፡ ሠልፍ ፡ ለማየት ፡ ካል ሆነ ፡ በቀር ፡ በማናቸውም ፡ ጊዜ ፡ ቢሆን ፡ በግልጥ ፡ ለመታየት ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አይወጡም ። ባለ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስትሮችና ፡ መኳንንቶች ፤ ያገር ፡ ባላባቶችና ፡ የካህናት ፡ አለቆች ፡ ግን ፡ ቀጠሮ ፡ እየጠየቁ ፡ በተፈቀደላቸ ው ፡ ቀንና ፡ ሰዓት ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ እየገቡ ፡ እጅ ፡ ለመንሣትና ፡ ለመነጋገር ፡ ይችላሉ ።

## በውጭ ፡ አገር ፡ ቋንቋ ፡ ስለ ፡ አለ ፡ መናገር ።

የዛሬው ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የእንግሊዝና ፡ የፈረንሣዊ ፡ ቋንቋ ፡ ያውቃሉ ። ነገር ፡ ግን ፡ የኦፊሴል ፡ ጉዳይ ፡ የሆነውን ፡ ሁሉ ፡ በስተርጓ ሚያቸው ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ አውቃለሁ ፡ ብለው ፡ በውጭ ፡ አገር ፡ ቋ ንቋ ፡ አያነጋግሩም ። ይኸውም ፡ የጃፓንን ፡ ቋንቋ ፡ ለማስከበር ፡ የተ ደረገ ፡ ይመስላል ።

## ስለ ፡ ነገሥታቱ ፡ ግብዣ ።

የጃፓን ፡ ነገሥታት ፡ ባመት ፡ አራት ፡ ጊዜ ፡ ትልልቅ ፡ ግብር ፡ እያደረጉ ፡ ያገር ፡ ሚኒስትሮችንና ፡ ትልልቆችን ፡ ባላባቶች ፤ ሰዎች ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ አምባሳደሮችንና ፡ ሚኒስትሮችን ፡ የሁሉም ፡ ቍጥራቸው ፡ እ ስከ ፡ አንድ ፡ ሺ ፡ ድረስ ፡ የሆነ ፡ ይጋብዛሉ ። ግብዣውም ፡ እንደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ ልማድ ፡ የተዘጋጀ ፡ ምግብና ፡ ሳኬ ፡ የሚባለው ፡ መጠ ጥ ፡ ብቻ ፡ ነው ። ያውም ፡ እንደ ፡ ቀድሞው ፡ ልማዳቸው ፡ ምግቡ ፡ በሁለት ፡ እንጨት ፡ እየተያዘ ፤ ሳኬውም ፡ በትንንሽ ፡ ነጭ ፡ ሲኒ ፡ እ የተቀዳ ፡ ነው ። የግብሩም ፡ አቀራረብ ፡ እንግዶቹ ፡ ሁሉ ፡ በተጠሩበ ት ፡ ሰዓት ፡ እየመጡ ፡ ባዳራሹ ፡ ከገቡ ፡ በኋላ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ መጥተው ፡ ወደ ፡ አዳራሹ ፡ ሲገቡ ፡ ሁሉም ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ ባንገት ፡

ይሰግዳሉ ። ንጉሠ ፡ ነገሥቱም ፡ በቀጥታ ፡ ወደ ፡ ግብር ፡ መብሊያው ፡ ሔደው ፡ ለብቻቸው ፡ ባንድ ፡ ገበታ ፡ ላይ ፡ ይቀመጣሉ ። በስተ ፡ ቀኝ ፡ ባለው ፡ አውራጃ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፤ በስተግራ ፡ ባለው ፡ አውራጃ ፡ ያገር ፡ ውስጥ ፡ ሰዎች ፤ ይቀመጣሉ ። የግብዣው ፡ ሰዓት ፡ ምንም ፡ ቢበዛ ፡ ከ፵ ደቂቃ ፡ አያልፍም ። ከ፵ ደቂቃ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ተነሥተው ፡ ወደ ፡ እልፍኛቸው ፡ ሲሔዱ ፡ እንግዶቹ ፡ በማረፊያው ፡ አዳራሽ ፡ ፲ ደቂቃ ፡ ያህል ፡ ቆይተው ፡ ሁሉም ፡ በየቤታቸው ፡ ይሔዳሉ ። ሳኬ ፡ የጠጡበትንም ፡ የሚያምረውን ፡ ነጩን ፡ ሲኒ ፡ እንደ ፡ መታሰቢያ ፡ እየሆነ ፡ ለሁሉም ፡ ይመረቅላቸውና ፡ በየቤታቸው ፡ ይወስዱታል ። ከምግቡም ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ በመሀርማቸው ፡ እየቋጠሩ ፡ ወደ ፡ ቤታቸው ፡ ወስደው ፡ እንደ ፡ በረከት ፡ ለቤተ ፡ ዘመዶቻቸው ፡ ያቀምሷቸዋል ።

---

## ስለ ፡ ነገሥታቱ ፡ ልዩ ፡ ግብዣ ።

ከውጭ ፡ አገር ፡ ልዩ ፡ መላክተኛ ፡ የመጣ ፡ እንደሆነ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱና ፡ እቴጌይቱ ፡ ቤተ ፡ ዘመዶቻቸውንና ፡ የሚገባቸውን ፡ አንዳንድ ፡ ያገር ፡ ሚኒስትሮች ፡ ጨምረው ፡ ባንድ ፡ ገበታ ፡ ተቀምጠው ፡ ልዩ ፡ መላክተኛውን ፡ ይጋብዛሉ ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ግብዣው ፡ ሁሉ ፡ ምግቡም ፡ መጠጡም ፡ ሹካውም ፡ ማንካውም ፡ ቢለዋውም ፡ ሰሐኑም ፡ የሚቀርበው ፡ እንደ ፡ አውሮፓ ፡ ነገሥታት ፡ ሥርዓት ፡ ነው ።

ለእኔም ፡ የተደረገልኝ ፡ ግብዣ ፡ በዚሁ ፡ ዓይነት ፡ ነው ።

---

## ምዕራፍ ፡ ፴፫ ።

## ስለ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ በዓላት ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ በያውራጃው ፡ የሚከበረው ፡ በዓል ፡ ብዙ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ በገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ የገብርኤል ፤ የራጉኤል ፤ የጊዮርጊስ ፤ የተክለ ፡ ሃይማኖት ፤ የገብረ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፤ ታቦት ፡ ባለበት ፡ አገር ፡ በየሰበካው ፡ በየወሩ ፡ እንደሚከበረው ፡ ነው ።

አሁን ፡ የምጽፈው ፡ ግን ፡ በመላው ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ የሚከበረውን ፡ ትልልቁን ፡ በዓላት ፡ ብቻ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ መስቀል ፤ ልደት ፤ ጥምቀት ፤ ፋሲካ ፡ እንደሚባለው ፡ ነው ።

ጥር ፡ ፩ ቀን ። የዘመን ፡ መለወጫ ፡ በዓላቸው ፡ ነው ።

በዚህም ፡ ቀን ፡ የቤተ ፡ መንግሥትና ፡ የቤተ ፡ ክህነት ፡ ትልልቅ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ እየመጡ ፡ እንኳን ፡ ከዚህ ፡ ዘመን ፡ አደረሰዎ ፡ እያሉ ፡ መልካም ፡ ምኞታቸውን ፡ ያቀርባሉ ። ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ በየወዳጁና ፡ በየዘመዱ ፡ ቤት ፡ እየሔደ ፡ እንኳን ፡ ከዚህ ፡ ዘመን ፡ አደረሰህ ፡ ይባባላል ። ይኸውም ፡ በጥር ፡ ወር ፡ የተደረገው ፡ የዘመን ፡ መለወጫ ፡ በዓል ፡ ከአውሮጶች ፡ የተበደሩቱ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የጥንታቸው ፡ አይደለም ።

በዚሁ ፡ ወር ፡ በ፭ኛው ፡ ቀን ፡ ስለ ፡ አዲሱ ፡ ዘመን ፡ በዓል ፡ ተብሎ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ለቤተ ፡ ዘመዶቻቸውና ፡ ለመንግሥቱ ፡ ሚኒስቴሮች ፡ ላገሩ ፡ ባላባቶችና ፡ ለውጭ ፡ አገር ፡ ዲፕሎማቲኮች ፡ በቤተ ፡ መንግሥት ፡ ራት ፡ ይጋብዛሉ ።

የካቲት ፡ ፫ ቀን ። የክረምት ፡ ማጋመሻ ፡ በዓል ፡ ይባላል ።

በዚህም ፡ በዓል ፡ ቤተ ፡ ዘመዱ ፡ ሁሉ ፡ በየቤቱ ፡ እየተሰበሰበ ፡ ቆሎ ፡ እየተቆላ ፡ ቆሎውን ፡ እየዘገነ ፡ ሰይጣንና ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ውጣ ፡ እያለ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ይበትናል ፤ ሲሳይና ፡ ጤና ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ ግባ ፡ እያለ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ይበትናል ፤ የተረፈውንም ፡ ይበሉታል ። ይኸውም ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ በየባላገሩ ፡ ለእንቁጣጣሽና ፡ ለግንቦት ፡ ልደታ ፡ እንደሚደረገው ፡ ነው ።

የካቲት ፡ ፲፩ ፡ ቀን ። ጂሙ ፡ የሚባለው ፡ የጃፓን ፡ መጀመሪያው ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ የነገሠበት ፡ ቀን ፡ ነው ። ይህም ፡ በዓል ፡ በቤተ ፡ መንግሥቱና ፡ በየመቅደሱ ፡ በየባላገሩም ፡ ይከበራል ። በዚሁም ፡ ቀን ፡ ንጉሠ፡ ነገሥቱ ፡ ለቤተ ፡ ዘመዶቻቸውና ፡ ለሚኒስትሮቹ ፡ ላገሩም ፡ ባላባቶችና ፡ ለውጭ ፡ አገር ፡ ዲፕሎማቲኮች ፡ በቤተ ፡ መንግሥት ፡ ራት ፡ ይጋብዛሉ ።

መጋቢት ፡ ፫ ፡ ቀን ። ያሻንጉሊት ፡ በዓል ፡ የሚባለውን ፡ ያከብራሉ ።

በዚህም ፡ ቀን ፡ ከነገሥታቱ ፡ ልጆች ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሕዝቡ ፡ ድረስ ፡ ያሉት ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ዋጋው ፡ ውድ ፡ የሆነ ፡ አሻንጉሊት ፡ እየገዙ ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥቱና ፡ ለእቴጌይቱ ፡ ለሚኒስትሮችና ፡ ለመኳንንቶች ፡ ለየትልልቁም ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እየወሰዱ ፡ ይሰጣሉ ። ይኸውም ፡ እየተሰበሰበ ፡ እንደ ፡ አንቲካ ፡ በክብር ፡ እየሆነ ፡ ይቀመጣል ። ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ለእንቁጣጣሽ ፡ እንግጫ ፤ ለመስቀል ፡ አበባ ፡ እየወሰዱ ፡ ለየትልልቁ ፡ ሰው ፡ እንደሚሰጡት ፡ ነው ።

መጋቢት ፡ ፳፩ ፡ ቀን ። ከጂሙ ፡ ጀምሮ ፡ ለሞቱት ፡ ነገሥታትና፡ እቴጌዎች ፡ የመታሰቢያ ፡ በዓል ፡ (ተዝካር፡ ) የሚደረግበት ፡ ቀን ፡ ነው ።

በዓሉም ፡ በንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ቤተ ፡ መንግሥትና ፡ በየትልልቁ ፡ ሽራይን ፡ እየተሰገደላቸው ፡ ይከበራል ። ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ ተዝካረ፡ ነገሥት ፡ እንደሚባለው ፡ ነው ።

ሚያዝያ ፡ ፫ቀን ። የጃፓን ፡ የመጀመሪያው ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ጂሙ ፡ የሞተበት ፡ በዓል ፡ ነውና ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ በሙሉ ፡ ይከበራል ።

ሚያዝያ ፡ ፰ቀን ። በጃፓን ፡ አገር ፡ መጀመሪያ ፡ የቡዳሃን ፡ ሃይማኖት ፡ ያገባ ፡ ሳኪያሙን ፡ የተወለደበት ፡ ቀን ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ የቡዳሃ ፡ መቅደስ ፡ ባለበት ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ይከበራል ።

ሚያዝያ ፡ ፳፱ቀን ። የዛሬው ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ግርማዊ ፡ ሒሮሂቶ ፡ የተወለዱበት ፡ ቀን ፡ ነው ። በዚህም ፡ ቀን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ በቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ አጠገብ ፡ ወደ ፡ አለው ፡ ወደ ፡ ዮዮጊ ፡ ከ፭ሰዓት ፡ በፊት፡ሔደው፡ የወታደር ፡ ሰልፍ ፡ ያያሉ፤ ማታም ፡ ቤተ ፡ ዘመዶቻቸውንና ፡ ሚኒስትሮችን ፡ ያገር ፡ ባላባቶችንና ፡ የውጭ ፡ አገርም ፡ ዲፕሎማቲኮችን ፡ በቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ራት ፡ ይጋብዛሉ ።

ግንቦት ፡ ፭ቀን ። የባንዲራ ፡ በዓል ፡ ይባላል ። ይኸውም ፡ በሙሉ ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ ይከበራል ። በዚህም ፡ ቀን ፡ ወንዶች ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ የልብስ ፡ ያላገኙም ፡የወረቀት፡ ባንዲራ ፡ እያበጁ ፡ ይይዛሉ ፤ የወረቀት ፡ ባሎንም ፡ እያበጁ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ይወረውራሉ ። ደግሞ ፡ ካንዱ ፡ ቤት፡ ወዳንዱ ፡ ቤት ፡ ገመድ ፡ እየተዘረጋ ፡ የወረቀት ፡ ባንዲራ ፡ ይደረደራል ። ይኸውም ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ በየቆላው ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ወንዶች ፡ ልጆች ፡ የማሽላ ፡ አገዳ ፡ (አሜራ)እየላጡ ፡ በክር ፡ እየሰኩ ፡ አላማ ፡ እያሉ ፡ ለከተራ ፡ ታቦት ፡ ሲወጣ ፡ እየያዙ ፡ ወደ ፡ ጥምቀተ ፡ ባሕር ፡ እየወረዱ ፡ በማግሥቱ ፡ ታቦት ፡ ሲመለስ ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እንደሚያኖሩት ፡ ነው ።

ሰኔ ፡ ፲፯ ፡ ቀን ። የጃፓን ፡ ነገሥታት ፡ እናት ፡ የፀሐይ ፡ ልጅ ፡ የምትባለው ፡ የያማቴራሱ ፡ ነፍስ ፡ የምትገለጽበት ፡ የኢሴ ፡ መቅደስ ፡ በዓል ፡ ነው ።

ሐምሌ ፡ ፩ቀን ። የፉጂያማ ፡ ተራራ ፡ በታምራት ፡ ከምድር ፡ ተወርውሮ ፡ የወጣበት ፡ ነው ፡ እያሉ ፡ የሚያከብሩበት ፡ ነው ።

ሐምሌ ፡ ፲፫ቀን ። የሰው ፡ ሁሉ ፡ የሞቱት ፡ ዘመዶች ፡ ነፍሳት ፡ መታሰቢያ ፡ በዓል ፡ ነው ። በዚሁም ፡ ቀን ፡ የሞቱት ፡ መቃብራቸውንና ፡ የድሮ ፡ ቤታቸውን ፡ ይጎበኛሉ ፡ ይባላልና ፡ ሕያዋኑ ፡ ዘመዶቻቸው ፡ የመቃብሩን ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ ንጹሕ ፡ ያደርጋሉ ። ቤታቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ያስጌጣሉ ። ድግስም ፡ እየተደገሰ ፡ በየመቅደሱ ፡ ይላካል ፤ ካህናቱም ፡ ጸሎት ፡ ያደርጋሉ ፤ በየደጃቸውም ፡ ላይ ፡ ነፍሳትን ፡ ለመቀበል ፡ የጪስ ፡ እንጨት ፡ ያጨሳሉ ። ይኸውም ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ ክብረ ፡ ቅዱሳን ፤ ተዝካረ ፡ ሙታን ፡ እንደሚባለው ፡ ነው ።

ሐምሌ ፡ ፴ ቀን ። የጃፓንን ፡ ሕዝብ ፡ ያሠለጠነና ፡ ጃፓንን ፡ ወደ ፡ ትልቅ ፡ ደረጃ ፡ ያደረሰ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሜጂ ፡ የሞተበት ፡ በዓል ፡ ነው ።

ኅዳር ፡ ፫ ቀን ። ትልቁ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሜጂ ፡ የተወለደበት ፡ ቀን ፡ ነው ። ይኸውም ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ በሙሉ ፡ ይከበራል ። በዚሁም ፡ ቀን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ለቤተ ፡ ዘመዶቻቸውና ፡ ለመንግሥቱ ፡ ሚኒስትሮች ፡ ላገሩ ፡ ባላባቶችና ፡ ለውጭ ፡ አገር ፡ ዲፕሎማቲኮች ፡ በቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ እራት ፡ ይጋብዛሉ ። ካህናቱም ፡ በሜጂ ፡ ሽራይን ፡ ትልቅ ፡ በዓል ፡ ያደርጋሉ ።

ኅዳር ፡ ፲፭ ቀን ። እድሜያቸው ፡ እስከ ፡ ፭ ዓመት ፡ የሆነ ፡ ወንዶች ፡ ልጆችና ፡ እድሜያቸው ፡ እስከ ፡ ፯ ዓመት ፡ የሆነ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ከሞግዚቶቻቸውና ፡ ወይም ፡ ከአስተማሪዎቻቸው ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ሽንቶ ፡ ሽራይን ፡ እየሄዱ ፡ እድሜያቸውን ፡ እንዲያረዝምላቸው ፤ ከክፉ ፡ ነገርም ፡ እንዲጠብቃቸው ፤ ዘመናቸውንም ፡ የጤናና ፡ የደስታ ፡ ዘመን ፡ እንዲያደርግላቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚለምኑበት ፡ የሕፃናት ፡ በዓል ፡ ነው ።

ኅዳር ፡ ፳፫ ቀን ። የሩዝ ፡ መከር ፡ በዓል ፡ ነው ። በዚህም ፡ ቀን ፤ ከሩዙ ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ እየያዙ ፡ ወደ ፡ ሽራይን ፡ እየሄዱ ፡ እንደ ፡ መሥዋዕት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚያቀርቡበት ፡ ቀን ፡ ነው ። በቤተ ፡ መንግሥቱም ፡ ከዲሱ ፡ ሩዝ ፡ የሚቀመሰው ፡ በዚሁ ፡ ቀን ፡ ነው ። ይኸውም ፡ በብሉይ ፡ ኪዳን ፡ በበዓለ ፡ ሠዊት ፡ እስራኤል ፡ ከመጀመሪያ ፡ እህላቸው ፡ አንዳንድ ፡ ጎሞር ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሥዋዕት ፡ እያሉ ፡ እንደሚያቀርቡት ፡ ነው ።

ታኅሣሥ ፡ ፳፭ ቀን ። የዛሬው ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ አባት ፡ ግርማዊ ፡ ቴይሾ ፡ የሞተበት ፡ ቀን ፡ ነው ። ይኸውም ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ በሙሉ ፡ ይከበራል ።

የጃፓን ፡ መንግሥትና ፡ የሕዝቡ ፡ በዓል ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ የተጻፈው ፡ ነው ።

በተረፈ ፡ በሽንቶ ፡ ሽራይንም ፡ በቡድሃ ፡ መቅደስም ፡ አንዳንድ ፡ የቅዱሳኖቻቸው ፡ በዓላት ፡ ይከበራሉ ። ይኸውም ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡

ታቦት ፡ በተተከለበት ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ የታቦቱን ፡ በዓል ፡ መላው ፡ የኢት ዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ ሳይሆኑ ፡ የሰበካው ፡ ሕዝብ ፡ ብቻ ፡ እንደሚያከብሩት ፡ ነው ።

ከዚህም ፡ በቀር ፡ የጃፓን ፡ ሕዝብ ፡ ምንም ፡ ሁሉም ፡ በክርስቶስ ፡ ባያ ምኑ ፡ ያዲሱን ፡ ዘመን ፡ ሥልጣኔ ፡ ለመከተል ፡ ሲሉ ፡ በክርስቶስ ፡ እንዳ መኑት ፡ እንደ ፡ ኢትዮጵያና ፡ እንደ ፡ ሌሎችም ፡ አገሮች ፡ ሕዝብ ፡ እሁድን ፡ በየሳምንቱ ፤ ልደትን ፡ በያመቱ ፡ ያከብራሉ ። ይኸንኑም ፡ የልደትን ፡ አከ ባበር ፡ ጊዜ ፡ ስላጋጠመኝ ፡ ባይኔ ፡ አይቻለሁ ።

በቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ ሳለሁ ፡ እንደ ፡ አውሮፓ ፡ ባሕረ ፡ ሐሣብ ፡ የልደት ፡ በዓል ፡ በታኅሣሥ ፡ ፳፭ ቀን ፡ ውሎ ፡ ነበርና ፡ የቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ ለበዓሉ ፡ ስምንት ፡ ቀን ፡ ሲቀረው ፡ ጀምራ ፡ በባንዲራና ፡ በሌላም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ጌጥ ፡ አጊጣ ፡ ነበር ። የጌጡም ፡ ዓይነት ፡ እንደ ፡ ከተማው ፡ ክፍል ፡ እየሆነ ፡ በየመንገዱ ፡ ዳር ፡ አንዱ ፡ ክፍል ፡ በአረንጓዴ ፡ ቀለም ፡ ጌጥ ፤ ደግሞ ፡ አንዱ ፡ ክፍል ፡ በቀይ ፡ ቀለም ፡ ጌጥ ፤ ደግሞ ፡ አንዱ ፡ ክፍል ፡ በተቀላቀለ ፡ ቀለም ፡ ጌጥ ፡ ተጌጦ ፡ ነበር ። በዚህም ፡ ላይ ፡ ከልብስ ፡ የተሠራ ፡ አርቲፊሴል ፡ አበባ ፡ ከሰበካው ፡ አርማ ፡ ጋራ ፡ በየቤቱ ፡ በርና ፡ በረንዳ ፡ እየተሰቀለ ፡ ይታይ ፡ ነበር ።

ይህም ፡ አደራረግ ፡ ወደፊት ፡ የጃፓን ፡ ሕዝብ ፡ በሙሉ ፡ በክርስቶስ ፡ እንዲያምኑ ፡ እንደ ፡ ትንቢት ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ይመስላል ።

## ሰባተኛ ፡ ትልቅ ፡ ክፍል ።

## ስለ ፡ ጃፓኖች ፡ ሥራና ፡ ኑሮ ።



ስለ፡ወንዶችና፡ስለ ፡ ሴቶች ፡ ልብስ ፡ አለባበስ፤ስለ ፡ ጠጉር ፡ አሠራር ፤ ስለ ፡ ፊት ፡ ማሳመር ፤ ስለ ፡ መልክና ፡ ቁመት ፤ ስለ ፡ ባርኔጣና ፡ ስለ ፡ ጫማ ፡ ማድረግ ፤ ስለ ፡ መብልና ፡ ስለ ፡ መጠጥ ፤ ስለ ፡ መከባበር ፤ ስለ ፡ እንግዳ ፡ አቀባበል ፤ ስለ ፡ ቤት ፡ አሠራር ፤ ስለ ፡ ፋብሪካ ፤ ስለ ፡ ትምሕርት ፤ ስለ ፡ መንገድ ፤ ስለ ፡ ኤሌክትሪክ ፡ መብራት ፤ ስለ ፡ ሥራ ፡ መውደድ ፤ ስለ ፡ ሥራ ፡ ሰዓት ፤ ስለ ፡ አመልና ፡ ጠባይ ፤ ስለ ፡ ጉብዝናቸው ፤ ስለ ፡ ጋብቻ ፤ ስለ ፡ ፍቺ ፤ ስለ ፡ ሞት ፡ ሰው ፡ አቀባበር ።

### ምዕራፍ ፡ ፴፬ ።

### ስለ ፡ ወንዶች ፡ ልብስ ፡ አለባበስ ።



በጃፓን ፡ አገር ፡ ወንዶቹ ፡ ሰዎች ፡ ከውስጥ ፡ ልብስ ፡ በላይ ፡ እጀ ፡ ሰፊ ፡ ቀሚስ ፡ ይለብሳሉ ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ሴቶች ፡ ሽርጥ ፡ የሚመስል ፡ የተሸበሸበ ፡ ከወገባቸው ፡ እስከ ፡ እግራቸው ፡ አጥልቀው ፡ በመታጠቂያ ፡ ይታጠቃሉ ። በዚህም ፡ ላይ ፡ ከወደፊቱ ፡ ክፍት ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ እጀ ፡ ሰፊ ፡ ቀሚስ ፡ ይደርባሉ ። በደረታቸውም ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ምልክት ፡ የሚያንጠለጥሉት ፡ ባለቤቱ ፡ እንደ ፡ ፈቀደ ፡ ነጭም ፡ ጥቁርም ፡ ሌላም ፡ ዓይነት ፡ ቀለም ፡ የገባ ፡ የሐር ፡ ወይም ፡ የፈትል ፡ ገመድ ፡ በጫፉም ፡ ጎፍላ ፡ ያለበት ፡ ነው ።

በላይኛው ፡ ልብሳቸው ፡ ላይ ፡ ዘራቸውን ፡ የሚያስታውቅ ፡ ምልክት ፡ በትከሻና ፡ በተከሻው ፤ በደረቱና ፡ በደረቱ ፤ በኋላው ፤ በድምሩ ፡ በ፭ ላይ ፡ በነጭ ፡ ሐር ፡ ይጠልፉበታል ። ይህንም ፡ አይቶ ፡ እገሌ ፡ የእገሌ ፡ ወገን ፡ ነው ፡ ለማለት ፡ ይቻላል ።

ይህንም ፡ የመሰለው ፡ ነገር ፡ በያገሩ ፡ ይደረጋል ። በአውሮጳ ፡ የመጀመሪያው ፡ አባቱ ፡ የዘሩ ፡ ስም ፡ ፍላድ ፡ የሆነ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የርሱ ፡ ተወላጅ ፡ ሁሉ ፡ ከክርስትና ፡ ስሙ ፡ ጋራ ፡ ፍላድ ፡ እየተባለ ፡ ሲጠራ ፡ ይኖራል ።

በአርመኖችም ፡ እንደዚሁ ፡ የዘር ፡ ስም ፡ አላቸው ።

የዘራቸው ፡ ስም ፡ ባግደሣር ፡ ሲሆን ፡ ባግደሣሪያን ። ቦጎስ ፡ ሲሆን ፡ ቦጎስያን ። አሣዱር ፡ ሲሆን ፡ አሣዱርያን ። ሙራድ ፡ ሲሆን ፡ ሙራድያን ። ቴርዝ ፡ ሲሆን ፡ ቴርዝያን ፡ ይባላሉ ።

በዚህም ፡ ዓይነት ፡ የዘር ፡ መታወቂያ ፡ ምልክት ፡ ማድረግ ፡ እጅግ ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ ነውና ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያም ፡ እንዲለመድ ፡ ተስፋ ፡ እናደርጋለን ።

ምሳሌ ። በሞረት ፡ ከጥዱ ፡ የሚወለድ ፡ ጥዱያዊ ። በኩራ ፡ ከወልዱ ፡ የሚወለድ ፡ ወልዱያዊ ። በሞጃ ፡ ከቤዛ ፡ የሚወለድ ፡ ቤዛዊ ። በአፍቀራ ፡ ከጎሌ ፡ የሚወለድ ፡ ጎሌያዊ ። በጠል ፡ ከማደሬ ፡ የሚወለድ ፡ ማደሬያዊ ። በግሼ ፡ ከአውሳቤ ፡ የሚወለድ ፡ አውሳቤያዊ ። በደብብ ፡ ከጸጋ ፡ የሚ ወለድ ፡ ጸጋዊ ። በጎንደር ፡ ከፋሲል ፡ የሚወለድ ፡ ፋሲልያዊ ። በትግሬ ፡ ከሥዑል ፡ ሚካኤል ፡ የሚወለድ ፡ ሚካኤላዊ ። በዋግ ፡ ከዋግሹም ፡ የሚ ወለድ ፡ ዋግሹማዊ ።

በወላሞ ፡ ከጦና ፡ የሚወለድ ፡ ጦናዊ ። በወለጋ ፡ ከጆቴ ፡ የሚወለድ ፡ ጆቴያዊ ። በነቀምቴ ፡ ከሞረዳ ፡ የሚወለድ ፡ ሞረዳዊ ፡ ቢባል ፡ ለትውል ዱ ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ነው ።

ደግሞ ፡ በብርድ ፡ ወራትና ፡ በሌላም ፡ ቀን ፡ አንዳንዱ ፡ ከወደኋላ ፡ ቀሚስ ፡ ከወደ ፡ ፊት ፡ ግን ፡ አጭር ፡ ክብ ፡ ካባ ፡ የሚመስል ፡ ይደ ርባሉ ።

---

## ስለ ፡ ጦር ፡ ሠራዊት ፡ ልብስ ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ የጦር ፡ ሠራዊት ፡ ከጀኒራሉ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ተራ ው ፡ ወታደር ፡ እንደ ፡ ሠለጠነው ፡ እንደ ፡ እንግሊዝ ፡ የጦር ፡ ሠራዊት ፡ ልብስ ፡ ይለብሳሉ ። የቆባቸውም ፡ የጐራዴያቸውም ፡ ዓይነቱ ፡ እንደነዚያ ው ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ የጦር ፡ አለቆች ፡ በሰልፍ ፡ ቀን ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ የጦር ፡ አለቆች ፡ ለመሆናቸው ፡ ምልክት ፡ ብቻ ፡ ርዝመቱ ፡ አንድ ፡ ክን ድ ፡ የሚሆን ፡ አጭር ፡ ጐራዴ ፡ ይታጠቃሉ ፡ እንጂ ፡ ረጅሙን ፡ ጐራዴ ፡ ዘወትር ፡ አይታጠቁትም ።

---

## ስለ ፡ ሴቶች ፡ ልብስ ፡ አለባበስ ።

የጃፓን ፡ አገር ፡ ሴቶች ፡ ከውስጥ ፡ ልብሳቸው ፡ በላይ ፡ አንድ ፡ ረጅ ም ፡ ቀሚስ ፡ ለብሰው ፡ በዚያ ፡ ላይ ፡ ደግሞ ፡ አንድ ፡ ረጅም ፡ ቀሚስ ፡ ይ ደርባሉ ።

በሁለተኛውም፡ቀሚስ፡ላይ፡አቢ፡የሚባለውን፡የልብስ፡ጥቅል፡ያዝላሉ።

አቢ ፡ ማለት ፡ በያይነቱ ፡ ቀለም ፡ የገባ ፡ ፬ ፡ ማዕዘን ፡ የታጠፈ ፡ ልብስ ፡ ነው ። እንኳን ፡ ትልልቆቹ ፡ ሴቶች ፡ ከ፳ ዓመት ፡ በላይ ፡ ያሉ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ አቅማቸው፡ ትንንሽ፡አቢ ፡ እየተሠራላቸው፡ ያዝላሉ ።

ይህንም ፡ አቢ ፡ የሚባለውን ፡ የልብስ ፡ ጥቅል ፡ ሴቶች፡ በጀርባቸው፡ እንዲያዝሉ ፡ የተለመደበት ፡ ምክንያቱ ፡ በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ ወንዶች ፡ ስለ ፡ ቅንዓት ፡ የሴቶቻቸው ፡ ሽንጥና ፡ ወገብ ፡ ማማሩ ፡ እንዳይታይ ፡ ነበር፤ በኋላ ፡ ግን ፡ በዘመን ፡ ብዛት ፡ እየተለመደ፡እንደ፡ጌጥ፡ሆኖ፡ ቀረ ፡ ይባላል ።

አቢ ፡ የሚያዝሉ ፡ ሴቶች ፡ ልጅ ፡ ወይም ፡ አቢ መሆኑ ፡ የሚታወቀው ፡ በቅርብ ፡ ሲሆኑ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በሩቅ ፡ ግን ፡ ሁሉም ፡ ልጅ ፡ ያዘሉ፤ ሴቶች ፡ ይመስላሉ ።

አሁን ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ አንዳንድ ፡ ሴቶች ፡ እንደ ፡ አውሮፓ ፡ ሴቶች ፡ መልበስ ፡ ጀምረዋል ። ነገር ፡ ግን ፡ አቢ ፡ በሚያዝሉት ፡ ሴቶች ፡ ዘንድ ፡ ያገራቸውን ፡ ክብር ፡ እንደ ፡ ናቁና ፡ እንዳዋረዱ ፡ ተቆጥሮባቸዋል ።

ከዚህም ፡ በቀር ፡ ወደ ፡ ዘመድ ፡ ቤት ፡ ሲሔዱና ፡ ለበዓል ፡ ሲወጡ፡ በአቢያቸው ፡ ላይ ፡ የሚደርቡት ፡ ከወደ ፡ ፊቱ ፡ ክፍት የሆነ ፡ ኪሚኖ ፡ የሚባል ፡ ልብስ ፡ አላቸው ። በዚህም ፡ ኪሚኖ ፡ በሚባለው ፡ ልብሳቸው፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ወንዶቹ ፡ ልብስ፡የትውልዳቸው ፡ ምልክት ፡ ይጠለፍበታል።

በእግራቸው ፡ አጭር ፡ ነጭ ፡ ሹራብ ፡ አድርገው ፡ በነጭ ፡ ልብስ ፡ ወይም ፡ በከፈይ ፡ የተለበጠ ፡ የእንጨት ፡ ጫማ ፡ ያደርጋሉ ። ተራዎቹ ፡ ሴቶች ፡ ግን ፡ የእንጨት ፡ ጫማ ፡ ብቻ ፡ ያደርጋሉ ።

የቀሚሳቸው ፡ ቅዱ ፡ በጣም ፡ ጠባብና ፡ ረጅም ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በፍጥነት ፡ ለመሔድ ፡ አይችሉም፤በፍጥነትም ፡ለመሔድ፡ቢሞክሩ ፡ በእግረሙቅ ፡ እንደ ፡ ታሠረ ፡ ሰው ፡ ያሠግራቸዋል ። ደግሞ ፡ ቀሚሳቸው ፡ ከወደ ፡ ፊት ፡ ክፍት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ከግራ ፡ ወደ ፡ ቀኝ ፡ እያስተላለፉ ፡ ይለብሱታልና ፡ በፍጥነት ፡ ሲሔዱ ፡ እንዳይጋለጡ ፡ በጣም ፡ ይጠነቀቃሉ ።

---

## ስለ ፡ ሴቶች ፡ ጠጕር ፡ አሠራር ።

የጃፓን ፡ ሴቶች ፡ የራስ ፡ ጠጕራቸው ፡ አሠራር ፡ እጅግ ፡ የተዋበ ፡ ነው ። ለዚሁም ፡ ሶስት ፡ ዓይነት ፡ አሠራር ፡ አላቸውና ፡ እንደ ፡ ፈቃዳቸው ፡ ይሠራሉ ።

፩ኛው ፡ ዓይነት ። በፊትና ፡ በኋላ ፤ በቀኝና ፡ በግራ ፤ እንደ ፡ መስቀል ፡ ሆኖ ፡ መከከሉ ፡ አክሊል ፡ ይመስላል ።

፪ኛው ፡ ዓይነት ። ጠጉራቸው ፡ ዙሪያውን ፡ ተሰብስቦ ፡ በመካከሉ ፡ ላይ ፡ ተቋጥሮ ፡ የእህል ፡ ምርት ፤ ወይም ፡ የህንዶችን ፡ ቆብ ፡ ይመስላል ።

፫ኛው ፡ ዓይነት ። ጠጉራቸው ፡ በሙሉ ፡ ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ተሰብስቦ ፡ በማንጅራታቸው ፡ ላይ ፡ ይቋጠራል ። አንዳንዱ ፡ የወርቅ ፡ ሚዶና ፡ የአርቲፊሲል ፡ አበባ ፡ ያደርጉበታልና ፡ በጣም ፡ ያምራል ።

የጃፓን ፡ ሴቶች ፡ በጆሮዋቸውና ፡ በንገታቸው ፡ ማናቸውንም ፡ የወርቅ ፡ ወይም ፡ የአልማዝ ፡ ጌጥ ፡ አያደርጉም ። እንደ ፡ ሸምበቆ ፡ አገዳ ፡ በረዛዘመው ፡ ጣታቸው ፡ ብቻ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ዓይነት ፡ ቀለበት ፡ ያደርጋሉ ።

## ስለ ፡ ወንዶች ፡ ፊት ፡ ማሳመር ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ ወንዶች ፡ ሁሉ ፡ ጢማቸውን ፡ እየላጩ ፡ ፊታቸውን ፡ ያሳምራሉ ። የራስ ፡ ጠጉራቸውንም ፡ በልኩ ፡ እየተቆረጡ ፡ በሚዶና ፡ በቡሩሽ ፡ ያሳምራሉ ። ምናልባት ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ ጢማቸውን ፡ የማይላጩና ፡ የራስ ፡ ጠጉራቸውን ፡ እያበጠሩ ፡ የማያሳምሩ ፡ ከሺ ፡ አንድ ፡ ይገኝ ፡ ይሆናል ። ያውም ፡ እጅግ ፡ ከራቁት ፡ በሰሜን ፡ ካሉት ፡ ባላገሮች ፡ ነው ።

## ስለ ፡ መልክና ፡ ስለ ፡ ቁመት ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ ከወንዶቹም ፡ ከሴቶቹም ፡ የሚበዙት ፡ ዓይናቸው ፡ ትንንሽ ፤ አፍንጫቸው ፡ ደፍጣጣ ፡ ነው ፤ ከነዚሁም ፡ በዓይናቸው ፡ መነጥር ፡ በጥርሳቸው ፡ ወርቅ ፡ የሚያደርጉት ፡ ይበዛሉ ። ቁመታቸውም ፡ አጫጭር ፡ ነው ። ምናልባት ፡ ከመቶው ፡ አሥር ፡ ረጃጅሞች ፡ ይገኙ ፡ ይሆናል ። የጦር ፡ አለቆች ፡ ግን ፡ ሁሉም ፡ ረጃጅሞችና ፡ አካለ ፡ ሙሉ ፡ ናቸው ።

## ስለ ፡ ባርኔጣ ፡ ማድረግ ።

የጃፓን ፡ ሰዎች ፡ ትልቁም ፡ ትንሹም ፡ እንደ ፡ ባለጠግነታቸው ፡ ማለፊያና ፡ መናኛ ፡ ይሁን ፡ እንጂ ፡ ሁሉም ፡ ባርኔጣ ፡ ያደርጋሉ ። የጥንቱን ፡ የጃፓንን ፡ ልብስ ፡ የሚለብሱና ፡ ጠጉራቸውን ፡ እንደ ፡ ጥንቱ ፡ ል

ማድ ፡ የሚያሳምሩ ፡ ሴቶች ፡ ብቻ ፡ ባርኔጣ ፡ አያደርጉም ። ቢሆንም ፡ የ ትልልቅ ፡ ወገን ፡ የሆኑት ፡ ወይዛዝሮች ፡ እጅግ ፡ የሚያምረውን ፡ በሀገ ራቸው ፡ የሚሠራውን ፡ የሐር ፡ ወይም ፡ የወረቀት ፡ ጥላ ፡ ይይዛሉ ።

## ስለ ፡ ጫማ ፡ ማድረግ ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ በመንግሥትና ፡ በኩምፓንያ ፤ በራሳቸውም ፡ ቢ ሆን ፡ በዋና ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ቀን ፡ ቀን ፡ የአውሮጳ ፡ ጫማ ፡ አድርገው ፡ ይውላሉ ። ማታ ፡ ማታ ፡ ግን ፡ በየቤታቸው ፡ ከት ንንሽ ፡ የእግር ፡ ሹራብ ፡ ጋራ ፡ የእንጨት ፡ ነጠላ ፡ ጫማ ፡ ያደርጋሉ ።

## ስለ ፡ መብል ።

በጃፓኖች ፡ ቤት ፡ ሁለት ፡ ዓይነት ፡ መብል ፡ ይዘጋጃል ።

አንደኛው ፡ ዓይነት ፡ ያገራቸው ፡ መብል ፡ ነው ። ይኸውም ፡ ከአታ ክልት ፤ ከዓሣ ፤ ከሥጋ ፤ ከሩዝ ፡ የሚሰናዳ ፡ ነው ። ዳቦ ፡ ወይም ፡ ሌላ ፡ ዓይነት ፡ እንጀራ ፡ የለም ። መብሉ ፡ ለስላሳና ፡ ጣፋጭ ፡ ነገር ፡ ነው ። ለ ውጭ ፡ አገር ፡ ሰው ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አያሰኝም ። የዓሣና ፡ የዶሮ ፡ ሥጋ ፡ ከምጣጤ ፡ የሚመስል ፡ ከቅመም ፡ የተሠራ ፡ መረቅ ፡ ቀርቦ ፡ በዚያ ፡ እ የተነከረ ፡ እርጥቡን ፡ ይበላል ።

መብል ፡ ሲቀርብ ፡ ለያንዳንዱ ፡ ሰው ፡ በተለየ ፡ ዕቃ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ለብዙ ፡ ሰዎች ፡ ባንድ ፡ ዕቃ ፡ አይቀርብም ። ወጡም ፡ በትንንሽ ፡ ሳህን ፡ ለየብቻው ፡ እየቀረበ ፡ ባለቤቱ ፡ እየመረጠ ፡ ይበላል ።

የሚበላውም ፡ በማለፊያ ፡ ሆኖ ፡ በታነጸ ፡ በሁለት ፡ ድብልብል ፡ እን ጨት ፡ እየተጣበቀ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እጅ ፡ አይነካውም ። ጌታ ፡ ጌታው ፡ ከ ዝሆን ፡ ጥርስ ፡ የተሠራ ፡ ማጣበቂያ ፡ አለው ።

ይህንኑም ፡ የሚያቀርቡ ፡ ልጃገረዶች ፡ ሴቶች ፡ ናቸው ፡ እንጂ ፡ ወን ድ ፡ አያቀርብም ።

ራት ፡ በሚበላበት ፡ ጊዜ ፡ ክራር ፡ እየተመታ ፡ ልጃገረዶች ፡ እንዲዘ ፍኑና ፡ እንዲጨፍሩ ፡ ይታዘዛሉ ።

ሁለተኛው ፡ ዓይነት ፡ መብል ፡ የአውሮጳ ፡ ወጥ ፡ ነው ። ጃፓኖች ፡ የ አውሮጳ ፡ ወጥ ፡ መሥራት ፡ ተምረው ፡ ለምደዋልና ፡ በጣም ፡ ይጣፍጣል ።

የሚቀርበውም ፡ አራት ፡ ዓይነት ፡ ነው ።

መጀመሪያ ፡ አዳብር ፡ ወይም ፡ ሾርባ ፤
ቀጥሎ ፡ ዓሣ ፡ ወይም ፡ ሌላ ፡ ዓይነት ፤
ቀጥሎ ፡ ሥጋ ፡ አተርም ፡ ዲኒችም ፡ ሌላም ፡ ቢኖር ፡ አንድነት ፡ ይቀርባል ፤
ቀጥሎ ፡ ጥብስና ፡ ሰላጣ ፤
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ጋቶና ፡ ፍሬ ፡ ነው ።

## ስለ ፡ መጠጥ ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ የጃፓን ፡ መብል ፡ በሚበላበት ፡ ጊዜ ፡ ከሩዝ ፡ ከወጣው ፡ ሳኬ ፡ ከሚባለው ፡ መጠጥ ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ መጠጥ ፡ አይቀርብም ። ያውም ፡ እንደ ፡ ሻይ ፡ ተፈልቶ ፡ ሳይበርድ ፡ ትኩሱን ፡ ነው ። የሚጠጣውም ፡ በትንሽ ፡ በቡን ፡ ሲኒ ፡ ነው ። ሲጠጡ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ይገባበዛሉና ፡ የጠጣበትን ፡ ሲኒ ፡ አጠገቡ ፡ ባቀረበው ፡ ውሀ ፡ አጥቦ ፡ ላንዱ ፡ ይሰጥና ፡ ሳኬውን ፡ አንሥቶ ፡ ይቀዳለታል ። ወይም ፡ አሣላፊዋ ፡ ልጃገረድ ፡ ትቀዳለትና ፡ ጠጥቶ ፡ እንደዚያው ፡ ሲኒውን ፡ አጥቦ ፡ ይመልስለታል ።

የውጭ ፡ አገር ፡ መብል ፡ በሚበላበትና ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰው ፡ በሚጋብዙበት ፡ ጊዜ ፡ ቢራም ፡ ሎሚናትም ፤ የወይን ፡ ጠጅም ፡ ሻምፓኝም ፡ ይቀርባል ።

## ስለ ፡ መከባበር ።

ጃፓኖች ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ሲገናኙ ፡ በጣም ፡ ይከባበራሉ ። እጅ ፡ አነሣሣቸውም ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ግንባር ፡ ለግንባር ፡ ተቃርበው ፡ ሁለቱም ፡ ጉልበታቸውን ፡ እየያዙ ፡ በጣም ፡ እያጐነበሱ ፡ ነው ። አንዱ ፡ ሰው ፡ ተቀምጦ ፡ ሌላው ፡ ሰው ፡ የመጣ ፡ እንደሆነ ፡ መጭው ፡ ቀርቦ ፡ በጉልበቱ ፡ ተንበርክኮ ፡ ግንባሩን ፡ ወደ ፡ መሬት ፡ ደፍቶ ፡ እጅ ፡ ሲነሣ ፡ የተቀመጠውም ፡ ሰው ፡ ተንበርክኮ ፡ አጎንብሶ ፡ እጅ ፡ ይነሣል ።

ከወንዶች ፡ ይልቅ ፡ ሴቶች ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ በጣም ፡ ይከባበራሉ ፡ አንዲቱ ፡ ሴት ፡ ለሌላይቱ ፡ ሴት ፡ እጅ ፡ ስትነሣ ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ ገረድ ፡ ለመቤቷ ፡ እጅ ፡ እነደምትነሣ ፡ ያህል ፡ ነው ።

ለባሎቻቸውም ፡ እጅ ፡ሲነሡ ፡ በማክበርና ፡ በመፍራት ፡ ነው ።



የጃፓን ፡ አገር ፡ ሴቶች ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ሲከባበሩ ።



ትልቅ ፡ እንግዳ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡
የጃፓን ፡ ሴቶች ፡ እጅ ፡ አነሳሥ ።

## ስለ ፡ እንግዳ ፡ አቀባበል ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ ወንዶችም ፡ ሴቶችም ፡ እንግዳ ፡ ያከብራሉ ። እንግዳም ፡ ወደ ፡ ቤታቸው ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ባለቤቱና ፡ ሚስቱ ፡ ሴቶች ፡ ልጆቹና ፡ ገረዶቹም ፡ በቤቱ ፡ መዝጊያ ፡ አጠገብ ፡ ተንበርክከው ፡ ይቆዩና ፡ እንግዳው ፡ ሲደርስ ፡ እንደ ፡ ተንበረከኩ ፡ በግንባራቸው ፡ እጅ ፡ ይነሣሉ ። በግብዣም ፡ ጊዜ ፡ እንግዳው ፡ በልቶ ፡ የጠገበ ፡ አይመስላቸውምና ፡ እባክህ ፡ ተጋበዝ ፡ እያሉ ፡ በለዘብታ ፡ ቃልና ፡ በብሩህ ፡ ገጽ ፡ ይለምናሉ ። ይኸውም ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ በሚፋቀረው ፡ ቤተ ፡ ዘመድ ፡ ቤት ፡ እንደ ሚደረገው ፡ ነው ።

---

## ስለ ፡ ቤት ፡ አሠራር ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ ይልቁንም ፡ በየከተማው ፡ ስሙ ፡ የታወቀ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ባንድ ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ብዙ ፡ ክፍል ፡ ያለው ፡ ሁለት ፡ ዓይነት ፡ ቤት ፡ ይሠራል ። አንደኛው ፡ ዓይነት ፡ እንደ ፡ ጥንቱ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ ልማድ ፡ የተሠራ ፤ በነጭ ፡ የሣር ፡ ኬሻ ፡ የተነጠፈ ፤ በመስታወትና ፡ መስታወት ፡ በሚመስል ፡ ወረቀት ፡ ያጌጠ ፤ ለዓይን ፡ የሚያምር ፡ ቤት ፡ ነው ። በዚህም ፡ ቤት ፡ ማንም ፡ ጌታ ፡ ቢሆን ፡ ጫማውን ፡ ሳያወልቅ ፡ ለመግባት ፡ አይፈቀድለትም ። ምክንያቱም ፡ ከጫማው ፡ ጋራ ፡ የሚገባው ፡ ጉድፍ ፡ የቤቱን ፡ ጥዳትና ፡ ምንጣፍ ፡ እንዳያበላሽ ፡ ነው ።

ሁለተኛው ፡ ዓይነት ፡ እንደ ፡ አዲሱ ፡ ዘመን ፡ የተሠራና ፡ በሣንቃ ፡ የተመታ ፤ ሥጋጃም ፡ የተነጠፈበት ፡ ቤት ፡ ነው ።

በዚህም ፡ ቤት ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰው ፡ ይቀበሉበታል ።

በዋና ፡ በዋና ፡ ከተሞች ፡ አንዳንድ ፡ ትልልቅ ፡ ቤት ፡ ይገኛል ፤ ያውም ፡ ቢሆን ፡ ካንድ ፡ እስከ ፡ አሥር ፤ ደርብ ፡ ያለበት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከዚህ ፡ የበለጠ ፡ ደርብ ፡ ያለበት ፡ አይገኝም ።

በየዋናው ፡ ከተማ ፡ የድንጋይ ፡ ቤት ፡ ምናልባት ፡ ከመቶው ፡ አሥር ፡ ይገኝ ፡ ይሆናል ። የቀረው ፡ ግን ፡ በብረትና ፡ በስሚንት ፡ ወይም ፡ በብረትና ፡ በሸክላ ፡ ጡብ ፡ የተሠራ ፡ ነው ። ቢሆንም ፡ ሥራውና ፡ ክፍሉ ፡ ያማረ ፡ ነው ።

በባላገር ፡ ያለው ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ጠባብና ፡ አጫጭር ፡ ግድግዳው ፡ የሣንቃ ፡ ክዳኑም ፡ የሸክላ ፡ ነው ። ከዚህም ፡ በቀር ፡ በሣርና ፡ በዛፍ ፡ ቅርፊት ፡ የተከደነ ፡ አንዳንድ ፡ ቤት ፡ ይታያል ።

የባላገሩ ፡ ቤት ፡ የተሠራው ፡ የምድር ፡ ባቡሩን ፡ መንገድ ፡ እየተ ከተለ ፡ ነው ። ከምድር ፡ ባቡር ፡ እርቀው ፡ የሚኖሩ ፡ ግን ፡ ትልልቅ ፡ ሀብታሞች ፡ ሰዎች ፡ ናቸው ። ቢሆንም ፡ ካንዱ ፡ መንደር ፡ ወደንዱ ፡ መንደር ፡ መገናኛ ፡ የአውቶሞቢል ፡ መንገድ ፡ አላቸው ።

## ስለ ፡ ፋብሪካና ፡ የእጅ ፡ ሥራ ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ የፋብሪካ ፡ ሥራ ፡ በጣም ፡ የተለመደና ፡ የሰፋ ፡ ነው ። ከፋብሪካዎቹም ፡ እኛ ፡ ያየናቸው ፡ ዋና ፡ ዋኖቹ ፡ የሐር ፡ ፋብ ሪካ ። የሸማ ። የብርጭቆ ። የሸክላ ። የሲሊ ። የአይሮፕላን። የመድፍና፡ የጠመንጃ ። የኤሌክትሪክ ፡ ማብሪያ ፡ ብርጭቆ ። የዶሮ ፡ ማርቢያ ። የ ጋዜጣና ፡ የመጽሐፍ ፡ ማተሚያ ። የሩዝ ፡ ማበጠሪያ ። የእንጨት ፡ ማ ነጫ ። የባቡር ፡ ዋጎንና ፡ሎኮሞቲፍ ፡ መሥሪያ። የትንኝና ፡ የዝንብ ፤ የሌላም ፡ ትል ፡ መግደያ ።ለሥራው ፡ ሁሉ ፡ የሚሆን ፡ ሞተር ፡ ነው ።

በያንዳንዱም ፡ ፋብሪካ ፡ የሚሠሩ ፡ ሠራተኞች ፡ ቍጥራቸው ፡ ከሁለት ፡ ሺ ፡ በላይ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከሁለት ፡ ሺ ፡ በታች ፡ የሆነ ፡ አይገኝም ።

ይህንም ፡ የመሰለው ፡ የፋብሪካ ፡ ሥራ ፡ ባገር ፡ ላይ ፡ ሶስት ፡ ጥ ቅም ፡ የሚያስገኝ ፡ ነው ። ፩ኛ ፡ ጥቅም ። ኩምፓንያው ፡ ብዙ ፡ ገቢ ፡ ገንዘብ ፡ ያገኛል ። ፪ኛ ፡ ጥቅም ። ሕዝቡ ፡ እየሠራ ፡ የእለት ፤ እንጀራ ፡ ያገኛሉ ። ፫ኛ ፡ ጥቅም ። መንግሥት ፡ የግብር ፡ (የታክስ) ገቢ ፡ ያገኛል ።

በየፋብሪካውም ፡ የሚሠሩት ፡ ሰዎች ፡ እንደ ፡ ራሳቸው ፡ አድርገው ፡ በትጋት ፡ ይሠራሉ ፡ እንጂ ፡ የልግም ፡ ሥራ ፡ አይሠሩም ። ይህንም ፡ በመሰለ ፡ ትጋት ፡ ባለጠጎች ፡ ሠራተኛ ፡ ሳይቸገሩ ፤ ድሆችም ፡ ሥራ ፡ ሳያጡና ፡ ሳይራቡ ፡ በደስታ ፡ ይኖራሉ ።

## ስለ ፡ ትምሕርት ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ የትምሕርት ፡ ነገር ፡ በብዙ ፡ ትጋት ፡ ተይዟል ። የመ ጀመሪያው ፡ ክፍል ፡ ትምሕርት ፡ ተማሪዎችና ፡ የመካከለኛው ፡ ትምሕር ት ፡ ተማሪዎች ፤ የዩኒቢርሲቲም ፡ ተማሪዎች ፡ ጧት ፡ በሁለት ፡ ሰዓት ፡ ወደ ፡ ትምሕርት ፡ ቤት ፡ ሲሔዱ ፤ በ፰ ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ለምሳ ፡ በየቤታ ቸው ፡ ሲመለሱ ፤ ወደ ፡ ማታም ፡ እንደዚሁ ፡ ሲሔዱና ፡ ሲመለሱ ፡ በየመ ንገዱ ፡ ዳር ፡ ቆሞ ፡ ለሚያያቸው ፡ ሰው ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ ለመ ስቀል ፡ ወይም ፡ ለጥምቀት ፡ በዓል ፡ የሚታየውን ፡ ሕዝብ ፡ ይመስላል ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ ወንድም ፡ ሴትም ፤ ጌታም ፡ ድሀም ፡ ቢሆን ፡ የማያነብና ፡ የማይጽፍ ፡ አይገኝም ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

እንግዴህ ፡ ሥልጣኔና ፡ ብልጥግና ፡ የሚገኘው ፡ በትምሕርት ፡ መሆኑን ፡ በጃፓን ፡ ሕዝብ ፡ ለመረዳት ፡ ይቻላል ።

## ስለ ፡ መንገድ ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ የመንገድ ፡ ሥራ ፡ በትጋት ፡ ተይዟል ። በያንዳንዱ ፡ አገር ፡ የባቡር ፡ መንገድ ፡ የትራምይ ፡ መንገድ ፤ የአውቶሞቢል ፡ መንገድ ፡ እየሆነ ፡ ሶስት ፡ ሶስት ፡ መንገድ ፡ ተሠርቶበታል ። ስለዚህ ፡ ሕዝቡ ፡ ካንዱ ፡ አገር ፡ ወደ ፡ ሌላው ፡ አገር ፡ በፍጥነት ፡ ለመዛወር ፤ የንግዱንም ፡ ዕቃ ፡ ካንዱ ፡ አገር ፡ ወዳንዱ ፡ አገር ፡ በፍጥነት ፡ ለማስተላለፍና ፡ ለማትረፍ ፡ ስለ ፡ ተመቻቸው ፡ ሕዝቡ ፡ በልጥገዋል ።

## ስለ ፡ ኤሌክትሪክ ፡ ማብራት ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ ምንም ፡ ትንሽ ፡ መንደር ፡ እንኳ ፡ ቢሆን ፡ የኤሌክትሪክ ፡ መብራት ፡ የሌለበት ፡ አይገኝም ። ስለዚህ ፡ የጨረቃ ፡ ብርሃንም ፡ ባይኖር ፡ አገሩ ፡ በሌሊት ፡ የጨረቃ ፡ ብርሃን ፡ ያህል ፡ ይታያል ።

## ስለ ፡ ሥራ ፡ መውደድ ።

የጃፓን ፡ ሰዎች ፡ ወንዶቹም ፡ ሴቶቹም ፤ ትልቁም ፡ ትንሹም ፡ ሥራ ፡ ወዳጆች ፡ ናቸው ። ስለዚህ ፡ ብዙ ፡ ችግረኛ ፡ የለባቸውም ። ብዙም ፡ ገንዘብ ፡ ያለው ፡ ቢሆን ፡ ገንዘቤ ፡ ብዙ ፡ ነው ፡ በማለት ፡ ከሥራ ፡ አያርፍም ።

በ፲፱፻፳፫ ዓመት ፡ በየቤቱ ፡ ለየራሱ ፡ ከሚሠራው ፡ በቀር ፡ በደመወዝ ፡ እየተቀጠረ ፡ የሚሠራው ፡ ወንዱም ፡ ሴቱም ፡ ቢቆጠር ፡ ብዛቱ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ እንዳለው ፡ ሆነ ።

## ወንዶች ።

| | | |
|---|---|---|
| በእርሻና ፡ በእጅ ፡ ሥራ ፡ የተቀጠሩ ፡ . | ፩ሚሊዮን ፡ | |
| በፋብሪካ ፡ ሥራ ፡ የተቀጠሩ ፡ . . . | ፩ሚሊዮን ፡ | ፪፻፺ሺ ። |
| በልዩ ፡ ልዩ ፡ ሥራ ፡ የተቀጠሩ ፡ . . . | ፩ሚሊዮን ፡ | ፪፻..ሺ ። |
| በአሽከርነት ፡ ሥራ ፡ የተቀጠሩ ፡ . . . . | ፩ሚሊዮን ፡ | |
| ሳይቀጠሩ ፡ በቀን ፡ ሥራ ፡ የሚሠሩ ፡ . . . . . . | | ፫፻፳ሺ ። |

## ሴ ቶ ች ።

በፋብሪካና ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ሥራ ፡ የተቀጠሩ ፡ ፲፱ሚሊዮን ፡ ፯፻፸ሺ ።
በህክምና ፤ ሥራ ፡ የተቀጠሩና ፡ የሚያክሙ ፡ . . . . ፩ሺ ።
በህክምና ፡ ሥራ ፡ የሚረዱና ፡ የሚያስታምሙ ፡ . . . ፴፰ሺ ።
አዋላጆች ፡ . . . . . . . . . . . . . . . ፴፰ሺ ።
(አውት ፡ ላይን ፡ ሂስቶረ ፡ አፍ ፡ ጃፓን ፡ ፬፻፲፯ ገጽ ፡ እይ )

## ስለ ፡ ቀን ፡ ሠራተኞች ፡ ዋጋና ፡ ስለ ፡ ሥራ ፡ ሰዓት ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ ማናቸውም ፡ ተራ ፡ ሠራተኛ ፡ በቀን ፡ አንድ ፡ ዬን ፡ ከሀያ ፡ ሳንቲም ፡ ያገኛል ። ለቍርስና ፡ ለምሳ ፡ ለራቱ ፡ ሰባ ፡ ሳንቲም ፡ ይበቃዋል ። አምሳ ፡ ሳንቲም ፡ ይተርፈዋል ። ስለ ፡ መኝታው ፡ ከሩቅ ፡ አገር ፡ የመጣ ፡ ሠራተኛ ፡ የሆነ ፡ እንደሆነ ፡ ባለቤቱ ፡ የመኝታ ፡ ቤት ፡ ይሰጠዋል ። ባላገር ፡ የሆነ ፡ እንደሆነ ፡ ግን ፡ ሲሠራ ፡ እየዋለ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ይሔዳል ።

የቀን ፡ ሠራተኛ ፡ ድሀ ፡ በድንገት ፡ የታመመ ፡ እንደሆነ ፡ ባለቤቱ ፡ ለሀኪም ፡ ዋጋ ፡ ከፍሎ ፡ ያሳክመዋል ። ሲድን ፡ ግን ፡ ከዋጋው ፡ እየቀነሰ ፡ ያስቀራል ። ለሠራተኛ ፡ የተወሰነው ፡ ሰዓት ፡ በቀን ፡ ፰ሰዓት ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ ከዚህ ፡ የበለጠ ፡ ሰዓት ፡ ለማሠራት ፡ የፈለገ ፡ እንደሆነ ፡ ከሠራተኛው ፡ ጋራ ፡ ተስማምቶ ፤ ልዩ ፡ ዋጋ ፡ ጨምሮ ፡ ይሰጠዋል ።

## ስለ ፡ ጃፓኖች ፡ አመልና ፡ ጠባይ ።

የጃፓን ፡ ሕዝብ ፡ ጠባያቸው ፡ ሁሉ ፡ እጅግ ፡ የተወደደ ፡ ነው ። መልካሙንና ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ ያለበትን ፡ ሁሉ ፡ ለመመርመር ፡ ብርቱ ፡ የሆነ ፡ ፈቃድ ፡ አላቸው ። ሽማግሎችንና ፡ ባልንጀሮቻቸውን ፡ አክባሪዎች ፤ ለሹሞች ፡ ታዛዥዎች ፡ ናቸው ። ማናቸውንም ፡ ነገር ፡ በተንኰልና ፡ በማታለል ፡ ከማድረግ ፡ በድፍረትና ፡ በግልጥ ፡ ማድረግ ፡ ይወዳሉ ። ክብርን ፡ ለማግኘት ፡ ተጣጣሪዎች ፡ ካገኙትም ፡ በኋላ ፡ ክብራቸውን ፡ ጠባቂዎች ፡ ናቸው ። ከጃፓኖች ፡ ብዙዎቹ ፡ ድህነትና ፡ ችግር ፡ አለባቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ ችለው ፡ በትዕግሥት ፡ ያሳልፉታል ፡ እንጂ ፡ አያፍሩበትም ። መንፈሳቸው ፡ ታሪክንና ፡ አዲስ ፡ ነገርን ፡ ለመመርመር ፡ በጣም ፡ የበረታ ፡ ነው ። ለማናቸውም ፡ ነገር ፡ ጥያቄና ፡ ክርክር ፡ ያበዛሉ ። ለጠየቁትም ፡ ነገ



የጃፓን ፡ አገር ፡ ሴቶች ፡ እንግዶች ፡ ለመቀበል ፡ ሲጠባበቁ ።




በጃፓን ፡ አገር ፡ የሻይ ፡ ቅጠል ፡ የሚለቅሙና ፡ የሚሰበስቡ ፡ የሴቶች ፡ ሠራተኞች ።

ር ፡ በቶሎ ፡ ምላሽ ፡ ለማግኘት ፡ ይፈልጋሉ ። የሰሙትንና ፡ የተረዱትን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ለወዳጆቻቸውና ፡ ለባልንጀሮቻቸው ፡ ለማካፈል ፡ በጣም ፡ ይቸኩላሉ ።

አውት ፡ ላይን ፡ ሒስቶሪ ፡ ፪፻ ገጽ ።
ጃፓንስ ፡ ሮማንስ ፡ ፪፳ ገጽ ። ተመልከት ።

## ስለ ፡ ጃፓኖች ፡ ጅግንነትና ፡ ጉብዝና ።

ጃፓኖች ፡ በጦርነት ፡ ጊዜ ፡ ጨካኞችና ፡ ልበ ፡ ቆራጦች ፡ ናቸው ።

ስለዚሁም ፡ ሲነገር ፡ ውበት ፡ ለግሪኮች ፤ ቅዱስነት ፡ ለእስራኤል ፤ ቅንነት ፡ ለሮማውያን ፤ ጅግንነት ፡ ለጃፓኖች ፡ ይባላል ።

በጦርነት ፡ ውስጥ ፡ ሲዋጉ ፡ የጠላት ፡ ወገን ፡ ድል ፡ የሚያደርግ ፡ የመሰላቸው ፡ እንደሆነ ፡ በጠላቶቻችን ፡ እጅ ፡ ተማርከን ፡ ክብራችንን ፡ አናዋርድም ፡ እያሉ ፡ በገዛ ፡ እጃቸው ፡ ራሳቸውን ፡ ይገድላሉ ።

ይኸውም ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ በመቅደላ ፡ ጦርነት ፡ ጊዜ ፡ አባ ፡ ታጠቅ ፡ ቴዎድሮስ ፡ እንዳደረጉት ፡ ነው ።

ደግሞ ፡ በመታመንና ፡ በፍቅር ፡ እያገለገሏቸው ፡ የሚኖሩት ፡ ወዳጆቻቸው ፡ ነገሥታቶች ፡ ሲሞቱ ፡ ከጌታችንና ፡ ከንጉሣችን ፡ ከዕገሌ ፡ የተረፈ ፡ እድሜ ፡ አያምረንም ፡ እያሉ ፡ ራሳቸውን ፡ ይገድላሉ ።

ይህንም ፡ የሚያስረዳ ፡ ነገር ፡ የቀድሞው ፡ ዘመን ፡ ይቅርና ፡ አሁን ፡ በቅርቡ ፡ ባ፲፱፻፲፪ ፡ ዓ ፡ ም ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሜጂ ፡ ሲሞት ፡ ከመስኮቦች ፡ ጋራ ፡ ተዋግቶ ፡ ድል ፡ ያደረገው ፡ ጀኔራል ፡ ኖጊ ፡ የሚባለው ፡ ወዳጁ ፡ ራሱን ፡ ገድሏል ።

ቀጥሎም ፡ በ፲፱፻፲፱ ፡ ዓ ፡ ም ፡ የሜጂ ፡ ልጅ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ቴይሾ ፡ ሲሞት ፡ ወዳጁ ፡ የነበረ ፡ ባሮን ፡ ኢኪዳ ፡ እንደዚሁ ፡ ራሱን ፡ ገድሏል ።

ደግሞ ፡ እብዝቶ ፡ ይበላና ፡ ይጠጣ ፡ የነበረ ፡ አንዱ ፡ ወዳጁ ፡ ንጉሡ ፡ ቴይሾ ፡ በታመመ ፡ ጊዜ ፡ መብልና ፡ መጠጡን ፡ ትቶ ፡ አድንልኝ ፡ እያለ ፡ ሌት ፡ ተቀን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይጸልይ ፡ ነበርና ፡ ጸሎቱ ፡ ሳይሰማለት ፡ ቀርቶ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ በሞተ ፡ ጊዜ ፡ ራሱን ፡ ገደለ ።

(አውት ፡ ላይን ፡ ሒስቶሪ ፡ ፬፻፲ ገጽ ፡ ተመልከት ፡)

በማናቸውም ፡ ቢሆን ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ በጦርነት ፡ ጊዜና ፡ በጌታው ፡ ፍቅር ፡ ራሱን ፡ የሚገድል ፡ ሰው ፡ እንደ ፤ ትልቅ ፡ ጅግንነት ፡ እየተቆጠረለት ፡ ሽራይን ፡ እየተሠራ ፡ ይሰገድለታል ። ሀውልትም ፡ ተቀርጾ ፡ ይቆምለታል ።

## ስለ ፡ ባልና ፡ ሚስት ፡ ጋብቻ ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ ለወንዱ ፡ ልጃቸው ፡ ሚስት ፡ የሚፈልጉና ፡ የሚመርጡ ፡ አባትና ፡ እናቱ ፡ ናቸው ። አንዳንዱ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ እንደ ፡ አውሮፓ ፡ ሕዝብ ፡ ልማድ ፡ ራሱ ፡ እየፈለገና ፡ እየመረጠ ፡ ያገባል ። የጋብቻው ፡ ሥርዓትና ፡ የሠርጉ ፡ አደራረግ ፡ በጣም ፡ ቀላል ፡ ነው ። በመጀመሪያ ፡ አባትና ፡ እናቱ ፡ ሚስት ፡ ፈልገውለት ፡ የልጅቱ ፡ አባትና ፡ እናት ፡ እሺ ፡ እንሰጣለን ፡ ካሉ ፡ በኋላ ፡ የማጫውን ፡ ገንዘብ ፡ ማሰናዳት ፡ ይጀምራሉ ። የማጫውም ፡ ስጦታ ፡ ሀብታምና ፡ ድሀ ፡ እንደመሆኑ ፡ የሚቻለውን ፡ ያህል ፡ የልብስና ፡ የጌጥ ፡ የመብልና ፡ የመጠጥ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ጥሬ ፡ ገንዘብ ፡ አይዶለም ። ማጫውም ፡ ከተሰናዳ ፡ በኋላ ፡ ወስደው ፡ ለልጅቱ ፡ አባትና ፡ እናት ፡ ይሰጧቸዋል ። እነዚያም ፡ ማጫውን ፡ የተቀበሉ ፡ እንደሆነ ፡ ሠርጉ ፡ በቶሎ ፡ እንዲሆን ፡ መፍቀዳቸው ፡ ነውና ፡ የሠርጉ ፡ ቀን ፡ ተቆርጦ ፡ ድግስ ፡ ይጀመራል ። ሳይቀበሉ ፡ የመለሱት ፡ እንደሆነ ፡ ግን ፡ ሠርጉ ፡ ይቆይ ፡ ማለታቸው ፡ መሆኑ ፡ በዚህ ፡ ይታወቃል ። በሙሽራውና ፡ በሙሽራይቱ ፡ ቤት ፡ ለሠርጉ ፡ የሚጠሩት ፡ ሰዎች ፡ ቤተ ፡ ዘመዶች ፡ የሆኑት ፡ ብቻ ፡ ናቸው ፡ እንጂ ፡ ሌሎች ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ አይጠሩም ። ሙሽራው ፡ ሚስቱን ፡ ለማምጣት ፡ ወደ ፡ ሚስቱ ፡ ቤት ፡ ሲሔድ ፡ የሚቻለውን ፡ ያህል ፡ ገጸ ፡ በረከት ፡ ይዞ ፡ ይሔዳል ። ሙሽራይቱም ፡ ወደ ፡ ባሏ ፡ ስትሔድ ፡ የሚቻላትን ፡ ያህል ፡ የቤት ፡ ዕቃና ፡ ልብስ ፡ ይዛ ፡ ትሔዳለች ። ሙሽራይቱ ፡ በሠርጓ ፡ ቀን ፡ የምትለብሰው ፡ ነጭ ፡ ሀር ፡ ነው ። ፊቷንና ፡ ራስዋንም ፡ ባይነ ፡ ርግብ ፡ ትሸፍናለች ። ወደ ፡ ባሏ ፡ ቤት ፡ ከገባች ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ዓይነ ፡ ርግቧን ፡ ገልጣ ፡ በትከሻዋ ፡ ላይ ፡ ጣል ፡ ታደርገዋለች ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በቤተ ፡ ዘመዶች ፡ መካከል ፡ ለሙሽራው ፡ ዝቅ ፡ ያለ ፡ መቀመጫ ፡ ለሙሽራይቱ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ መቀመጫ ፡ ተሰናድቶ ፡ ሁለቱም ፡ ይቀመጣሉ ። የሚጣፍጥ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ዓይነት ፡ ምግብና ፡ ሳኬ ፡ (የሩዝ ፡ አረቂ ፡ ) ይቀርብላቸዋል ። አሣላፊቱም ፡ ሶስት ፡ መለኪያ ፡ አቅርባ ፡ በሶስቱም ፡ መለኪያ ፡ ሳኬውን ፡ ቀድታ ፡ አንዱን ፡ መለኪያ ፡ አንሥታ ፡ ለሙሽራው ፡ ትሰጠዋለች ፤ እርሱም ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ፉት ፡ ብሎ ፡ ለሙሽራይቱ ፡ ይሰጣታል ፤ እርሷም ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ፉት ፡ ብላ ፡ ትመልስለታለች ፤ እንደዚህ ፡ እያደረጉ ፡ አንዱን ፡ መለኪያ ፡ እርሱ ፡ ሶስት ፡ ጊዜ ፡ እርሷ ፡ ሶስት ፡ ጊዜ ፡ ፉት ፡ ፉት ፡ እያደረጉ ፡ ሶስቱንም ፡ መለኪያ ፡ ይጠጣሉ ። ይኸውም ፡ ሙሽራው ፡ ዘጠኝ ፡ ጊዜ ፤ ሙሽራይቱ ፡

ዘጠኝ ፡ ጊዜ ፤ ማለት ፡ ነው ። ምሳሌውም ፡ ባልና ፡ ሚስቱ ፡ አንድ ፡ አካል ፡ ለመሆናቸው ፡ ነው ፡ ይባላል ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሙሽሮቹና ፡ ቤተ ፡ ዘመዶቹ ፡ ባንድነት ፡ ሆነው ፡ ወደ ፡ ሽንቶ ፡ ሽራይን ፡ ሔደው ፡ ጋብቻቸውን ፡ በጸሎት ፡ ያጸናሉ ። ይኸውም ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ የተክሊል ፡ ጋብቻ ፡ እንደማለት ፡ ነው ።

---

## ስለ ፡ ባልና ፡ ሚስት ፡ መፋታት ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ ባል ፡ ሚስቱን ፡ የሚፈታበት ፡ ሕግ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ እንደተጻፈው ፡ ጸንቶ ፡ ይኖር ፡ ነበር ።

፩ኛ ። ሴት ፡ ለባሏ ፡ አባትና ፡ እናት ፡ የማትታዘዝና ፡ ፈቃዳቸውን ፡ የማትፈጽም ፡ የሆነች ፡ እንደሆነ ፤ ባሏም ፡ አለመታዘዟን ፡ የተረዳው ፡ እንደሆነ ፡ ይፈታታል ።

፪ኛ ። ልጅ ፡ የማትወልድ ፡ መካን ፡ የሆነች ፡ እንደሆነ ፡ ከልጅ ፡ የሚስቴ ፡ ፍቅር ፡ ይበልጥብኛል ፡ ካላለ ፡ በቀር ፡ ይፈታታል ።

፫ኛ ። አመንዝራ ፡ የሆነችበት ፡ እንደሆነ ፡ ይፈታታል ።

፬ኛ ። ቁስለ ፡ ሥጋና ፡ ይኸን ፡ የመሰለ ፡ ለማየት ፡ የሚያሰቀቅና ፡ የማይድን ፡ ቁስል ፡ የያዛት ፡ እንደሆነ ፡ ይፈታታል ።

፭ኛ ። ቀናተኛ ፡ ሆና ፡ ባሏን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ የምትናገር ፡ የሆነች ፡ እንደሆነ ፡ ይፈታታል ።

፮ኛ ። አሳባቂና ፡ ነገረኛ ፡ በመሆኗ ፡ ከቤተ ፡ ዘመዶቹ ፡ ጋራ ፡ የምታጣላው ፡ የሆነች ፡ እንደሆነ ፡ ይፈታታል ።

፯ኛ ። የባሏን ፡ ገንዘብ ፡ እየሠረቀች ፡ ወደ ፡ አባቷ ፡ ቤት ፡ የምታሽሽ ፡ ወይም ፡ ያለፈቃዱ ፡ ለዘመድ ፡ ለወዳጅ ፡ እየሰጠች ፡ የምታባክን ፡ የሆነች ፡ እንደሆነ ፡ ይፈታታል ።

ከዚህም ፡ በላይ ፡ በተጻፈው ፡ ነገር ፡ ሕግ ፡ አፍራሽ ፡ መሆኗን ፡ ባሏ ፡ ከተረዳውና ፡ ለመፍታት ፡ ከፈለገ ፡ ለዳኛ ፡ ሳይነግር ፡ እንዲፈታት ፡ ነፃነት ፡ ነበረው ። አሁን ፡ ግን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂ ፡ ሕገ ፡ መንግሥት ፡ ካቆመ ፡ ወዲህ ፡ ሕግ ፡ አፍራሽ ፡ መሆኗ ፡ በዳኛ ፡ ፊት ፡ ሳይመሰከርና ፡ ሳይገለጥባት ፤ ዳኛውም ፡ ትፈታ ፡ ብሎ ፡ ሳይፈርድባት ፡ ባሏ ፡ እንደፈቀደ ፡ እንዳይፈታት ፡ ተከልክሏል ።

## ስለ ፡ ሞተ ፡ ሰው ፡ ፍታትና ፡ አቀባበር ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ ሰው ፡ ሲሞት ፤ ራሱን ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ እግሩን ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡ አድርገው ፡ አስተኝተው ፡ ባጠገቡ ፡ ዕጣን ፡ እያጨሱ ፡ ካህናቱን ፡ ይጠራሉ ።

ካህናቱም ፡ መጥተው ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ የሚጠራበትን ፡ ስሙን ፡ በነጭ ፡ ሣንቃ ፡ ላይ ፡ ጽፈው ፡ በሬሳው ፡ አጠገብ ፡ ያስቀምጣሉ ። ወዲያውም ፡ አፉን ፤ አፍንጫውን ፤ ጆሮውን ፡ መድኃኒትነት ፡ ባለው ፡ ዱቄት ፡ ይሞሉታል ። ሬሳውም ፡ ፵፰ ሰዓት ፡ ከቆየ ፡ በኋላ ፡ በሙቅ ፡ ውሀ ፡ ያጥቡታል ። ቀጥለውም ፡ ካህናቱ ፡ አጭር ፡ ጸሎት ፡ ከጸለዩለት ፡ በኋላ ፡ የራሱን ፡ ጠጉር ፡ ላጭተው ፡ ከተልባ ፡ እግር ፡ ወይም ፡ ከጥጥ ፡ የተሠራ ፡ ነጭ ፡ ልብስ ፡ አምጥተው ፡ ያለብሱታል ። በሬሳውም ፡ አጠገብ ፡ ነጭ ፡ ሀር ፡ በለበሰው ፡ ጠረጴዛ ፡ ላይ ፡ አበባ ፡ ያስቀምጣሉ ።

በሬሳውና ፡ በሰዎቹ ፡ መካከል ፡ መጋረጃ ፡ ተጋርዶ ፡ ከመጋረጃ፡ውጭ ስምንት ፡ ካህናት ፡ ልብሰ ፡ ተክህኖ ፡ ለብሰው ፡ ሶስቱ ፡ በቀኝ ፡ ሶስቱ ፡ በግራ ፡ ሁለቱ ፡ በሬሳው ፡ ግንባር ፡ ሆነው ፡ ይጸልያሉ ። ከካህናቱ ፡ ቀጥለው ፡ የሟቹ ፡ አባትና ፡ እናት ፤ ቀጥላ ፡ ሚስቱ ፤ ቀጥለው ፡ ልጆቹ ፤ ቀጥለውም ፡ ዘመዶቹ ፡ እንደ ፡ ትውልዳቸው ፡ አቀራረብ ፡ በተራ ፡ ይቀመጣሉ።

የሐዘን ፡ ልብሳቸው ፡ ምልክቱ ፡ ሰማያዊና ፡ ነጭ ፡ ልብስ ፡ ነው ። ሚስቱ ፡ ፊቷን ፡ ፑድር ፡(ነጭ ፡ ዱቄት )ደምድማ ፡ ከንፈሯንም ፡ በቀይ ፡ ቀለም ፡ ታቀላለች ። የራስ ፡ ጠጉሯንም ፡ እንደ ፡ ሀገሩ ፡ ልማድ ፡ አበጥራ ፡ ደህና ፡ አድርጋ ፡ በጌጠኛ ፡ ሚዶ ፡ ትይዘዋለች ። በውስጥ ፡ ማለፊያ ፡ ቀሚስ ፡ ለብሳ ፡ በአቢዋ ፡ ላይ ፡ ሰማያዊ ፡ ሀር ፡ ትደርባለች ። ከሠርግ ፡ ቀን ይልቅ ፡ በሐዘኗ ፡ ቀን ፡ ያምርባታል ፡ ይባላል ።

ሻይና ፡ የሚጣፍጥ ፡ ምግብ ፡ ሁሉ፡ቀርቦ፡ለቤተ፡ዘመዱና፡ለካህናቱ፡ ይታደላል ።ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ካህናቱ ፡ ጸሎት ፡ ያደርጉና ፡ ጉዞ፡ ይጀመራል ። ጉዞውም ፡ ሲጀመር ፡ አዲሱ ፡ ስሙ ፡ የተጻፈበትን ፡ ሣንቃ ፡ አንድ ፡ ካህን ፤ አበባውን ፡ ደግሞ ፡ ሌላው ፡ ካህን ፡ ይዘው ፡ ይጓዛሉ ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አሥር ፡ ካህናቶች ፡ ሁለት ፡ ሁለቱ ፡ እየሆኑ ፡ እየዘመሩ ፡ ሬሳውን ፡ ይከተላሉ ። ወደ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ቅጥር ፡ ግቢ ፡ ሲደርሱ ፡ ሬሳውን ፡ አራት ፡ ሰዎች ፡ ተሸክመው ፡ አግብተው ፡ ያጋድሙታል ። ሚስቱና ፡ ዘመዶ

ቹም ፡ ተከትለው ፡ ይገባሉ ። ካህናቱም ፡ ዕጣን ፡ እያጠኑ ፡ ጸሎት ፤ ይጸልያሉ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ባለጠጋ ፡ ቢሆን ፡ በሸክላ ፡ ሣጥን ፤ ድሀ ፡ ቢሆን ፡ በእንጨት ፡ ሣጥን ፡ አድርገው ፡ ወደ ፡ ተቆፈረው ፡ መቃብር ፡ ያገቡታል ። የተቆፈረውም ፡ አፈር ፡ እስቲመለስና ፡ መሬቱ ፡ እስቲተካከል ፡ ድረስ ፡ ካህናቱ ፡ ግብዓተ ፡ መሬት ፡ ይደግማሉ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ቀባሪው ፡ ሁሉ ፡ ይበተንና ፡ ሚስቱ ፡ እንዳጌጠች ፡ ለብቻዋ ፡ ወደ ፡ ቤትዋ ፡ ትመለሳለች ።

የፍታቱ ፡ ገንዘብ ፡ ሚቹ ፡ ባለ ፡ ገንዘብ ፡ እንደ ፡ መሆኑ ፡ እየታየ ፡ ከሁለት ፡ ዬን ፡ እስከ ፡ አምሳ ፡ ዬን ፡(ከ፩ ብር ፡ እስከ ፡ ፳ ብር)ለካህናቱ ፡ ይሰጣል ።

የዚህም ፡ የአቀባበርና ፡ የፍታት ፡ ሥርዓት ፡ ከእኛ ፡ አገር ፡ የፍታት ፡ ሥርዓት ፡ ልዩነቱ ፡ በሶስት ፡ነገር ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በሌላው ፤ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ይመሳሰላል ።

መጀመሪያው ፡ ልዩነት ። በእኛ ፡ አገር፡ሰው፡ሲሞት፡ወዲያው ፡ሬሳው፡ ታጥቦ ፡ ዕለቱን፡ ይቀበራል ።በጃፓን ፡ አገር ፡ ግን ፡ ፵፰ ሰዓት ፡ ያቆዩታል።

፪ኛው ፡ ልዩነት ። በእኛ ፡ አገር ፡ ሚስቱና ፡ ዘመዶቹ፡ የሐዘን ፡ ልብስ፡ ይለብሳሉ ። በጃፓን ፡ አገር ፡ ግን ፡ የበዓልና የጌጥ ፡ ልብስ ፡ ለብሰው ፡ ያስቀብራሉ ።

፫ኛው ፡ ልዩነት ። በእኛ ፡ አገር ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ የሚጠራበት ፡ ስሙ ፡ የሚወጣለት ፡ ክርስትና ፡ በተነሣበት ፡ ቀን ፡ ነው ። በጃፓን ፡ አገር ፡ ግን ፡ በሞተበት ፡ ቀን ፡ ያወጡለታል ።

ይህ ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ የተጻፈው ፡ እንደ ፡ ቡዳሃ ፡ ሃይማኖት ፡ ሥርዓት ነው ። በሺንቶ ፡ ሃይማኖት ፡ ሥርዓት ፡ ግን ፡ የሺንቶ ፡ ካህናት ፡ ሬሳና፡ ቍስል ፡ የሚፈስ ፡ ደምም ፡ ሲያዩ ፤ አጥብቀው ፡ ይጸየፋሉ ። ሬሳም ፡ አሲዘው ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ሲሔዱ ፡ በሩቅ ፡ በሩቅ ፡ ሆነው ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ አይጠጉም ። ሬሳውንም ፡ በሸራይን ፡ ውስጥ ፡ አያገቡትም ። ይኸውም ፡ በብሉይ ፡ ዘመን ፡ የአሮን ፡ ልጆች ፡ ካህናቱና ፡ ሌዋውያኑ፡ ይኸን ፡ የመሰለውን ፤ ነገር ፡ ይጸየፉ ፡ እንደ ፡ ነበረው ፡ ነው ።

## ስምንተኛ ፡ ትልቅ ፡ ክፍል ።

### ስለ ፡ ጃፓኖች ፡ ሃይማኖት ፤ ስለ ፡ ሽንቶ ፡ ሃይማኖት ፤ ስለ ፡ ቡዳሃ ፡ ሃይማኖት ፤ ስለ ፡ ክርስቲያን ፡ ሃይማኖት ፤

### ምዕራፍ ፡ ፴፰ ።
### ስለ ፡ ጃፓኖች ፡ ሃይማኖት ።

ጃፓኖች ፡ ሃይማኖት ፡ የላቸውም ፡ አረማውያን ፡ ናቸው ፡ እየተባለ ፡ በንዳንድ ፡ ሰዎች ፡ አፍ ፡ ሲወራ ፡ እንሰማ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ አሁን ፡ ባይናችን ፡ እንዳየነው ፡ ሃይማኖት ፡ የላቸውም ፡ እየተባለ ፡ የሚወራው ፡ ወሬ ፡ እውነት ፡ አለመሆኑን ፡ ተረድተነዋል ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ ሶስት ፡ ዓይነት ፡ ሃይማኖት ፡ አለ ።

፩ኛው ፡ ሃይማኖት ፡ ሽንቶ ፡ ይባላል ።

ትርጓሜውም ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንገድ ፡ ማለት ፡ ነው ።

፪ኛው ፡ ሃይማኖት ፡ ቡዳሃ ፡ ይባላል ።

ትርጓሜውም ፡ እውቀትን ፡ የሚገልጽ ፡ ብርሃን ፡ ማለት ፡ ነው ።

፫ኛው ፡ ሃይማኖት ፡ ክርስቲያንነት ፡ ነው ።

ትርጓሜውም ፡ የክርስቶስ ፡ ወገን ፡ ማለት ፡ ነው ።

እንግዴህ ፡ የጃፓኖችን ፡ ሃይማኖት ፡ ነገር ፡ ከመጽሐፋቸው ፡ እንዳነበብሁትና ፡ ከቃላቸውም ፡ እንደ ፡ ሰማሁት ፡ አድርጌ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥዬ ፡ ጽፌዋለሁ ።

#### ፩ኛ ፡ ስለ ፡ ሽንቶ ፡ ሃይማኖት ።

የሽንቶ ፡ ሃይማኖት ፡ ለዘለዓለም ፡ በአምላክነቱ ፡ ጸንቶ ፡ ከሁሉ ፡ በላይ ፡ ሆኖ ፡ የሚኖር ፡ ዓለሙን ፡ ሁሉ ፡ የፈጠረ ፡ አንድ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ማመን ፡ ነው ።

ይኸውም ፡ ምንም ፡ በሕግና ፡ በሥርዓት ፡ ባይጋጠም ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ በማለት ፡ የእስራኤልን ፡ ሃይማኖት ፡ ይመስላል ።

#### ስለ ፡ ትንሣኤ ፡ ሙታን ፡ ነገር ።

ጃፓኖች ፡ ሰው ፡ ሲሞት ፡ ሥጋው ፡ ይፈርሳል ፡ ይበሰብሳል ። ነፍሱ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ፈጠራት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትመለሳለች ። ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ያኗኗሯን ፡ ነገር ፡ እግዚአብሔር ፡ ያውቃል ፡ እንጂ ፡ እኛ ፡ አናውቅም ፡ ይላሉ ።

ከዚህም ፡ በቀር ፡ ለሀገራቸው ፡ መልካም ፡ ሥራ ፡ ለሠሩት ፡ ነገሥታትና ፡ ትልልቅ ፡ ሰዎች ፡ የመታሰቢያ ፡ ቤት ፡ እየሠሩ ፡ ነፍሳቸው ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ በዚህ ፡ ትገለጣለች ፡ እያሉ ፡ ይሰግዱላቸዋል ።

ምሳሌ ። ጄኔራል ፡ ኖጊ ፡ የሚባለው ፡ ጃፓኖች ፡ በ፲፱፻፺፯ ፡ ዓ ፡ ም ፡ ከመስኮቦች ፡ ጋራ በተዋጉ ፡ ጊዜ ፡ የጦር ፡ አለቃ ፡ ሆኖ ፡ የተዋጋና ፡ ድል ፡ ያደረገ ፡ ነው ።

ሁለቱም ፡ ወንዶቹ ፡ ልጆቹ ፡ በዚያው ፡ በጦርነቱ ፡ ውስጥ ፡ ስለ ፡ ሞቱ ፤ ሁለቱም ፡ ልጆችህ ፡ ሞቱ ፡ ብለው ፡ ቢነግሩት ፡ ልጆቼ ፡ ስለ ፡ ጃፓን ፡ ነጻነት ፡ ቢሞቱ ፡ ሞቱብኝ ፡ ብዬ ፡ ለማዘን ፡ አይገባኝም ፡ ብሎ ፡ በወታደሮቹ ፡ ፊቱ ፡ የደስታ ፡ ቃል ፡ ተናግሮ ፡ ነበር ።

በኋላም ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂ ፡ በሞተ ፡ ጊዜ ፡ የጃፓንን ፡ ነጻነት ፡ እየጠበቀና ፡ እያጸና ፡ መልካም ፡ ሥራ ፡ የሠራላት ፡ ጌታዬና ፡ ንጉሤ ፡ ሲሞት ፡ እኔ ፡ በሕይወት ፡ መቆየት ፡ አይገባኝም ፡ ብሎ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂ ፡ ሬሳ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ሲሔድ ፡ እርሱና ፡ ሚስቱ ፡ ባንድ ፡ ቀን ፡ ራሳቸውን ፡ ገደሉ ። ስለዚህ ፡ በቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ ውስጥ ፡ መታሰቢያ ፡ ቤት ፡ ተሠርቶለት ፡ ይሰገድለታል ።

---

### በሸንቶ ፡ ሸራይን ፡ ስለሚጸለየው ፡ ጸሎት ።

በሸንቶ ፡ ሸራይን ፡ ሚራ ፡ የሚባል ፡ ክብ ፡ መስታወት ፡ የሚመስል ፡ ከነሐስ ፡ ወይም ፡ ከሌላ ፡ ማዕድን ፡ የተሠራ ፡ በመንበሩ ፡ ላይ ፡ ይቀመጣል ፡ እንጂ ፡ ሌላ ፡ ምስልም ፡ ሥዕልም ፡ ማስቀመጥ ፡ ክልክል ፡ ነው ።

በሸንቶ ፡ ሃይማኖት ፡ ጸንተው ፡ የሚኖሩ ፡ ጃፓኖች ፡ ወደ ፡ ሸራይን ፡ ገብተው ፡ ጸሎት ፡ ሲጀምሩ ፡ በመጀመሪያ ፡ ሶስት ፡ ጊዜ ፡ ያጨበጭባሉ ። ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ምንም ፡ ሳይናገሩና ፡ ድምጻቸውን ፡ ሳያሰሙ ፡ ለማግኘት ፡ የሚመኙትን ፡ በልባቸውና ፡ በአሳባቸው ፡ ብቻ ፡ (በለሆሳስ) ለእግዚአብሔር ፡ ያስታውቃሉ ።

እግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ ነውና ፡ ሳንናገር ፡ በልባችን ፡ የምንለምነውን ፡ ያውቃል ፡ ይላሉ ።

---

### ስለ ፡ አካል ፡ ጥራትና ፡ ስለ ፡ ልብ ፡ ንጽሕና ።

በሸንቶ ፡ ሃይማኖት ፡ የአካል ፡ ጥራትና ፡ የልብ ፡ ንጽሕና ፡ እንደ ፡ ሃይማኖት ፡ ይቆጠራል ። ስለዚህ ፡ ወደ ፡ ሸንቶ ፡ ሸራይን ፡ የሚገባ ፡ ሰው ፡

ሁሉ ፡ አስቀድሞ ፡ በሽራይኑ ፡ ቅጥር ፡ ግቢ ፡ ወደ ፡ ተጠራቀመው ፡ ውሀ ፡ ሔዶ ፡ እጆቹን ፡ ታጥቦ ፡ ያጠራል።ቀጥሎም፡ካህኑ፡በእጁ ፡ በያዘው ፡ ማራገቢያ ፡ነፋሱን ፡ ያነፍስለታል።ይህም፡አካሉንና፡ልቡን፡ለማንጻት፡ነው፡ይባላል ።

አፍንና ፡ እጅን ፡ ሳይታጠቡ ፡ ጸሎት ፡ መጸለይ ፡ አይገባም ፡ ይላሉ ።

ይህም ፡ በሲኖዶስ ፡ በዘቲ ፡ ሌሊት ፡ መንፈቀ ፡ ሌሊት ፡ ተንሢአከ ፡ ተሐጺበከ ፡ በማይ ፡ ጸሊ ። ወንፋሕ ፡ ውስተ ፡ እደዊከ፤ ወትከውን ፡ ንጹሐ ፡ እምርእስከ ፡ እስከ ፡ እገሪከ ፡ ካለው ፡ ጋራ ፡ የገጠመ ፡ ነው ።

የአካል ፡ ጥራት ፡ ማለት ፡ በመሔድም ፤ በመቀመጥም ፤ በመነሣትም ፡ በመተኛትም ፤ በሥራም ፤ በሌላውም ፡ ይህን ፡ በመሰለው ፡ ሁሉ ፡ በማናቸውም ፡ ጊዜ ፡ቢሆን ፡ አካልንና ፡ ልብስን ፡ እድፍ ፡ እንዳያገኘው ፡ መጠንቀቅ ፤ ቢያገኘውም ፡ በቶሎ ፡ በውሀ ፡ አጥቦ ፡ ንጹሕ ፡ ማድረግ ፡ ነው ።

የልብ ፡ ንጽሕና ፡ ማለት ፡ ዘወትር ፡ እውነትን ፡ ማሰብና ፡ መናገር ፤ እውነትንም ፡ መሥራት ፤ ውሳጣዊ ፡ ሰውነትንና ፡ ውሳጣዊ ፡ ሥራን ፡ ሁሉ ፡ በትክክል ፡ ማድረግ ፡ ነው ።

ምሳሌ ። አንድ ፡ ሰው ፡ በሌሊት ፡ ሔዶ ፡ የሌላውን ፡ ሰው ፡ ገንዘብ ፡ ለመስረቅ ፡ ቁርጥ ፡ አሳብ ፡ ካደረገ ፡ በኋላ ፡ ውሻ ፡ ይጮህብኛል፤ባለቤት ፡ ይነቃብኛል ፡ ብሎ ፡ ቢቀር ፡ የልብ ፡ ንጽሕና ፡ አይባልም ፤ ነገር ፡ግን፡ይህ፡ የማይገባ ፡ ሥራ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ አሳቡን፡አሸንፎ፡የቀረ ፡ እንደሆነ ፡ የልብ ፡ ንጽሕና ፡ ይባላል ።

ሁለተኛ ። የዝሙት ፡ ሥራ ፡ ለመሥራት ፡ ቁርጥ ፡ አሳብ ፡ ካደረገ ፡ በኋላ ፡ ባለቤቱ ፡ ደርሶ ፤ ቢቻለው ፡ ይገድለኛል ፤ ባይቻለው ፡ ለዳኛ ፡ ነግሮ ፡ ያስቀጣኛል ፡ ብሎ ፡ ቢቀር ፡ የልብ ፡ ንጽሕና ፡ አይባልም ። ነገር ፡ ግን ፡ ይህ ፡ የማይገባ ፡ ሥራ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ አሳቡን ፡ አሸንፎ ፡ የቀረ ፡ እንደሆነ ፡ የልብ ፡ ንጽሕና ፡ ይባላል ።

በማናቸውም ፡ ቢሆን ፡ የልብ ፡ ንጽሕና ፡ ማለት ፡ በእውነት ፡ ነገር ፡ ይሉኝታ ፡ አለማድረግ ፡ ነው ።

ይህም ፡ ብፁዓን ፡ ንጹሐነ ፡ ልብ፤ እስመ ፡ እሙንቱ ፡ ይሬእይዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ከተባለው ፡ ከወንጌል ፡ ቃል ፡ ጋራ ፡ የገጠመ ፡ ነው ።

## ፪ኛ ፡ ስለ ፡ ቡዳሃ ፡ ሃይማኖት ።

የቡዳሃ ፡ አባት ፡ ሱድሆድህና ፡ ይባላል ። ይኸውም ፡ በካፒላባስቱ ፡ አጠገብ ፡ ያለች ፡ የኒፓል ፡ ወሰነተኛ ፡ የምትሆን ፡ የሻክያ ፡ ንጉሥ ፡ ነው ። እነዚሁም ፡ የፀሐይ ፡ ልጆች ፡ ነን ፡ እያሉ ፡ የሚያወሩ ፡ ናቸው ።

ቡዳሃ ፡ ከክርስቶስ ፡ ልደት ፡ በፊት ፡ በ፮፻፳፫ ፡ ዓመት ፡ በኒፓል ፡ አ ጠገብ ፡ ባለች ፡ ሉምቢኒ ፡ በምትባል ፡ አገር ፡ ተወለደ ። ስሙም ፡ ቡዳሃ ፡ እስቲባል ፡ ጉተማ ፡ ይባል ፡ ነበር ። አባቱም ፡ በጥንቃቄ ፡ አሳደገው ። ለ ትምሕርትም ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ እንዳይወጣና ፡ ባይኑ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ እንዳያይ ፤ በጆሮውም ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ እንዳይሰማ ፡ ብሎ ፡ በቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ግቢ ፡ አስተማሪ፡አግብቶ ፡ እንዲማር ፡ አደረገ ። ፈረስ ፡ መጋ ለብና ፡ ማደንም ፡ በዚያው ፡ በቅጥር ፡ ግቢ ፡ ባለው ፡ ሜዳና ፡ ዱር ፡ ተማ ረ ። እድሜውም ፡ ፲፱ ፡ ዓመት ፡ ሲሆን ፡ ያክስቱን ፡ ልጅ ፡ ያሶድሐራ ፡ የ ምትባለውን ፡ አገባ ። ዘወትርም ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ያደርግ ፡ ነበር ። አባ ቱ ፡ ከሚገዛው ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ቆንጃጅት ፡ ሴቶች ፡ እያስመረጠ፡እያመጣ፡ ሲያዘፍንለትና ፡ ሲያስጨፍርለት ፡ ሙዚቃና ፡ መሰንቆም ፡ ሲያስመታለት፡ ይውል ፡ ነበር።ወደ ፡ ውጭ ፡ ለመውጣት ፡ ግን ፡ አይፈቀድለትም ፡ ነበር። ምክንያቱም ፡ ልጁ ፡ በድንገት ፡ አንድ ፡ የሚያሳዝን ፡ ነገር ፡ እንዳያይ ፤ ዘወ ትር ፡ ደስ ፡ እንደ ፡ አለው ፡ ብቻ ፡ እንዲኖር ፡ ነበር ።

ነገር ፡ ግን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ የተወሰነውንና ፡ የተቆረጠውን ፡ ሰው፡ በጥበቡ ፡ ሊያስቀረው ፡ አይችልምና ፡ ጉተማ ፡ (ቡዳሃ)ወደ ፡ ውጭ ፡ ለመ ውጣት ፡ ቁርጥ ፡ አሳብ ፡ አደረገና፡ለአባቱ ፡ አስታወቀው ። አባቱም ፡ የል ጁን ፡ አሳብ ፡ ለማሸነፍ ፡ ስላልቻለ ፡ በክብር ፡ ሆኖ ፡ እንዲወጣ ፡ የወርቅ ፡ ሠረገላና ፡ ተከታዮቹ ፡ እንዲዘጋጁ ፡ አዘዘለት ።

እርሱም ፡ ባራት ፡ ፈረሶች ፡ በሚሳብ ፡ የወርቅ ፡ ሠረገላ ፡ ተቀምጦ ፡ የተመዘዘ ፡ ሰይፍ ፡ የያዙ ፡ አሽከሮች ፡ በፊት ፡ በፊቱ፡እየሔዱ ፡ የንጉሡ፡ ልጅ፡ጉተማ፡መሆኑን ፡ እየተናገሩ ፡ መንገደኛውን ፡ ሁሉ ፡ እያስለቀቁለት ባማረ ፡ አጀብ ፡ ታጅቦ ፡ ባለ ፡ ወርቅ ፡ መርገፍ ፡ ጃንጥላ፡(ድባብ) ፡ ተይዞለ ት፡ ሲሔድ ፡ በመንገዱ ፡ ዳር ፡ እጁና ፡ እግሩ ፡ እየተንቀጠቀጠ ፡ ልብሱን፡ መልበስ ፤ ምራቁን ፡ መሰብሰብ ፡ ያቃተውና ፡ ጥርሶቹ ፡ የወላለቁ ፤ ሥጋ ው ፡ አልቆ ፡ አጥንቱና ፡ ጅማቱ ፡ ተለይቶ ፡ የሚታይ ፤ የራሱ ፡ ጠጉር ፡ ጥጥ ፡ የመሰለና ፡ ወገቡ ፡ ጎብጦ ፡ በበትር ፡ ተመርኲዞ ፡ እየተሳበ ፡ የሚ ሔድ ፡ አንድ ፡ ሽማግሌ ፡ ሰው ፡ አይቶ ፡ ነጂውን ፡ ሠረገላውን ፡ አቁም ፡ ብሎ ፡ ይህ ፡ ምንድነው ፡ እያለ ፡ ይጠይቅ ፡ ጀመር ።

ነጂውም ፡ በእድሜ ፡ ያረጀ ፡ ሰው ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ። በእድ ሜ ፡ ያረጀ ፡ ማለት ፡ ምን ፡ ማለት ፡ ነው ፡ ቢለው ፡ ኃይሉ ፡ የደከመ ፤ እ ውቀቱ ፡ የጠፋ ፤ ለሞት ፡ የቀረበ ፡ ማለት ፡ ነው ፡ አለው ።

ይህ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ ነውን ፡ አለው ።

አዎን ፡ የፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ እድልና ፡ ዕጣ ፡ እንደዚህ፡ ነውና ። ሰው፡ ሆኖ ፡ የማያረጅ ፡ የለም ፡ አለው ። ጉተማም ፡(ቡዳሃ)ይህን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ፡ እያዘነ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ተመለሰ ።

ደግሞ ፡ በሌላ ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ፊተኛው ፡ ባጀብና ፡ በክብር ፡ ሆኖ ፡ ሲ ወጣ ፡ በመንገዱ ፡ ዳር ፡ በቁስለ ፡ ሥጋ ፡ የተጨማለቀና ፡ የወደቀ ፤ ከእ ግርና ፡ ከእጁ ፡ የደም ፡ ዝናም ፡ እየዘነመ ፡ ልብሱን ፡ መልበስ ፡ ያቃተው፤ ባጠገቡም ፡ ረዳት ፡ የሌለው ፡ አንድ ፡ ድሀ ፡ በሽተኛ ፡ አይቶ ፡ ይህ፡ ደግሞ ፡ ምንድነው ፡ ብሎ ፡ ሠረገላ ፡ ነጂውን ፡ ቢጠይቅ ፡ በሽተኛ ፡ ሰው፡ ነው ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ።

ይህም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ ነውን ፡ ቢለው ፤ አዎን ፡ የፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ እድልና ፡ ዕጣ ፡ እንደዜህ ፡ ነውና ፡ የበሽታው ፡ ዓይነት ፡ ይለዋወ ጥ ፡ እንጂ ፡ ሰው ፡ ሆኖ ፡ የማይታመም ፡ የለም ፡ አለው ። ይህንም ፡ በማ የቱ ፡ እያዘነ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ተመለሰ ።

ደግሞ ፡ ሶስተኛ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ፊተኛው ፡ ባጀብና ፡ በክብር ፡ ሆኖ ፡ ሲወጣ ፡ በመገዱ ፡ ዳር ፡ ግምጃ ፡ የለበሰ ፡ ቃሬዛ ፡ ተሸክመው ፤ በቀኝና፡ በግራ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ እያለቀሱና ፡ እየጮሁ ፡ ሲሔዱ ፡ አይቶ ፡ ይህ ፡ ደ ግሞ ፡ ምንድነው ፡ ብሎ ፡ ቢጠይቅ ፡ የሞተ ፡ ሰው ፡ ነው ፡ ወደ ፡ መቃብ ር ፡ ይወስዱታል ፡ ብሎ ፡ ነገረው ። የሞተ ፡ ማለት ፡ ምን ፡ ማለት ፡ ነው፡ ብሎ ፡ ቢጠይቅ ፤ ከዘመድ ፡ ከወዳጅ ፡ የተለየ ፤ ሁለተኛ ፡ መናገርና ፡ መስማት ፡ ማየት ፡ የማይችል ፤ እንደ ፡ ድንጋይ ፡ የደረቀና ፡ እንደ ፡ ዛፍ፡ የተቆረጠ ፤ እንደ ፡ ግንብ ፡ የተናደ ፤ እንደ ፡ ቅጠል ፡ የረገፈ ፡ ሆኖ ፡ የሚቀር ፤ ተመልሶም፤ወደ ፡ ዓለም ፡ የማይመጣ ፡ ማለት ፡ ነው ፡ አለው ።

ይህም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ ነውን ፡ ቢለው ፡ አዎን ፡ የፍጥረ ት፡ሁሉ፡እድልና ፡ዕጣ፡ እንደዚህ ፡ ነውና ፡ሰው፡ ሆኖ ፡ የማይሞት ፡ የለም ፡ አለው ። ከዜህም ፡ በኋላ ፡ እያዘነ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ተመለሰ ።

በሌላ ፡ ቀን ፡ ደግሞ ፡ አራተኛ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ፊተኛው ፡ ባጀብ ና ፡ በክብር ፡ ሆኖ ፡ ሲወጣ ፡ በመንገዱ ፡ ዳር ፡ ሰውነቱን ፡ የጠበቀና ፡ አሳቡን ፡ የሰበሰበ ፤ ወደ ፡ ቀኝም ፡ ወደ ፡ ግራም ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ የማ ያይ ፡ የመለመኛ ፡ አኩፋዳና ፡(ከረጢት)በትር ፡ ብቻ ፡ ይዞ ፡ የቆመ ፡

ሰው ፡ አይቶ ፡ ይህ ፡ ደግሞ ፡ ምንድነው ፡ ብሎ ፡ ቢጠይቅ ፡ የብራሃማ ፡ መነኩሴ ፡ ነው ፡ አለው ።

መነኩሴ ፡ ማለት ፡ ምን ፡ ማለት ፡ ቢለው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ገብቶ ፡ ሰውነቱን ፡ ሁሉ ፡ ለመልካም ፡ ሥራ ፡ አሳልፎ ፡ የሰጠ ፤ ከዘመዱና ፡ ከወዳጁ ፡ ከሥጋዊ ፡ ፈቃዱም ፡ የተለየ ፤ ለሰው ፡ ሁሉ ፡ የሚራራና ፡ የሚያዝን ፤ በማንም ፡ ላይ ፡ ጉዳት ፡ እንዲመጣ ፡ የማያስብ ፡ ማለት ፡ ነው ፡ አለው ።

ጉተማም ፡(ቡዳሃ)የእነዚያ ፡ በፊት ፡ ያያቸው ፡ የሶስቱ ፡ ሰዎች ፡ ኑሮ ፡ ልቡን ፡ አሳዝኖትና ፡ አሰቅቆት ፡ ስለ ፡ ነበረ ፤ አሁን ፡ የብራሃማን ፡ መነኩሴ ፡ ኑሮ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ልቤን ፡ ለማሳረፍ ፡ ከዜህ ፡ የተሻለ ፡ ኑሮ ፡ ለማግኘት ፡ አልችልምና ፡ እንደዜህ ፡ መነኩሴ ፡ ሆኜ ፡ እኖራለሁ ፡ በማለት ፡ ሐሳቡን ፡ ቆርጦ ፡ በደስታ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ተመለሰ ።

ወደ ፡ ቤቱም ፡ ውስጥ ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ሚስቱ ፡ ከወንበር ፡ ተነሥታ ፡ ቆማ ፡ ልቡን ፡ ደስ ፡ ያሰኘሁ ፡ መስፍንትት ፡ አንተን ፡ የወለዱ ፡ አባትና ፡ እናት ፡ የታደሉ ፡ ናቸው ፤ የአንተ ፡ ሚስትም ፡ የሆንሁ፡እኔ ፡ የታደልሁ ፡ ነኝ ፡ እያለች ፡ ትናገር ፡ ጀመረች ። እርሱ ፡ ግን ፡ እናንተስ ፡ እኔን ፡ በማግኘታችሁ ፡ የታደላችሁ ፡ ሆናችሁ ። እኔ ፡ ግን ፡ የታደልሁ ፡ የምሆነው ፡ የልቤን ፡ ምኞት ፡ ያገኘሁ ፡ እንደሆነ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ስለ ፡ ተናገረ ፡ ሚስቱ ፡ በጣም ፡ ደነገጠች ።

ይህንም ፡ የምንኩስና ፡ አሳቡን ፡ ለአባቱና ፡ ለእናቱ ፡ በዘወርዋራ ፡ መንገድ ፡ እያደረገ ፡ ቢነግራቸው ፡ የማይፈቅዱለት ፡ መሆኑን ፡ ስለ ፡ ተረዳው ፡ በሌሊት ፡ ተሠርቆ ፡ ለመሔድ ፡ ቁርጥ ፡ አሳብ ፡ አደረገ ።

ነገር ፡ ግን ፡ በዚያ ፡ ወራት ፡ አንድ ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ተወልዶለት ፡ ነበርና ፡ የእርሱ ፡ ነገር ፡ እጅግ ፡ አስጨነቀው ። ቢሆንም ፡ ልቡ ፡ በምንኩስናው ፡ ቆርጧልና ፡ አሳቡን ፡ ለመለወጥ ፡ አልቻለም ። ስለዚህ ፡ ልጁን ፡ ስሞ ፡ ለመሰናበት ፡ ብቻ ፡ ወደ ፡ መኝታ ፡ ቤት ፡ ቢገባ ፡ እናቲቱ ፡ በልጁ ፡ ላይ ፡ እጅዋን ፡ ጣል ፡ አድርጋበት ፡ ተኝታ ፡ አየና ፡ እጅዋን ፡ አንሥቼ ፡ ልጄን ፡ ስስም ፡ እርስዋ ፡ ትቀሰቀስና ፡ ታስቸግረኛለች ፡ ብሎ ፡ ሳይስመው ፡ ጥሎት ፡ ሔደ ።

በደጅም ፡ አሽከሩ ፡ ሁለት ፡ ፈረሶች ፡ ጭኖ ፡ ይጠብቀው ፡ ነበርና ፡ በፈረሱ ፡ ተቀምጦ ፡ አሽከሩን ፡ አስከትሎ ፡ እንደሚቻለው ፡ እስቲነጋ ፡ ድረስ ፡ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ ሲጋልብ ፡ አድሮ ፡ ጧት ፡ አሽከሩን ፡ ከፈረሱ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ መልሶ ፡ እርሱ ፡ ብቻውን ፡ ሔደ ።

በዚያም ፡ ዘመን ፡ የነገሥታት ፡ ልጆች ፡ ጠጉራቸውን ፡ ያሳድጉ ፡ ነበርና ፡ ያደገውን ፡ ጠጉሩን ፡ በሰይፉ ፡ ቆርጦ ፡ ጣለ ። ልብሱንም ፡ ሁሉ ፡ ለነዳያን ፡ እየመጸወተ ፡ ጨርሶ ፡ የብራሃማ ፡ መነኮሳት ፡ በሚኖሩበት ፡ ቢናሬስ ፡ በሚባል ፡ ገዳም ፡ ገብቶ ፡ እየተማረ ፡ ተቀመጠ ።

ይኸውም ፡ የተደረገው ፡ በተወለደ ፡ በ፳፱ዓመቱ ፡ ከክርስቶስ፡ልደት፡ በፊት ፡ ፭፻፴፬ ፡ ዓመት ፡ ነው ። ከቢናሬስም ፡ ወጥቶ ፡ ነፍሱ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ አሳብ ፡ የምታርፍበትን ፡ ሥራ ፡ ለመፈለግ ፡ ካንዱ ፡ ስፍራ ፡ ወደ ፡ ሌላው ፡ ስፍራ ፡ ሲዛወር ፡ ጋያ ፡ በሚባል ፡ ከተማ ፡ አጠገብ ፡ ኒራንጃን ፡ በሚባል ፡ ወንዝ ፡ ዳር ፡ ብቻውን፡ለመኖርና ፡ የነፍሱን ፡ ዕረፍት፡ ለማግኘት ፡ ቁርጥ ፡ አሳብ ፡ አደረገ ። በዚያም ፡ ፫ ድሆች ፡ ሰዎች ፡ መጥተው ፡ ባንድነት ፡ ለመኖር ፡ ተቀላቀሉት ፤ በዚያም ፡ በጾምና ፡ በሌላም፡ ሥራ ፡ ሰውነቱን ፡ እያደከመ ፡ የቀርከሃ ፡ ሥር ፡ ብቻ ፡ እየበላ ፡ ፮ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ።

ዋናውም ፡ አሳቡ ፡ ራሱንና ፡ ሌሎቹንም ፡ ሰዎች ፡ ከችግርና ፡ ከጭንቀት ፡ የሚያድንበትን ፡ ነገር ፡ ለማግኘት ፡ ነበር ። ከ፮ዓመትም ፡ በኋላ፡ ሰውን ፡ ወደ ፡ ችግርና ፡ ወደ ፡ ጭንቀት ፡ ወጥመድ ፡ የሚያገቡ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ያሉት ፡ ሶስት ፡ ነገሮች ፡ ሆነው ፡ አገኛቸው ።

፩ኛ ፡ ሥጋዊነት ።

፪ኛ ፡ ጠማምነት ።

፫ኛ ፡ ድንቆርነት ።

ትርጓሜ ።

ሥጋዊነት ፡ ማለት ። መብላትንና ፡ መጠጣትን ፡ ዝሙትን ፤ ሹመትንና ፡ ክብረትን ፤ ይህንም ፡ የመሰለውን ፡ ሁሉ ፡ መፈለግና ፡ በጠቅላላው ፡ በቃኝ፡ አለማለት ፡ ነው ።

ጠማምነት ፡ ማለት ። ሲቻለውና ፡ ሲመቸው ፡ ለሰው ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ አለማድረግ ፤ ሌላም ፡ ሰው ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ እንዳያደርግ ፡ ማሰናከል ። ይህንም ፡ የመሰለውን ፡ የክፋት ፡ ሥራ ፡ መሥራትና ፡ በጠቅላላው፡ የመልካም ፡ ሥራ ፡ ተቃዋሚ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ድንቆርነት ፡ ማለት ። ራሱ ፡ ተመራምሮ ፡ መልካሙንና ፡ ክፉውን ፡ አለማወቅ ፡ ሌላውም ፡ ሰው ፡ ቢነግረውና ፡ ቢያስተምረው ፡ አለመቀበል ። ይህንም ፡ የመሰለውን ፡ አለማድረግና ፡ በጠቅላላው ፡ አስበም ፡ ተመክሮም ፡ ሥራ ፡ ለመሥራት ፡ አለመውደድ ፡ ነው ።

ቡዳሃም ፤ ሰውን ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ወደ ፡ ችግርና ፡ ወደ ፡ ጭንቀት ፡ ወጥመድ ፡ የሚያገቡ ፡ እነዚህ ፡ ሶስት ፡ ነገሮች ፡ መሆናቸውን ፡ ከተረዳው ፡ በኋላ ፡ ራሱና ፡ ሌሎቹም ፡ ሰዎች ፡ ከነዚህ ፡ ከሶስቱ ፡ ነገሮች ፡ የሚያመ ልጡበትን ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ የተጻፉትን ፡ ሶስት ፡ ነገሮች ፡ አገኘ ፡፡

፩ኛ ፡ ራስን ፡ መግዛትና ፡ መቆጣጠር ፡፡

፪ኛ ፡ ደግነት ፡፡

፫ኛ ፡ አስታዋይነት ፡፡

## ትርጓሜ ፡፡

ራስን ፡ መግዛትና ፡ መቆጣጠር ፡ ማለት ፡፡ ዓይን ፡ ያየውን ፡ ሁሉ ፡ ልብ ፡ ለማግኘትና ፡ ለመሥራት ፡ ሲያስብ ፤ አሳብን ፡ ማሸነፍና ፡ መተው ፤ በጠቅላላውም ፡ በቃኝ ፡ ማለት ፡ ነው ፡፡

ደግነት ፡ ማለት ፡፡ ገንዘብ ፡ ለቸገረው ፡ ገንዘብ ፤ ትምሕርት ፡ ለቸገ ረው ፡ ትምሕርት ፤ ምክር ፡ ለቸገረው ፡ ምክር ፡ መስጠትና ፡ በጠቅላላው ለተቸገረው ፡ ሁሉ ፡ መራራት ፡ ነው ፡፡

አስታዋይነት ፡ ማለት ፡፡ ባይኑ ፡ አይቶ ፡ በልቡ ፡ አስቦና ፡ ተመራ ምሮ ፡ መሥራት ፤ ራሱም ፡ አስቦ ፡ መሥራት ፤ ባይችል ፡ ሰው ፡ የነገ ረውንና ፡ ያስተማረውን ፡ እየተቀበለ ፡ መሥራት ፤ በጠቅላላውም ፡ ደግና ፡ ክፉን ፡ አውቆና ፡ ለይቶ ፡ መሥራት ፡ ነው ፡፡

እነዚህንም ፡ ሶስቱን ፡ ነገሮች ፤ በ፰ ወገን ፡ አስፋፍቶ ፡ አስተምሯቸዋል ፡፡

፩ኛ ፡ በሥራ ፡ ሁሉ ፡ መታመን ፡፡

፪ኛ ፡ በሥራ ፡ ሁሉ ፡ ቅን ፡ መሆን ፡፡

፫ኛ ፡ እውነተኛ ፡ መሆን ፡፡

፬ኛ ፡ ጠባየ ፡ መልካም ፡ መሆን ፡፡

፭ኛ ፡ እውነተኛውን ፡ ነገር ፡ ይዞ ፡ መቆየት ፡፡

፮ኛ ፡ በእውነት ፡ ነገር ፡ መበርታትና ፡ ይሉኝታ ፡ አለማድረግ ፡፡

፯ኛ ፡ ለእውነት ፡ ነገር ፡ መቅናትና ፡ መትጋት ፡፡

፰ኛ ፡ ያንድነት ፡ ኃይል ፡ ማድረግ ፡ ይገባል ፡ ይል ፡ ነበር ፡፡

ቡዳሃ ፡ ለልቡ ፡ ዕረፍት ፡ የሚሰጠውን ፡ ይህን ፡ መሠረት ፡ ከ መሠረተ ፡ በኋላ ፡ የምንኲስና ፡ ሥራ ፡ ይዞ ፡ ራሱን ፡ ብቻ ፡ ጠቅሞ ፡ ለመኖር ፡ አላሰበም ፡ ነበርና ፡ በየአገሩ ፡ እየተዛውረ ፡ ያስተምር ፡ ጀመር ፡፡ ወሬውም ፡ በየአገሩ ፡ ሁሉ ፡ በተሰማ ፡ ጊዜ ፡ ነገሥታቱም ፡ እንኳ ፡ ሳይ ቀሩ ፡ እየመጡ ፡ ትምሕርቱን ፡ ይሰሙ ፡ ጀመር ፡፡ ያባቱንም ፡ ገናንነት ፡

የሚያውቁ ፡ አንዳንዱ ፡ ነገሥታት ፡ ምንኩስናውን ፡ ትቶ ፡ ወደ ፡ አባቱ ፡ እንዲመለስ ፡ ይመክሩት ፡ ነበር ። እርሱ ፡ ግን ፡ ምክራቸውን ፡ አልተቀበላቸውም ።

የቡዳሃ ፤ የቤት ፡ ዘመድ ፡ ስሙ ፡ ሲድሐርትሀ ፡ የመጠሪያም ፡ ስሙ ፡ ጉተማ ፡ ነበር ። በኋላ ፡ ግን ፡ ይህን ፡ የመሰለውን ፡ የሰውን ፡ ልብ ፡ የሚያሳርፍ ፡ ትምሕርት ፡ በማስተማሩ ፡ ብዙ ፡ መነኮሳት ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ተሰብስበው ፡ ነበርና ፡ ትምሕርቱ ፡ ወደ ፡ ልባቸው ፡ ስለ ፡ ገባና ፡ ደስ ፡ ስለ ፡ አሰኛቸው ፡ ቡዳሃ ፡ የሚባል ፡ ስም ፡ አወጡለት ።

ትርጓሜውም ። ለሰው ፡ እውቀትን ፡ የሚገልጽ ፡ ብርሃን ፡ ማለት ፡ ነው ። ትምሕርቱንም ፡ እየሰሙ ፡ በምንኩስና ፡ ኑሮ ፡ ለመኖር ፡ የወደዱ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ አስቄጥሶች ፡ ተባሉ ። ትርጓሜውም ፡ መናንያን ፡ ማለት ፡ ነው ።

ለነዚሁም ፡ ለአስቄጥሶቹ ፡ የመኖሪያቸውን ፡ ሕግ ፡ መጀመሪያ ፡ እርሱ ፡ በመሥራት ፡ እያሳየ ፡ መነኮሳቱም ፡ እንዲሠሩት ፡ ወሰነላቸው ።

---

## ቡዳሃ ፡ ለየመነኮሳቱ ፡ የሰጣቸው ፡ ደምብ ።

### አንደኛ ።

አትስረቁ ። አትግደሉ ። ሐሰት ፡ አትናገሩ ። አትሴስኑ ። አትስከሩ ። የተወሰነው ፡ ሰዓት ፡ ሳይደርስ ፡ አትብሉ ። ጌጠኛና ፤ ሽቱ ፡ የተቀባ ፡ ልብስ ፡ አትልበሱ ። በአልጋ ፡ ላይና ፡ በምቹ ፡ ስፍራ ፡ አትተኙ ። አትጨፍሩ ፤ በሙዚቃ ፡ አትዝፈኑ ። ከዓለማዊ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ራቁ ። ወርቅና ፡ ብር ፡ በቤታችሁ ፡ አታስቀምጡ ። ከእለት ፡ ምግብ ፡ በቀር ፡ ወርቅና ፡ ብር ፡ ከማንም ፡ አትቀበሉ ።

### ሁለተኛ ።

ከሌላ ፡ ሰው ፡ ሃይማኖት ፡ የእኛ ፡ ሃይማኖት ፡ ይበልጣል ፡ አትበሉ ። የሌላውንም ፡ ሃይማኖት ፡ አትስደቡ ።

### ሶስተኛ ።

በራሳችሁ ፡ አትታመኑ ። ተጠራጣሪዎችም ፡ አትሁኑ ። ፈንጠዚያ ፡ አታድርጉ ። ምኞት ፡ አታብዙ ። አትቆጡ ። በሥራችሁ ፡ አትመኩ ። ከሞት ፡ በኋላ ፤ እንደ ፡ ምድራዊ ፡ ኑሮ ፡ እንኖራለን ፡ አትበሉ ። አትኩሩ ። አትታበዩ ። ቂሎች ፡ ( ሞኞች ) አትሁኑ ።

### አራተኛ ።

ለተቸገረ ፡ ሁሉ ፡ እርዱ ። ዘወትር ፡ መልካም ፡ ሥራ ፡ ሥሩ ። ታገሡ ። ቃላችሁ ፡ አንድ ፡ ይሁን ። ዋጋ ፡ እናገኛለን ፡ ሳትሉ ፡ ሥሩ ። ጥበብን ፡

እሹ ። እውነተኞች ፡ ሁኑ ። መልካሙን ፡ አሳባችሁን ፡ አትለዋወጡ ። ተፋቀሩ ። ቸር ፡ ሁኑ ።

አምስተኛ ።

በእግር ፡ ሒዱ ። በትርና ፡ የመለመኛ ፡ አኰፋዳ ፡ ( ከረጢት ) ያዙ ። ለምናችሁ ፡ ያገኛችሁትን ፡ ብሉ ፡ እንጂ ፡ ለነገ ፡ ብላችሁ ፡ ትርፍ ፡ አታስቀምጡ ። ፀሐይ ፡ ሳትወጣ ፡ ተነሥታችሁ ፡ ታጠቡና ፡ የምትሠሩትን ፡ አስቡ ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በፍሬና ፡ በቂጣ ፡ ቢገኝ ፡ ከወተት ፡ ጋራ ፤ ባይገኝ ፡ ከውሀ ፡ ጋራ ፡ አፋችሁን ፡ አሟሹ ፡ ( ቁርስ ፡ አድርጉ ) በቀን ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ብቻ ፡ ብሉ ። ያውም ፡ በ፩ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ይሁን ። ጥላ ፡ ከዞረ ፡ በኋላ ፡ ምንም ፡ አትቅመሱ ። ( የጧት ፡ ጥላ ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡ ነው ። ከ፮ሰዓት ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ጥላ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ይዞራልና ፡ ከ፮ሰዓት ፡ በኋላ ፤ አትብሉ ፡ ማለቱ ፡ ነው ) ነገር ፡ ግን ፡ ሰውነቱ ፡ የደከመ ፡ ወይም ፡ የታመመ ፡ የሆነ ፡ እንደሆነ ፡ ከ፮ሰዓት ፡ በኋላ ፡ ጥቂት ፡ ፍሬና ፡ እንጀራ ፡ ይብላ ። በበዓል ፡ ቀን ፡ ግን ፡ ሁላችሁም ፡ ወደ ፡ ማታ ፡ ጥቂት ፡ ፍሬና ፡ እንጀራ ፡ ብሉ ።

ስድስተኛ ።

በልመና ፡ የተገኘው ፡ ማናቸውም ፡ ምግብ ፡ ባንድነት ፡ ተቀላቅሎ ፡ አለቃውም ፡ ማኅበሩም ፡ ሁላችሁም ፡ ትክክል ፡ ብሉ ፡ እንጂ ፡ ለአለቃችሁ ፡ ልዩ ፡ ምግብ ፡ አታዘጋጁ ።

በመብል ፡ ላይ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ አትቆዩ ። ከበላችሁ ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ወራቱ ፡ አኳሆን ፡ ጥቂት ፡ አርፋችሁ ፡ ሥራችሁን ፡ እያሰባችሁ ፡ ሥሩ ።

(እንደ ፡ ወራቱ ፡ አኳሆን ፡ ማለት ፡ በሙቀት ፡ ወራትና ፡ በብርድ ፡ ወራት ፡ የማረፊያው ፡ ሥፍራና ፡ የሚደረገው ፡ እረፍት ፡ ለየብቻ ፡ ስለሆነ ፡ ነው ።)

ከዕረፍት ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ማኅበር ፡ ለመሆን ፡ ወይም ፡ ማኅበሩን ፡ ለማየት ፡ ከሩቅ ፡ አገር ፡ የሚመጡትን ፡ እየተቀበላችሁ ፡ እውነተኛውን ፡ መንገድ ፡ አስተምሯቸው ። ማኅበሩንም ፡ ለማየት ፡ የሚመጡትን ፡ ሁሉ ፡ አስተካክላችሁ ፡ ተቀበሏቸው ፡ እንጂ ፡ ይህ ፡ ጌታ ፡ ነው ፡ ይህ ፡ ድሀ ፡ ነው ፡ ብላችሁ ፡ አታድሉ ።

---

## ስለ ፡ ቡዳሃ ፡ ሃይማኖት ፡ ትምሕርት ።

ቡዳሃ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በዚህ ፡ ዓለምና ፡ በሚመጣው ፡ ዓለም ፡ ከጭንቀትና ፡ ከመከራ ፡ የሚድንበትንና ፡ በደስታ ፡ የሚኖርበትን ፡ ኢስተማረ።

እንጂ ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስለ፡አንድነቱ፡ወይም፡ ስለ፡ሶስትነቱ ፡ ምንም፡ አላስተማረም ፤ ስለሚመጣውም ፡ ዓለም ፡ ሕይወትና ፡ ደስታ ፡ ትምሕርቱ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ እንደተጻፈው ፡ ነው ።

ሰው ፡ ምንም ፡ ቢማር ፡ ባንድ ፡ ጊዜና ፡ በቶሎ ፡ ከኃጢአት ፡ ንጹሕ፡ ለመሆን ፡ አይችልምና ፡ ኔርባንን ፡ እስኪያልፍ ፡ ድረስ ፡ ነፍሱ ፡ ሁለተኛ ፡ መወለድ ፡ያስፈልጋታል ፡ (ኔርባን ፡ ማለት ፡ የሰው ፡ ነፍስ ፡ ከኃጢአት ፡ ሁሉ ፡ በጭራሽ ፡ ንጽሕት ፡ የምትሆንበት ፡ ጊዜ ፡ ነው ።)

ስለዚህ ፡ ሰው ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ ነፍሱ ፡ እንደገና ፡ ተመልሳ ፡ ባንድ ፡ በሌላ ፡ ፍጥረት ፡ ገብታ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ትወለድና ፡ ያለፈውን ፡ የኃጢአቷ ን ፡ ደመወዝ ፡ እየተቀበለች ፡ ወደፊት ፡ የተሻለ ፡ መልካም ፡ ሥራ ፡ እየሠ ራች ፡ ትኖራለች ። ያም ፡ የገባችበት ፡ ፍጥረት ፡ የሞተ ፡ እንደሆነ ፡ እን ደገና ፡ ተመልሳ ፡ በሌላ ፡ ፍጥረት ፡ ገብታ ፡ የመልካም ፡ ሥራዋን ፡ እያሻ ሻለች ፡ ትሠራለች፡እንዲህም፡እየተመላለሰችና፡እየተወለደች፡ከኃጢአት፡ ሁሉ ፡ ፈጽማ ፡ ንጽሕት ፡ ስትሆን ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ አሳብ ፡ ሁሉ ፡ ነፃ ፡ ወ ጥታ ፡ በዕረፍትና ፡ በሰላም ፡ በደስታና ፡ በሕይወት ፡ ትኖራለች ። ኔርባን ን ፡ አለፈች ፡ ማለት ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ ነው ።

የኔርባን ፡ ዋና ፡ ትርጓሜ፡ ሥጋዊ ፡ አሳብና ፡ ሥጋዊ፡ኑሮ፡ማለት ፡ ነው ።

ይኸውም ፡ ወርቅ ፡ በእሳት ፡ እየተፈተነ ፡ እንዲጠራ ፡ ነፍስም ፡ በመ ከራ ፡ እየተፈተነች ፡ ከኃጢአት ፡ ሁሉ ፡ ትነፃለች ። ሥጋ ፡ ግን ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ አይነሣም ፡ ብሎ ፡ አስተምሯል ።

ስለ ፡ ኔርባን ፡ ነገር ። ያገራችን ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሊቃውንት ፡ ሰው ፡ ከ ሞተ ፡ በኋላ ፡ ነፍሱ ፡ እየተመለሰች ፡ በሌላ ፡ ፍጥረት ፡ እየገባች ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ትወለዳለች ፡ አይሉም ፡ እንጂ፡መንፈሳዊ ፡ ሥራ ፡ በመሥራት ፡ ከማ ዕርግ ፡ ወደ ፡ ማዕርግ ፡ ይደርሳል ፡ ይላሉ ። ስለዚሁም ፡ በቅዱስ ፡ ጴጥሮ ስ ፡ በሁለተኛው ፡ መልእክቱ ፡ በምዕ ፡ ፩ ፡ ቍጥ ፡ ፫—፱የተጻፈውን ፡ ንባ ብ ፡ አንድም ፡ ብለው ፡ በሚተረጉሙት ፡ በሁለተኛው ፡ ትርጓሜ ፡ የሚና ገሩት ፡ ቃል ፡ በቡዳሃ ፡ ትምሕርት ፡ ኔርባን ፡ ከሚባለው ፡ ጋራ ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ ይቃረባል ። ይኸውም ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ የተጻፈው ፡ ነው ።

፩ኛ ። ሰው ፡ በእግዚአብሔር ፡ አምኖ ፡ መንፈሳዊ ፡ ሥራ ፡ ለመሥራ ት ፡ ሲጀምር ፡ ከመዓርገ ፡ ጽማዌ ፡ ይደርሳል ፡ ይላሉ ። መዓርገ ፡ ጽማዌ፡ ማለት ፡ ባለማወቅና ፡ በማወቅ ፡ መካከል ፡ መኖር ፡ ነው ።

፪ኛ ። መንፈሳዊ ፡ ሥራውን ፡ እየጨመረ ፡ ሲሔድ ፡ ከመዓርገ ፡ ጽማዌ ፡ ወደ ፡ መዓርገ ፡ ልባዌ ፡ ይደርሳል ። መዓርገ ፡ ልባዌ ፡ ማለት ፡ ከላዋቂነት ፡ ወጥቶ ፡ ፍጹም ፡ አዋቂ ፡ መሆን ፡ ነው ።

፫ኛ ። መንፈሳዊ ፡ ሥራውን ፡ እየጨመረ ፡ ሲሔድ ፡ ከመዓርገ ፡ ልባዌ ፡ ወደ ፡ መዓርገ ፡ አንብዓ ፡ ንስሐ ፡ ይደርሳል ፡ ይላሉ ። አንብዓ ፡ ንስሐ ማለት ፡ የሠራውን ፡ ኃጢአት ፡ ባሰበ ፡ ቍጥር ፡ እንባው ፡ ሳይታገድ ፡ እንደ ፡ ገደል ፡ ውሀ ፡ መፍሰስ ፡ ነው ።

፬ኛ ። መንፈሳዊ ፡ ሥራውን ፡ እየጨመረ ፡ ሲሔድ ፡ ከመዓርገ ፡ አንብዓ ፡ ንስሐ ፡ ወደ ፡ መዓርገ ፡ ኵነኔ ፡ ይደርሳል ። መዓርገ ፡ ኵነኔ ፡ ማለት ፡ ሥጋን ፡ ለነፍስ ፡ ማስገዛትና ፡ በጠቅላላው ፡ ፈቃደ ፡ ሥጋን ፡ ሁሉ ፡ አሸንፎ ፡ መኖር ፡ ነው ።

፭ኛ ። መንፈሳዊ ፡ ሥራውን ፡ እጨመረ ፡ ሲሔድ ፡ ከመዓርገ ፡ ኵነኔ ፡ ወደ ፡ መዓርገ ፡ ሁሰት ፡ ይደርሳል ።

መዓርገ ፡ ሁሰት ፡ ማለት ፡ ከስፍራው ፡ ሳይነቃነቅ ፡ በአሳቡና፡ በእውቀቱ ፡ ብቻ ፡ እንደ ፡ ፀሐይ ፡ በሁሉ ፡ ስፍራ ፡ እየደረሰ ፡ ሁሉን፡ማየትና ፡ ማወቅ ፡ ነው ።

፮ኛ ። መንፈሳዊ ፡ ሥራውን ፡ እየጨመረ ፡ ሲሔድ፡ከመዓርገ፡ሁሰት ፡ ወደ ፡ መዓርገ ፡ ንጻሬ ፡ ይደርሳል ። መዓርገ ፡ ንጻሬ ፡ ማለት ፡ ገና ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሳለ ፡ መላእክትን ፡ በየነገዳቸውና ፡ በየሰፈራቸው ፡ ሆነው ፡ የሚሠሩትን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ማየት ፡ ነው ።

፯ኛ ። መንፈሳዊ ፡ ሥራውን ፡ እየጨመረ ፡ ሲሔድ ፡ ከመዓርገ፡ንጻሬ ፡ ወደ ፡ መዓርገ ፡ ተሰጥሞ ፡ ይደርሳል ። መዓርገ ፡ ተሰጥሞ ፡ ማለት ፡ በዚህ፡ ዓለም ፡ ጨለማ ፡ ሳይኖርበትና ፡ ሳያገኘው ፡ በባሕረ ፡ ብርሃን ፡ ተሰጥሞና ፡ ተውጦ ፡ መኖር ፡ ነው ።

፰ኛ ። መንፈሳዊ፡ ሥራውን ፡ እየጨመረ ፡ ሲሔድ ፡ ከመዓርገ ፡ ተሰጥሞ ፡ ወደ ፡ መዓርገ ፡ ፍቅር ፡ ይደርሳል ።መዓርገ ፡ ፍቅር ፡ ማለት፡ ኃጥዕ ፤ ጻድቅ ፤ አማኒ ፤ መናፍቅ ፡ ብሎ ፡ በለመለያየት ፡ ሁሉን ፡ አስተካክሎ ፡ መውደድ ፡ ነው ።

፱ኛ ። መንፈሳዊ ፡ ሥራውን ፡ እየጨመረ ፡ ሲሔድ ፡ ከመዓርገ ፡ ፍቅር ፡ ወደ ፡ መዓርገ ፡ አእምሮ ፡ ይደርሳል ። መዓርገ ፡ አእምሮ ፡ ማለት ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሆኖ ፡ ዘወትር ፡ እግዚአብሔርን ፡ ሲያይ ፡ መኖር ፡ ነውና ፡ ይህ ፡ የመጨረሻው ፡ ማዕርግ ፡ ነው ።

ይህም ፡ ትርጓሜ ፤ ሰው ፡ ኔርባንን፡እስኪያልፍ፡ድረስ ፡ ከሞተ ፡ በኋላ፡ ነፍሱ፡እንደ ፡ ገና፡እየተወለደች፡በዚህ፡ዓለም፡የሥራዋን፡ዋጋ፡እየተቀበለች፡ ትኖራለች ። ኔርባንን ፡ ካለፈች ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ገና ፡ መወለድ ፡ የለ ባትም ፡ ከሚባለው ፡ ከቡዳሃ ፡ ትምሕርት ፡ ጋራ ፡ የተቀራረበ ፡ ነው ።

## ስለ ፡ ቡዳሃ ፡ ሃይማኖት ፡ በያገሩ ፡ መዘርጋት ።

ቡዳሃ ፡ ሞራል ፡ የሚባለውን ፡ የመልካም ፡ ኑሮና ፡ አካሔድ ፡ ትምሕ ርት ፡ እያስተማረ ፡ ፵ ፡ ዓመት ፡ ከኖረ ፡ በኋላ ፡ በተወለደ ፡ በ፹ ፡ ዓመቱ ፡ ከክርስቶስ ፡ ልደት ፡ በፊት ፡ በ፭፻፵፫ ፡ ዓመት ፡ አረፈ ።

በዚሁም ፡ ዓመት ፡ መነኮሳቱና ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ሁሉ ፡ ራጃግሬሃ ፡ በሚባል ፡ አገር ፡ ጉባኤ ፡ አድርገው ፡ የቡዳሃ ፡ ትምሕርት ፡ የጸና ፡ እንዲ ሆን ፡ ወስነው ፡ በያገሩ ፡ ሚሲዮኖች ፡ (መምሕራን)እየሔዱ ፡ እንዲያስተ ምሩ ፡ አደረጉ ።

ወዲያውም ፡ በሰሜንና ፡ በደቡብ ፡ ህንድ ፤ በሴሎን ፤ በበርማ ፤ በሲ ያም ፤ በመካከለኛውም ፡ እስያ ፡ ሁሉ ፡ ተዘረጋ ።

ከክርስቶስ ፡ ልደት ፡ በኋላ ፡ በ፷፯ ፡ ዓመት ፡ ወደ ፡ ቻይና ፡ ደረሰና ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ተቀበሉት ።

በ፫፻፸፪ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡ ወደ ፡ ኮሪያ ፡ ደረሰና ፡ ነገሥታቱ ፡ ሳይ ቀሩ ፡ ተቀበሉት ።

በ፭፻፶፪ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡ ነግሦ ፡ የነበረው ፡ የፒክቺ ፡ (ኩዶራ) ንጉሥ ፡ የቡዳሃን ፡ ካህናት ፡ ጠርቶ ፡ ብዙ ፡ መጻሕፍት ፡ አሲዞ ፡ አንድ ፡ ደ ብዳቤ ፡ ጨምሮ ፡ ኪሜይ ፡ ወደሚባለው ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ላኳቸው ፡ ነበር ።

የደብዳቤውም ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ የቡዳሃ ፡ ትምሕርት ፡ ለጊዜው ፡ ለመረ ዳት ፡ የሚያስቸግር ፡ ይመስላል ። ነገር ፡ ግን ፡ ጥቂት ፡ በጥቂት ፡ እያለ ፡ ወደ ፡ ልብ ፡ ሲገባ ፡ ለልብ ፡ ዕረፍት ፡ ይሰጣል ። የለመኑትም ፡ ሁሉ ፡ ይገኝበታል ። የልብም ፡ አሳብ ፡ ሁሉ ፡ ይፈጸምበታልና ፡ ባገርህ ፡ ውስጥ ፡ እንዲዘረጋ ፡ ብታደርግ ፡ መልካም ፡ ነው ፡ የሚል ፡ የወዳጅነት ፡ ቃል ፡ ነው ።

ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ኪሜይም ፡ ደብዳቤውን ፡ ባነበበ ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አለ ሙና ፡ ካህናቱንም ፡ መጻሕፍቱንም ፡ አክብሮ ፡ ተቀበላቸው ።

(ደስታው ፡ ግን ፡ የለመኑት ፡ ሁሉ ፡ ይገኝበታል ፡ ስላለው ፡ ይመስላል ፡)
ከዚያ ፡ ጀምሮ ፡ የቡዳሃ ፡ ትምሕርት ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ተ
ዘረጋ ።

ነገር ፡ ግን ፡ ነገሥታቱ ፡ ከጥንት ፡ ካባቶቻቸው ፡ ጀምሮ ፡ የቆየው
ን ፡ የሽንቶን ፡ ሃይማኖት ፡ የሚጎዳና ፡ የሚያጠፋ ፡ እንዳይሆን ፡ ይጠነ
ቀቁ ፡ ነበርና ፡ የቡዳሃ ፡ ካህናት ፡ የእኛ ፡ ሃይማኖት ፡ ከሽንቶ ፡ ሃይማኖ
ት ፡ ልዩነት ፡ የለውም ፡ እያሉ ፡ በብልሃት ፡ ለነገሥታቱ ፡ ይነግሩ ፡ ነበር ።

ስለዚህ ፡ የቡዳሃ ፡ መቅደስ ፡ በተሠራበት ፡ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ ባጠገቡ ፡
የሽንቶ ፡ ሽራይን ፡ እንዲሠራ ፡ ልማድ ፡ ሆነ ።

## በቡዳሃ ፡ መቅደስ ፡ ስለሚጸለየው ፡ ጸሎት ።

በቡዳሃ ፡ ሃይማኖት ፡ ጸንተው ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ቡዳሃ ፡
መቅደስ ፡ ገብተው ፡ በቡዳሃ ፡ ምስል ፡ ፊት ፡ ቆመው ፡ እየተንበረከኩና ፡
እየቆሙ ፡ እርሱ ፡ ይህን ፡ ትልቅ ፡ ትምሕርት ፡ በማስተማሩ ፡ ቡዳሃን
እያመሰገኑ ፡ የፈለጉትንና ፡ የተመኙትንም ፡ ቡዳሃ ፡ እንዲፈጽምላቸው
ና ፡ ከክፉ ፡ ነገር ፡ እንዲጠብቃቸው ፡ ይጸልያሉ ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ የሚያቀርቡት ፡ ጸሎት ፡ የላቸውም ። ይህንም ፡ ስለ ፡ አደረጉ ፡
ቡዳሃን ፡ የመልካም ፡ ሥራ ፡ መሪና ፡ አስተማሪ ፡ በትምሕርቱም ፡ ዓለም
ን ፡ ከጭንቅና ፡ ከመከራ ፡ ያዳነ ፡ ትልቅ ፡ ቅዱስ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ይሰ
ግዱለታል ፡ እንጂ ፡ በማናቸውም ፡ ምክንያት ፡ ቢሆን ፡ ቡዳሃን ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ነው ፡ ብለው ፡ አይሰግዱለትም ።

## የሽንቶና ፡ የቡዳሃ ፡ ካህናት ፡ በማስተማር ፡ ስለ ፡ መሽቀዳደማቸው ።

ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ጂሙ ፡ ከነገሠበት ፡ ከክርስቶስ ፡ ልደት ፡ በፊት ፡
ከ፮፻፷ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ የቡዳሃ ፡ ሃይማኖት ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ እ
ስከ ፡ ገባበት ፡ እስከ ፭፻፶፪ ፡ ዓመ ፡ ምሕ ፡ ሽንቶ ፡ የመንግሥት ፡ ሃይማ
ኖት ፡ ሆኖ ፡ ይኖር ፡ ነበር ። ይኸውም ፡ ሺ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ዓመት ፡ ያ
ህል ፡ ነው ። ከ፭፻፶፪ ፡ ዓመ ፡ ምሕ ፡ ወዲህ ፡ ግን ፡ የቡዳሃ ፡ ሃይማኖት ፡
የመንግሥት ፡ ሃይማኖት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የቡዳሃ ፡ መቅደስና ፡ የካህናቱ ፡ ቍ
ጥር ፡ እየበዛ ፡ሔዶ ፡ ነበር ። ስለዚህ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሚጂ ፡ ሕገ ፡ መ
ንግሥት ፡ ባቆመ ፡ ጊዜ ፡ ከእንግዴህ ፡ ወዲህ ፡ ከጥንት ፡ ካባቶቻችን ፡ ጀ
ምሮ ፡ ተያይዞ ፡ የመጣልን ፡ የሽንቶ ፡ ሃይማኖት ፡ የመንግሥት ፡ ሃይማኖት ፡

ይሁን ፡ የቡዳሃ ፡ ሃይማኖት ፡ ግን ፡ የሕዝብ ፡ ሃይማኖት ፡ ሆኖ ፡ በነጻነት ፡ ይኑር ፡ ብሎ ፡ ወሰነ ። እንደዚህም ፡ መወሰኑ ፡ የቡዳሃ ፡ ሃይማኖት ፡ እየደከመና ፡ እያነሰ ፤ የሺንቶ ፡ ሃይማኖት ፡ እየበረታና ፡ እየበዛ ፡ የሚሔድ ፡ መስሎት ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ የጃፓን ፡ ልጆች ፡ የሺንቶን ፡ ሃይማኖትና ፡ የቡዳሃን ፡ ሃይማኖት ፡ በትክክል ፡ በመንግሥት ፡ ትምሕርት ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ እንዲማሩ ፡ ተፈቅዶ ፡ ነበርና ፡ የቡዳሃ ፡ ሃይማኖት ፡ እየሰፋ ፡ መሔዱ ፡ አልቀረም ።

ስለዚህ ፡ በ፲፱፻፳፩ ፡ (፲፱፻፳፰ )ዓመ ፡ ምሕ ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ የሺንቶ ፡ ሺራይን ፡ ቢቆጠር ፡ ፲፯ሺ፱፻፳፰ ፡ ሆነ ። የቡዳሃ ፡ መቅደስ ፡ ግን ፡ ፵፩ሺ፻፵፰ ፡ ሆነ ። ከሺንቶ ፡ ሺራይን ፡ ብልጫው ፡ ፳፫ሺ፱፻፳ ፡ መሆኑ ፡ ነው ። ስለዚህም ፡ የጃፓን ፡ ልጆች ፡ የቡዳሃን ፡ ሃይማኖት ፡ በመንግሥት ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ እንዳይማሩ ፡ ለመከልከል ፡ ታስቦ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ በሕዝብ ፡ መካከል ፡ ሁከት ፡ የሚያስነሣ ፡ መሆኑን ፡ ስለ ፡ ተረዱት ፡ የሺንቶን ፡ ሃይማኖትና ፡ የቡዳሃን ፡ ሃይማኖት ፡ ካህናቱ ፡ በየሺራይኑና ፡ በየመቅደሱ ፡ ያስተምሩት ፡ እንጂ ፡ በመንግሥት ፡ ትምሕርት ፡ ቤት ፡ የሁለቱም ፡ ሃይማኖት ፡ መነገሩ ፡ ይቅር ፡ ተብሎ ፡ ተከለከለ ።

---

## በጃፓን ፡ አገር ፡ የክርስቲያን ፡ ሃይማኖት ፡ ስለ ፡ መግባቱ ።

በ፲፭፻፴፬ (፲፭፻፵፪)ዓ፡ ም ፡ ፌርናንዶ ፡ ማንዴዝ ፡ ፒንቶ ፡ የሚባል ፡ የፖርቱጊዝ ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ ገባ ። እርሱም ፡ ፫ዓመት ፡ ተቀምጦ ፡ ወደ ፡ ሀገሩ ፡ ሲመለስ ፡ ሁለት ፡ ጃፓኖች ፡ ከእርሱ ፡ ጋራ ፡ ወስዶ ፡ ማላካ ፡ በሚባል ፡ በፖርቱጊዝ ፡ ቅኝ ፡ አገር ፡ ትቷቸው ፡ ሔዶ ፡ ነበር ። ከነዚሁም ፡ አንደኛው ፡ አንዠሮ ፡ ይባላል ፤ ከተጠመቀ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ጳውሎስ ፡ ተባለ ።

ከዚህም ፤ በኋላ ፡ በፖርቱጊዝ ፡ ቅኝ ፡ አገር ፡ በህንድ ፡ እያስተማረ ፡ የሚኖረው ፡ የጄዝዊት ፡ (ኢየሱሳውያን) ገዳም ፡ ወገን ፡ አባ ፡ ኢክሳቢር ፡ የሚባለው ፡ ሚሲዮን ፤ በ፲፭፻፵፩ (፲፭፻፵፱)ዓ ፡ ም ፡ አንዠሮን ፡ (ጳውሎስ) መንገድ ፡ መሪ ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ ገባ ። ባመቱም ፡ ያማጉቺ ፡ በሚባል ፡ አገር ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ተከለ ። ሥራውም ፡ ሁሉ ፡ እየቀናው ፡ ስለ ፡ ሔደ ፡ ባንድ ፡ ዓመት ፡ ውስጥ ፡ አንድ ፡ ሺ ፡ ጃፓኖች ፤ አጠመቀ ።

ይህም ፡ ወሬ ፡ በአውሮጳ ፡ በተሰማ ፡ ጊዜ ፡ ሌሎችም ፡ የዶሚኒ ካና ፡ የፍራንሲስካ ፡ የአውጉስታኒካም ፡ ገዳሞች ፡ ብዙ ፡ ሚሲዮኖች ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ መላክ ፡ ጀመሩ ። የክርስቲያንም ፡ ሃይማኖት ፡ እ የሰፋ ፡ ይሔድ ፡ ጀመር ። ነገር ፡ ግን ፡ ኢያሚትሱ ፡ የሚባለው ፡ ሶስተ ኛው ፡ ቶኩጋዋ ፡ የመንግሥት ፡ እንደራሴ ፡ በሆነበት ፡ በ፲፮፻፳(፲፮፴፩) ዓ ፡ ም ፡ ትልቅ ፡ ስደትና ፡ መከራ ፡ አገኟቸው ፡ ነበር ። ምክን ያቱም ፡ ከቶኩጋዋ ፡ አስቀድሞ ፡ የመንግሥት ፡ እንደራሴ ፡ የነበረው ፡ የሂዳዮሺ ፡ ትውልድ ፡ ከአዲሱ ፡ እንደራሴ ፡ ትውልድ ፡ ከኢያማትሱ ፡ ጋራ ፡ ይዋጋ ፡ ነበርና ፡ ክርስቲያኖች ፡ የሆኑት ፡ ወታደሮች ፡ በጦርነቱ ፡ ውስጥ ፡ እየተገኙ ፡ በርትተውም ፡ መዋጋታቸው ፡ እየታወቀባቸው ፡ ነው ። በዚህም ፡ ላይ ፡ ደግሞ ፡ ሚሲዮኖች ፡ በፖለቲካ ፡ ሥራ ፡ ውስጥ ፡ እየ ገቡ ፡ ወደ ፡ ፖርቱጌዝና ፡ ወደ ፡ እስጳንያ ፡ ሲላላኩ ፡ እየተገኙ ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ ቀሳውስቱንና ፡ ዲያቆናቱን ፡ ካገሩም ፡ ውስጥ ፡ ወደ ፡ ካቶሊክ ፡ ሃይማኖት ፡ የገቡትን ፡ ሰዎች ፡ እየያዙ ፡ በጭካኔ ፡ የአረማውያን ፡ ቅጣ ት ፡ ይቀጧቸው ፡ ነበር ።

ስለነዚሁም ፡ ክርስቲያኖች ፡ መከራ ፡ ጉቢን ፡ የሚባለው ፡ ታሪክ ፡ ጸ ሐፊ ፡ በናጋሳኪ ፡ ላይ ፡ የተደረገውን ፡ ሲናገር ፡ እጅግ ፡ ያሳዝናል ።

፩ኛ ። እግራቸውንና ፡ እጃቸውን ፡ ከየአጽቁ ፡ እየቆረጡ ፡ በሥቃይ ፡ ይገድሏቸው ፡ ነበር ።

፪ኛ ። ከነነፍሳቸው ፡ ከአንገታቸው ፡ በታች ፡ እየቀበሩ ፡ ወገን ፡ (ላምና ፡ ፈረስ ፡)ያስሔዱባቸው ፡ ነበር ።

፫ኛ ። እንደ ፡ ሩዝ ፡ በጆኒያ ፡ እያገቡ ፡ የጆኒያውን ፡ አፍ ፡ እያሠሩ ፡ ከምረው ፡ በእሳት ፡ ያቃጥሏቸው ፡ ነበር ።

፬ኛ ። እግራቸውንና ፡ እጃቸውን ፡ በግንድ ፡ ላይ ፡ እየወጠሩ ፡ በችን ካር ፡ ይቸነክሩዋቸው ፡ ነበር ።

፭ኛ ። በብረት ፡ አጥር ፡ ውስጥ ፡ እያገቡ ፡ ከአጥሩ ፡ ውጪ ፡ ምግብና ፡ ውሀ ፡ እያስቀመጡና ፡ እያሳዩ ፡ በረሃብና ፡ በጥማት ፡ ይገድሏቸው ፡ ነበር ።

ከዚህም ፡ ሁሉ ፡ እጅግ ፡ የባሰና ፡ የከፋ ፡ አንዱን ፡ ሲቀጡ ፡ ሌላውን ፡ በፊቱ ፡ እያስቀመጡ ፡ እያሳዩ ፡ በኋላ ፡ እርሱን ፡ መቅጣታቸው ፡ ነው ። በዚ ህም ፡ ላይ ፡ ደግሞ ፡ ፹፯ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ተቃጥለው ፡ ፈረሱ ፡ ይላል ።

በኋላ ፡ ግን ፡ ሌሎችም ፡ የፕሮቶስታንት ፡ ሚሲዮኖች ፡ ከአሜሪካ ም ፤ ከእንግሊዝም ፤ ከጀርመንም ፡ አገር ፡ እየመጡ ፡ ማስተማር ፡ ጀም

ረው ፡ ነበርና ፡ ስለ ፡ ብዛታቸው ፡ ሁሉንም ፡ ለማጥፋት ፡ እየፈሩ ፡ ዝም ፡ እስከ ፡ ማለት ፡ ደረሱ ። እንደዚህም ፡ ብልጭ ፡ ድርግም ፡ እያሉ ፡ ሲኖሩ ፡ በ፲፰፻፹፩ ፡ (፲፰፻፹፱)ዓመ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ሜጂ ፡ ሕገ ፡ መንግሥት ፡ ባቆመ ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡ ሃይማኖት ፡ ሙሉ ፡ ነጻነት ፡ አገኙና ፡ በሰላም ፡ ይኖሩ ፡ ጀመር ።

አሁን ፡ ዛሬ ፡ በሙሉ ፡ ጃፓን ፡ የካቶሊኮችም ፤ የፕሮትስታንቶችም ፡ የመስኰብ ፡ ኦርቶዶክሶችም ፤ የሁሉም ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ባንድነት ፡ ሆኖ ፡ ቢቆጠር ፡ ፪፻፵፭ ፡ ሆነ ። ከጃፓንም ፡ ሕዝብ ፡ ወደ ፡ ክርስቲያንነት ፡ የተመለሱ ፡ በድምሩ ፡ ፫፻፴፫ ፡ ሺ ፡ ይሆናሉ ።

ከነዚሁም ፡ መቶው ፡ ሺ ፡ ካቶሊካውያን ። ሁለት ፡ መቶ ፡ ሺ ፡ ፕሮትስታንቶች ። ሠላሳ ፡ ሶስት ፡ ሺ ፡ የመስኰብ ፡ ኦርቶዶክስ ፡ ናቸው ። በነዚህም ፡ ላይ ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ የሚኖሩ ፡ ብዙ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ክርስቲያኖች ፡ ይገኛሉ ።

በዚያም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ መከራ ፡ በተቀበሉበት ፡ ናጋሳኪ ፡ በሚባለው ፡ አገር ፡ እጅግ ፡ የተዋበና ፡ ትልቅ ፡ ካቴድራል ፡ (ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡) ተሠርቶበት ፡ አውሮጳውያን ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ ሲመጡ ፡ ካቴድራሉን ፡ ለማየትና ፡ ለማድነቅ ፡ ወደ ፡ ናጋሳኪ ፡ ይሔዳሉ ።

Mohamed Bilen

Mohamed Bilen

Mo Mo

Po Bow




በቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ ውስጥ ፡ ያለው ፡ ዋናው ፡ የምድር ፡ ባቡር ፡ መቋሚያ ።

## ዘጠኘኛ ፡ ትልቅ ፡ ክፍል ።

## ከቶኪዮ ፡ እስከ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ስለ ፡ ሆነው ፡ ነገር ።

በቶኪዮ ፡ ስለ ፡ መሰነባበት ። ስለ ፡ እስፈንክስ ፡ መርከብ ። በኮቤ ፡ ስለ ፡ መሰነባበት ። ለጃፓን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ቴሌግራም ፡ ስለ ፡ ማሳለፍ ። በሻንጋሂ ፡ ሆስፒታልና ፡ ሳናቴርዮም ፡ ስለ ፡ ማየት ። ሆንግኮንግ ፡ ስለ ፡ መድረስ ። ስለ ፡ ሁለት ፡ ጃፓኖች ፡ መቅረት ። ሳይጎን ፡ ስለ ፡ መድረስና ፡ የካምቦድዥን ፡ ንጉሥ ፡ ስለ ፡ ማየት ። ሲንጋፑር ፡ ስለ ፡ መድረስና ፡ የልዑል ፡ መርድ ፡ አዝማች ፡ አስፋ ፡ ወሰንን ፡ ሎንዶን ፡ መግባት ፡ ስለ ፡ መስማት ። ኮሎምቦ ፡ ስለ ፡ መድረስ ። ጂቡቲ ፡ ስለ ፡ መድረስ ። ከጂቡቲ ፡ እስከ ፡ ኮቤ ፡ ስለ ፡ ባሕሩ ፡ ርዝመት ። ድሬዳዋ ፡ ስለ ፡ መድረስ ። አዲስ ፡ አበባ ፡ ስለ ፡ መግባታችን ።

### ምዕራፍ ፡ ፴፮ ።

ወደ ፡ ሀገራችን ፡ ለመመለስ ፡ ከቶኪዮ ፡ የምንነሣበት ፡ ቀኑ ፡ በታኅሣሥ ፡ ፲፪ ፡ ቀን ፡ መሆኑ ፡ ተቆርጦ ፡ በጋዜጣ ፡ ወጥቶ ፡ ነበርና ፡ በቶኪዮ ፡ ከተማ ፡ የተዋወቅናቸው ፡ ወዳጆቻችን ፡ ሁሉ ፡ ለመሰናበት ፡ ሲሉ ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ መጥተው ፡ ከማታው ፡ በ፩ ሰዓት ፡ ከእኛ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ባቡር ፡ መቋሚያ ፡ ሔዱ ። በደረስንም ፡ ጊዜ ፡ የሚበዙት ፡ ወዳጆቻችን ፡ በባቡር ፡ መቋሚያ ፡ ተሰብስበው ፡ አገኘናቸው ።

ከውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስቴርም ፡ ቀይስ ፡ ሚኒስትር ፡ ክቡር ፡ ምስተር ፡ ናጋያና ፡ ዋናው ፡ ጸሐፊ ፡ ምስተር ፡ ኪሽዋና ፡ መጥተው ፡ ነበር ።

ከንጉሠ ፡ ነገሥቱም ፡ የሊጋባው ፡ ባልደረቦች ፡ ምስተር ፡ ዋታናቢና ፡ የእርሱ ፡ ምክትሎች ፡ መጥተው ፡ ነበር ። ከነዚህም ፡ በቀር ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መላክተኞች ፡ በባቡር ፡ ሲሳፈሩ ፡ እናያለን ፡ በማለት ፡ የመጡ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ።

በቡሩም ፡ ለመነሣት ፡ ፫ ደቂቃ ፡ ሲቀረው ፡ ከተሰበሰቡት ፡ ወዳጆቻችን ፡ መካከል ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ድምጡን ፡ ከፍ ፡ አድርጎ ፡ ወዳጆቻችን ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መላክተኞች ፡ ወደ ፡ ሀገራቸው ፡ መመለሳቸው ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ባንዛይ ፡ እንበል ፡ ብሎ ፡ ተናገረና ፡ ሁሉም ፡ ቀኝ ፡ እጃቸውን ፡ እያነሡ ፡ ፫ ጊዜ ፡ ባንዛይ ፤ ባንዛይ ፤ ባንዛይ ፤ እያሉ ፡ ከጮሁ ፡ በኋላ ፡ እጅ ፡ ለእጅ ፡ እየተያያዝን ፡ ተሰነባብተን ፡ ባቡሩ ፡ ተ

ጓዝ ። ይህንም ፡ የሚያህል ፡ የደስታና ፡ የፍቅር ፡ ምልክት ፡ ስለ ፡ አሳዩን ፡ ከዘመዶቻችን ፡ እንደ ፡ ተለያየን ፡ ያህል ፡ ልባችን ፡ አዘነ ። ሌሊቱንም ፡ ሁሉ ፡ ስንጓዝ ፡ አድረን ፡ በማግሥቱ ፡ ጧት ፡ በ፩ ሰዓት ፡ ኮቤ ፡ ከተማ ፡ ደረስንና ፡ መጀመሪያ ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ በደረስን ፡ ጊዜ ፡ በገባንበት ፡ በኦሪያንታል ፡ ሆቴል ፡ (ምሥራቃዊ ፡ ሆቴል )ገባን ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፯ ።

በኮቤ ፡ ከተማ ፡ ተቀምጠን ፡ ከሜሳጀሪ ፡ ማሪቲም ፡ ኩምፓንያ ፡ ጋራ ፡ እንደ ፡ ተነጋገርነው ፡ ወደ ፡ ሀገራችን ፡ የምንመለስበትን ፡ መርከብ ፡ ስንጠባበቅ ፡ እስፊንክስ ፡ የሚባለው ፡ የፈረንሳዊ ፡ መርከብ ፡ በዚሁ ፡ ወር ፡ በ፲፰ኛው ፡ ቀን ፡ ከጧቱ ፡ በ፫ ሰዓት ፡ ኮቤ ፡ ደረሰ ።

እስፊንክስ ፡ የሚባለው ፡ መርከብ ፡ ከተሠራ ፡ ፲፯ ዓመቱ ፡ ነው ። ከኋላው ፡ እስከ ፡ ፊቱ ፡ ሞላልነቱ ፡ ፪፻፱፪ ሜትር ። የጐድኑም ፡ ስፋት ፡ ፲፰ ሜትር ። ክብደቱ ፡ ፲፰ሺ ፡ ቶን ፡ ነው ።

ባንድ ፡ ሰዓት ፡ እስከ ፡ ፴ኪሎ ፡ ሜትር ፡ መሔድ ፡ ይችላል ። በውስጡ ፡ ያሉት ፡ ሠራተኞች ፡ ከነሹሞቹ ፡ ፪፻፯ ናቸው ። ከነዚህም ፡ በቀር፡ ለ፬፻ መንገደኞች ፡ የሚበቃ ፡ አልጋ ፡ አለበት ።

ይህም ፡ እስፊንክስ ፡ የሚባለው ፡ መርከብ ፡ እንደ ፡ ሜሳጃሪ ፡ ማሪቲም ፡ ኩምፓንያ ፡ ደንብ ፡ በኮቤ ፡ ፲ሰዓት ፡ መቆም ፡ አለበትና ፡ ከማታው ፡ በ፩ ሰዓት ፡ እንድትገቡ ፡ ብሎ ፡ ኮቤ ፡ ያለው ፡ የኩምፓኒያው ፡ ወኪል ፡ ስለ ፡ አስታወቀን ፡ በዚያው ፡ በሰዓቱ ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ገባን ።

በመርከቡም ፡ ውስጥ ፡ ብዙ ፡ ጃፓኖች ፡ ከቶኪዮና ፡ ከኦሳካ ፡ ድረስ ፡ ከእኛ ፡ ጋራ ፡ ለመሰነባበት ፡ መጥተው ፡ አገኘናቸው ። ኮቤም ፡ ያለው ፡ የግብጽ ፡ ቆንስል ፡ አብሮ ፡ ነበር ።

በመሰነባበትም ፡ ጊዜ ፡ ከሀገራችን ፡ ከአዲስ ፡ አበባ ፡ ወደ ፡ ጃፓን ፡ አገር ፡ ለመሔድ ፡ እንደ ፡ ተነሣንበት   ቀን ፡ የሁላችንም ፡ ልብ ፡ አዘነ ።

ይልቁንም ፡ እናት ፡ ልጇ ፡ መንገድ ፡ ሲሔዱ ፡ እንደምታደርገው ፡ ከውስጣቸው ፡ አንዳንዱ ፡ ጋቶና ፡ ችኮላት ፡ ይህንም ፡ የመሰለ ፡ የሚጣፍጥ ፡ ምግብ ፡ ስለ ፡ መሰነባበቻ ፡ እያሉ ፡ በሰጡን ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡ መልካም ፡ አሳባቸው ፡ እያመሰገንን ፡ በሐዘን ፡ ተሰነባበትን ።

ከመርከቡም ፡ ከወጡ ፡ በኋላ ፡ መርከቡ ፡ እስኪነሣ ፡ በመሬት ፡ ቆመው ፡ ይጠብቁ ፡ ነበርና ፡ መርከቡ ፡ ጉዞ ፡ ሲጀምር ፡ መሐርማቸውንና ፡ ባርኔጣቸውን ፡ እያራገቡ ፡ ተሰናበቱን ።

በሀገሬም ፡ ቢሆን ፡ በውጭ ፡ አገርም ፡ ቢሆን ፡ እንደ ፡ ጃፓኖች ፡ እንግዳ ፡ አክባሪዎችና ፡ አፍቃሪዎች ፡ በዘመኔ ፡ ሁሉ ፤ አላየሁም ።

ሌሊቱንም ፡ ስንሔድ ፡ አድረን ፡ በማግሥቱ ፡ ጧት ፡ እንደ ፡ ነገሥታት ፡ መላክተኞች ፡ ደንብ ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ያለውን ፡ ቴሌግራም ፡ አሣለፍሁ ።

ለግርማዊ ፡ የጃፓን ፡ ንጉሠ ፤ ነገሥት ።

በጃፓን ፡ አገር ፡ ከገባን ፡ ጀምሮ ፡ በምድርም ፡ በባሕርም ፡ ስለ ፡ ተደረገልን ፡ የክብር ፡ አቀባበል ፡ አመሰግናለሁ ። የመንግሥትዎን ፤ ጽናት ፡ የሕዝብዎን ፡ ደግነት ፡ በማየቴ ፡ የዘላለም ፡ መታሰቢያ ፡ ይዤ ፡ ወደ ፡ ሀገሬ ፡ መመለሴን ፡ ለግርማዊነትዎ ፡ እገልጻለሁ ። ይኸም ፡ አዲሱ ፡ ዓመት ፡ ለግርማዊነትዎና ፡ ለቤተ ፡ ዘመዶችዎ ፡ ሁሉ ፡ የደስታና ፡ የጤና ፡ ዘመን ፡ እንዲሆን ፡ የልቤን ፡ ምኞት ፡ አቀርባለሁ ።

የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፤ ነገሥት ፡ መንግሥት ፡ አምባሳዶር ።

ቀጥሎም ፡ ከጃፓን ፡ አገር ፡ እስፊንክስ ፡ በሚባለው ፡ መርከብ ፡ መነሣታችንን ፡ ለግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ አስታውቁ ፡ ብዬ ፡ ወደ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ የውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስቴር ፡ ቴሌግራም ፡ አሣለፍሁ ።

ከኮቤም ፡ ከተነሣንበት ፡ ሰዓት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሻንጋይ ፡ የባሕሩ ፡ ማዕበል ፡ በጣም ፡ በርትቶ ፡ ነበርና ፡ ምንም ፡ ባንታመም ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ መጩነቃችን ፡ አልቀረም ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ በዚሁ ፡ ወር ፡ በ፳፩ኛው ፡ ቀን ፡ ከጧቱ ፡ በእኩል ፡ ሰዓት ፡ ሻንጋይ ፡ ስለ ፡ ደረስን ፡ ከማዕበሉ ፡ ሁከት ፡ አረፍን ።

መርከባችንም ፡ ሲቆም ፡ በሸን ፡ ከተማ ፡ በፔንኪንግ ፡ የሚኖረው ፡ የጃፓን ፡ ሚኒስትር ፡ በሻንጋይ ፡ ነበርና ፡ ወዲያው ፡ ዋና ፡ ጸሐፊውን ፡ ልኮ ፡ ምሳ ፡ እንድንጋበዝለት ፡ ስለ ፡ ለመነን ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሔደን ፤ ተጋበዝን ።

ከ፩ ፡ ሰዓትም ፡ በኋላ ፡ በሻንጋይ ፡ ያለው ፡ አድቢንቲስት ፡ የሚባለው ፡ የአሜሪካ ፡ ማኅበር ፡ ዋና ፡ ጸሐፊ ፡ መጥቶ ፡ በሻንጋይ ፡ የተሠራውን ፡ ሆስፒታልና ፡ ሳናቴርዩም ፡ (የጤና ፡ መጠበቂያ ፡ )እንድናይለት ፡ ስለ ፡ ለመነን ፡ በከተማውም ፡ ውስጥ ፡ ከከተማውም ፡ ውጭ ፡ ያለውን ፡ ሁለቱንም ፡ ሆስፒታሎችና ፡ ሳናቴርዩም ፡ አየን ።

ከከተማ ፡ ውጭ ፡ ያለው ፡ ሳናቶርዩም ፡ እጅግ ፡ የተዋበና ፡ ብዙ ፡ ሕሙማን ፡ የሚታከሙበት ፡ ስለሆነ ፡ በኤሌክትሪክም ፡ በመታጠብም ፡ በሌላም ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ብልሃት ፡ ሲያክሙ ፡ ለማየት ፡ አንድ ፡ ሌሊት ፡ በዚያው ፡ በሳናቶርዩም ፡ ውስጥ ፡ አደርሁ ።

ምንም ፡ ባያመኝና ፡ ጤናማ ፡ ብሆን ፡ አደራረጉን ፡ ለማየት ፡ ብዬ፡ አካልን ፡ ሁሉ ፡ በማጠብ ፡ በሚያክሙበት ፡ በመታጠቢያው ፡ ቤት ፡ ገብቼ፡ እየታጠብሁ ፡ አደራረጉን ፡ አየሁ ።

በማግሥቱ ፡ የአውሮጶች ፡ አዲስ ፡ ዓመት ፡ ነበርና ፡ ሻንጋይ ፡ ያለው ፡ የአሜሪካ ፡ ቆንስል ፡ ጀኔራል ፡ በአሜሪካኖች ፡ ሳናቶርዩም ፡ ማደሬን ፡ ሰምቶ ፡ ኑሮ ፡ በ፲፩ ሰዓት ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሔጄ ፡ ስለ ፡ አዲሱ ፡ ዘመን ፡ ከተጠሩት ፡ እንግዶች ፡ ጋራ ፡ ሻይ ፡ እንድጋበዝለት ፡ በስልክ ፡ ቀርበ ፡ ነግሮኝ ፡ ነበርና ፡ ወደዚያ ፡ ሔድሁ ።

በዚያም ፡ ከሁለት ፡ መቶ ፡ የሚበልጡ ፡ አሜሪካኖችና ፡ በሻንጋይም ፡ የሚኖሩ ፡ የየመንግሥቱ ፡ ቆንስሎች ፡ ስለ ፡ ተሰበሰቡ ፡ ሻይና ፡ ሌላም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ዓይነት ፡ እየተጠጣ ፡ ዳንስ ፡ እየተደረገ ፡ እስከ ፡ ፯፡ሰዓት ፡ ቆይተን ፡ ተለያየን ።

በታኅሣሥ ፡ ፳፫ ፡ ቀን ፡ በ፲፫ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ መርከባችን ፡ ከሻንጋይ ፡ ተነሥቶ ፡ ጉዞ ፡ ጀመረ ። በማግሥቱም ፡ ጧት ፡ የራድዮ ፡ ቴሌግራም ፡ ወደ ፡ ተሰቀለበት ፡ ሔደን ፡ ስንመለከት ፡ ልዑል ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ አልጋ ፡ ወራሽ ፡ መርድ ፡ አዝማች ፡ አስፋ ፡ ወሰን ፡ ፓሪስ ፡ ደርሰው፡ የሬፑብሊክ ፡ ፕሬዚዳን ፡ በታላቅ ፡ ክብር ፡ ተቀበሏቸው ። ባልታወቁ ፡ ወታደሮችም ፡ መቃብር ፡ ላይ ፡ አበባ ፡ አስቀመጡ ፡ የሚል ፡ ቃል ፡ ተጽፎ ፡ አየን ።

ልዑል ፡ መርድ ፡ አዝማች ፡ አስፋ ፡ ወሰን ፡ ወደ ፡ አውሮጳ ፡ እንዲሔዱ ፡ መታሰቡን ፡ የሰማነው ፡ ገና ፡ ከአዲስ ፡ አበባ ፡ ሳንነሣ ፡ ነበር ።

ነገር ፡ ግን ፡ ስለ ፡ አገሩ ፡ እሩቅነት ፡ መሔዳቸውንና ፡ መቅረታቸውን ፡ ሳንሰማ ፡ እስካሁን ፡ ቆይተን ፡ ነበርና ፡ አሁን ፡ የመሔዳቸውን ፡ እርግጡን ፡ ወሬ ፡ በመስማታችንና ፡ አውሮጳንም ፡ ለማየት ፡ በመታደላቸው ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ አለን ።

በዚሁም ፡ ወር ፡ በ፳፯ኛው ፡ ቀን ፡ ጧት ፡ በ፪ ሰዓት ፡ ሆንግኮንግ ፡ ገባን ። መርከባችንም ፡ እንደ ፡ ቆመ ፡ የሆንግኮንግ ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ እንኳን ፡ በደህና ፡ መጣችሁ ፡ የሚል ፡ መላክተኛ ፡ ልከ ፡ ወዲያውም ፡ ለምሳ ፡ መጋ

በዙን ፡ ነገረን ። በ፮ ሰዓትም ፡ ባገረ ፡ ገዥው ፡ ቤት ፡ ምሳ ፡ ተጋብዘን ፡ ስንመለስ ፡ በ፲ ሰዓት ፡ መርከባችን ፡ ጉዞ ፡ ጀመረ ።

ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ መጥተው ፡ አገር ፡ አይተው ፡ የሚመለሱ ፡ ሁለት ፡ ጃፓኖች ፡ ከኛ ፡ ጋራ ፡ ነበሩና ፡ ባልታወቀ ፡ ምክንያት ፡ ሆንግኮንግ ፡ ላይ ፡ ቀርተው ፡ ኑሮ ፡ መቅረታቸውን ፡ የመርከቡ ፡ ሹም ፡ ነገረን ።

እነዚህም ፡ ሰዎች ፡ ገና ፡ ከጃፓን ፡ ሲነሡ ፡ ዘመዶቻቸው ፡ እየመጡ ፡ አደራ ፡ ብለውን ፡ ነበርና ፡ ከመርከቡ ፡ ተለይተው ፡ በመቅረታቸው ፡ ስለ ፡ አዘንን ፡ የቀሩበትን ፡ ምክንያት ፡ በቴሌግራም ፡ እንዲጠይቅልን ፡ ለመርከቡ ፡ ሹም ፡ አስታወቅነው ። በሁለተኛውም ፡ ቀን ፡ መርከቡ ፡ ለጥቂት ፡ አምልጧቸው ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሌላ ፡ አደጋ ፡ አላገኛቸውም ። አሁንም ፡ በሌላ ፡ መርከብ ፡ ሆነው ፡ ሴንጋፑር ፡ ላይ ፡ ይደርሱብችኋል ፡ የሚል ፡ ምላሽ ፡ ስለ ፡ መጣልን ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አለን ።

---

## ምዕራፍ ፡ ፴፰ ።

በታኅሣሥ ፡ ፳፱ ቀን ፡ ወደ ፡ ማታ ፡ በ፰ሰዓት ፡ ሳይጎን ፡ ከተማ ፡ ደረስን ።

ወዲያው ፡ እንደ ፡ ደረስንም ፡ የሳይጎን ፡ ከተማ ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ ዋና ፡ ጸሐፊ ፡ መጥቶ ፡ አገረ ፡ ገዥው ፡ አሁን ፡ ለጊዜው ፡ ወደ ፡ ባላገር ፡ ሔዱልና ፡ ነገ ፡ በጧት ፡ ይመለሳል ። ስለ ፡ ሆነ ፡ ግን ፡ የሚያስፈልጋችሁን ፡ ሁሉ ፡ ለማድረግ ፡ እኔ ፡ እችላለሁ ። አሁንም ፡ ፈቃዳችሁ ፡ ቢሆን ፡ በአውቶሞቢል ፡ ከከተማ ፡ ውጭ ፡ አውጥቼ ፡ ጥቂት ፡ አናፍሼ ፡ ልመልሳችሁ ፡ ብሎ ፡ ስለ ፡ ነገረን ፡ ከመርከብ ፡ ወጥተን ፡ ወደ ፡ አውቶሞቢል ፡ ገባን ፤ ከከተማም ፡ ውጭ ፡ እስከ ፡ ፴ ኪሎ ፡ ሜትር ፡ ወጥተን ፡ በሳይጎን ፡ ከተማ ፡ ዙሪያ ፡ ያለውን ፡ ማለፊያ ፡ ማለፊያውን ፡ ቦታ ፡ ስናይ ፡ አምሽተን ፡ ከማታው ፡ ባንድ ፡ ሰዓት ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ተመለስን ።

በማግሥቱም ፡ አገረ ፡ ገዥው ፡ ከሔደበት ፡ አገር ፡ ስለ ፡ ተመለሰ ፡ በ፲ሰዓት ፡ ቀጠሮ ፡ አድርጎልን ፡ ሔደን ፡ ተገናኘን ። ወዲያውም ፡ መርከባችን ፡ በሳይጎን ፡ አራት ፡ ቀን ፡ ያህል ፡ የሚቆይ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ አንግኮር ፡ በሚባለው ፡ አገር ፡ የዱሮ ፡ ከተማ ፡ ፍራሽ ፤ እንደ ፡ አንቲካ ፡ ሆኖ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እየሔደ ፡ የሚያየው ፡ መኖሩን ፡ ሰምተናልና ፡ ወደዚያ ፡ ሔደን ፡ ለማየት ፡ እንወዳለን ፡ አልነው ። እርሱ ፡ ግን ፡ አንግኮር ፡ ከሳ

ይጎን ፡ በአውቶሞቢል ፡ ፲፪ ሰዓት ፡ የሚያስሔድ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በመራቁ ፡ ምክንያት ፡ መርከቡ ፡ ጥዷችሁ ፡ ይሔዳልና ፡ ከሳይጎን ፡ ፬ሰዓት ፡ ብቻ ፡ የሚያስሔደውን ፡ ካምቦድዥ ፡ የሚባለውን ፡ አገር ፡ ሔዳችሁ ፡ ብታዩ ፡ ይሻላል ፡ አለን ።

ይህ ፡ ካምቦድዥ ፡ የሚባለው ፡ አገር ፡ የፈረንሳዊ ፡ ቅኝ ፡ አገር ፡ ነውን ፡ ብለን ፡ ብንጠይቀው ፡ በራሱ ፡ ንጉሥ ፡ እየተገዛ ፡ በፈረንሳዊ ፡ ጥግነት ፡ የሚኖር ፡ መንግሥት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የፈረንሳዊ ፡ ቅኝ ፡ አገር ፡ አይደለም ። ጥግነት ፡ ማለትም ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ፖለቲካ ፡ ለመነጋገር ፡ በፈረንሳዊ ፡ መንግሥት ፡ አማካይነት ፡ ካልሆነ ፡ ብቻውን ፡ ለመነጋገር ፡ አይችልም ፡ ማለት ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ መለሰልን ።

እኛም ፡ አራት ፡ ቀን ፡ ሙሉ ፡ በመርከብ ፡ ውስጥ ፡ ከመቀመጥ ፡ እየዞርን ፡ አገር ፡ ብናይ ፡ ይሻላል ፡ ብለን ፡ ይህን ፡ ስላመለከቱን ፡ እግዚአብሔር ፡ ይስጥልን ። ነገር ፡ ግን ፡ ንጉሥ ፡ ያለበት ፡ አገር ፡ ከሆነ ፡ ባገሩ ፡ ውስጥ ፡ መግባታችንን ፡ መስማቱ ፡ አይቀርምና ፡ ለማናቸውም ፡ ቢሆን ፡ ለመገናኘት ፡ ፈቃድ ፡ ብናገኝ ፡ መልካም ፡ ይሆናል ፡ አልነው ።

አገረ ፡ ገዥውም ፡ በካምቦድዥ ፡ የሚቀመጠውን ፡ የፈረንሳዊ ፡ እንደራሴ ፡ በስልክ ፡ ጠይቄ ፡ ምላሹን ፡ ማታ ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ድረስ ፡ እልካለሁ ፡ ብሎ ፡ አሰናበተን ።

ከማታውም ፡ በ፪ሰዓት ፡ ካገረ ፡ ገዥው ፡ ዋና ፡ ጸሐፊ ፡ አንድ ፡ ደብዳቤ ፡ ስለ ፡ መጣልን ፡ ከፍተን ፡ ብናየው ፡ ነገ ፡ ጧት ፡ በ፭ ሰዓት ፡ አውቶሞቢል ፡ ይመጣላችኋልና ፡ ወደ ፡ ካምቦድዥ ፡ እንድትሔዱ ።

ግርማዊ ፡ የካምቦድዥ ፡ ንጉሥም ፡ እናንተን ፡ ለመቀበል ፡ መፍቀዳቸውን ፡ በስልክ ፡ አስታውቀውናል ፡ የሚል ፡ ሆኖ ፡ አገኘነው ።

እኛም ፡ የካምቦድዥን ፡ አገር ፡ መልካምነት ፡ ሰምተን ፡ ነበርና ፡ ባንድ ፡ ወገን ፡ አገሩን ፡ ለማየት ፡ በሁለተኛውም ፡ ወገን ፡ ግርማዊነታቸውን ፡ ለማየት ፡ ስለ ፡ ተፈቀደልን ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አለን ። በማግሥቱም ፡ በ፭ሰዓት ፡ በአውቶሞቢል ፡ ሆነን ፡ ወደ ፡ ካምቦድዥ ፡ ጉዞ ፡ ጀመርን ። መንገዱ ፡ ዝፍት ፡ የተለቀለቀና ፡ ያማረ ፡ ነው ። በመንገዱም ፡ ቀኝና ፡ ግራ ፡ ያለው ፡ መሬት ፡ እጅግ ፡ ለም ፡ ነው ። የሚበዛውም ፡ ሩዝ ፡ ነው ። ሩዙም ፡ እኩሉ ፡ ይታጨዳል ። እኩሉም ፡ ይወቃል ። እኩሉም ፡ ገና ፡ እሸት ፡ ነው ። ፬ ሰዓት ፡ ሲሆን ፡ ፖናማ ፡ ከሚባል ፡ ትልቅ ፡ ወንዝ ፡ ደረስን ። ወንዙም ፡ እጅግ ፡ ሰፊ ፡ ነው ። ከዳር ፡ እስከ ፡ ዳሩ ፡ በትልቅ ፡ የጢስ ፡ መርከብ ፡ ፲

ደቂቃ ፡ ያስሔዳል ። ይኸውም ፡ ትልቅ ፡ የጢስ ፡ መርከብ ፡ ላዩ ፡ በሣንቃ ፡ የተነጠፈ ፡ ወለል ፡ ነውና ፡ ከመሬቱ ፡ ጋራ ፡ መሸጋገሪያ ፡ ሣንቃ ፡ ሠርተው ለት ፡ ተጠግቶ ፡ ሲቆም ፡ አውቶሞቢሉ ፡ ከነሰዎቹና ፡ ከነዕቃው ፡ በውስጡ ፡ ይገባል ። የሚይዘውም ፡ ከ፭ ፡ እስከ ፡ ፩ ፡ አውቶሞቢል ፡ ነውና ፡ አውቶሞቢ ሉን ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ማዶ ፡ ይሔዳል ። ከወደቡም ፡ ሲደርስ ፡ እንደ ፡ ፊተ ኛው ፡ ከመሬቱ ፡ ጋራ ፡ በሚያገናኘው ፡ መሻገሪያ ፡ አውቶሞቢሉን ፡ አሸ ጋግሮ ፡ የጢሱ ፡ ጀልባ ፡ ከካምቦድዥ ፡ የሚመጡትን ፡ ሌሎች ፡ አውቶ ሞቢሎች ፡ ይዞ ፡ ይመለሳል ።

ከዚያም ፡ ተጉዘን ፡ ለ፯ ፡ ሰዓት ፡ ሩብ ፡ ሲቀረው ፡ ካምቦድዥ ፡ ከተማ ፡ ደረስን ። በዚያም ፡ ያለው ፡ የፈረንሣዊ ፡ መንግሥት ፡ እንደራሴ ፡ ከሳይጎ ን ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ እንደ ፡ ተቀበለው ፡ ትእዛዝ ፡ ጸሐፊውን ፡ በቤቱ ፡ በር ፡ አቁሞ ፡ ያስጠብቀን ፡ ነበርና ፡ እንደ ፡ ደረስን ፡ ተቀብሎ ፡ ለማረፊያ ፡ ወደ ፡ ተሰናዳልን ፡ ስፍራ ፡ ይዞን ፡ ገባ ። እኩል ፡ ሰዓትም ፡ ካረፍን ፡ በኋላ ፡ ወ ደ ፡ ምሳ ፡ መጋበዣው ፡ ቤት ፡ ወሰዱን ። በዚያም ፡ የፈረንሳዊ ፡ መንግሥ ት ፡ እንደራሴ ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ ክብር ፡ የካምቦድዥን ፡ መንግሥት ፡ ጠቅላይ ሚኒስትሩንና ፡ ያገር ፡ ግዛት ፡ ሚኒስትሩን ፣ የፍርድ ፡ ሚኒስትሩንና ፡ የር ሻ ፡ ሚኒስትሩን ፡ ለምሳ ፡ ጋብዞ ፡ ነበርና ፡ ወዲያው ፡ እንደ ፡ ገባን ፡ በየስ ማቸው ፡ እየነገረ ፡ አስተዋወቀን ።

ለምሳም ፡ በተቀመጥን ፡ ጊዜ ፡ የፈረንሣዊ ፡ መንግሥት ፡ እንደራ ሴ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሰዎችና ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ አራት ፡ የጂቡቲ ፡ ሰዎች ፡ በወሰን ፡ ላይ ፡ ተጋጥመው ፡ ከጂቡቲ ፡ ሰዎች ፡ ወ ገን ፡ ሥልሳ ፡ ሰዎች ፡ ሞቱ ፡ የሚል ፡ ቃል ፡ ዛሬ ፡ ጧት ፡ በራዲዮ ፡ ሰማሁ ፡ ብሎ ፡ ነገረን ። እኛም ፡ የኢትዮጵያ ፣ መንግሥት ፡ ሰዎችና ፡ የጂቡቲ ፡ ሰዎች ፡ ይዋጋሉ ፡ ብለን ፡ አንጠረጥርም ። ነገር ፡ ግን ፡ ሱማሌዎቹና ፡ አዳሎቹ ፡ በየጊዜው ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ይዋጋሉና ፡ እንደ ፡ ልማዳቸው ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ተዋግተው ፡ ይሆናል ፡ አልነው ። እኔም ፡ እንደዚሁ ፡ ይመስለኛል ፡ አለ ።

ከምሳም ፡ በኋላ ፡ ባንደኛው ፡ አዳራሽ ፡ ተቀምጠን ፡ ያገሩንና ፡ የንጉ ሡን ፡ አኳሆን ፡ ጠቅላይ ፡ ሚኒስትሩን ፡ ከዚህ ፡ እንደሚከተለው ፡ ጠየቅሁት ።

ጥያቄ ፡ የካምቦድዥ ፡ ሕዝብ ፡ ቍጥር ፡ ምን ፡ ያህል ፡ ነው ።

ምላሽ ፣ ፪ ሚሊዮን ፡ ፯፻ሺ ፡ ነው ።

ጥያቄ ፣ የዛሬው ፡ ንጉሥ ፡ ስንተኛ ፡ ናቸው ።

ምላሽ ፣ ሰባኛ ፡ ናቸው ።

ጥ ፤ ትውልዳቸው ፡ ከላይ ፡ ጀምሮ ፡ ሳያቋርጥ ፡ የመጣ ፡ ነውን ።

ም ፤ አዎን ፡ ተያይዞ ፡ የመጣ ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ ልጅ ፡ የሌለው ፡ እንደሆነ ፡ ትልልቆቹ ፡ ሰዎች ፡ ከዚያው ፡ ከዘሩ ፡ እየመረጡ ፡ ያነግሣሉ ።

ጥ ፤ የመንግሥቱ ፡ ሃይማኖት ፡ ምንድነው ።

ም ፤ የቡዳሃ ፡ ሃይማኖት ፡ ነው ። ስለዚህም ፡ ከ፲፩ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ የቡዳሃን ፡ ሃይማኖት ፡ በግድ ፡ እንዲማሩ ፡ አዋጅ ፡ ተነግሯል ።

ጥ ፤ ንጉሡ ፡ በሳምንት ፡ስንት ፡ ቀን፡ወደ ፡ ቡዳሃ ፡ መቅደስ ፡ ይሔዳሉ ።

ም ፤ በውጭ ፡ ወደ ፡ አለው ፡ መቅደስ ፡ አንዳንድ ፡ጊዜ፡ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ቶሎ ፡ ቶሎ ፡ አይሔዱም ። ነገር ፡ ግን ፡ በቤተ ፡ መንግሥታቸው ፡ ግቢ ፡ የቡዳሃ ፡ መቅደስ ፡ አለና ፡ ሰባት ፡ ሰባት ፡ ካህናት ፡ በተራ ፡ እየገቡ ፡ ዘወትር ፡ ይጸልያሉ ። ንጉሡም ፡ ራሳቸው ፡ የቡዳሃ ፡ መቅደስ ፡ የበላይ ፡ ሹምና ፡ የሃይማኖት ፡ ጠባቂ ፡ ናቸው ።

ጥ ፤ ካህናቱ፡በየተራ፡እየገቡ፡ስለ፡መጸለያቸው፡ከንጉሡ፡ምን፡ያገኛሉ ።

ም ፤ የበሰለ ፡ የእለት ፡ ምግብ ፡ ወይም ፡ ለእለት ፡ ምግብ ፡ ብቻ ፡ መግዣ ፡ መሐልቅና ፡ የሚለብሱትን ፡ ወይባ ፡ ልብስ ፡ ያገኛሉ ።

ጥ ፤ ገንዘብሳ ፡ አይሰጧቸውምን ።

ም ፤ ሌላ ፡ ምንም ፡ ገንዘብ ፡ አይሰጧቸውም ። ቢሰጧቸውም ፡ እንዳይቀበሉ ፡ የቡዳሃ ፡ ሕግ ፡ ይከለክላቸዋል ።

ጥ ፤ የትምሕርት ፡ ቤት ፡ በብዙ ፡ ተከፍቷልን ።

ም ፤ ለቡዳሃ ፡ ሃይማኖት ፡ ብዙ ፡ የትምሕርት፡ቤት ፡ ተከፍቷል ። ስለ ውጭ ፡ አገር ፡ ቋንቋ ፡ ግን ፡ ያውም ፡ ለመጀመሪያ ፡ ትምሕርት፡ ጥቂቶች ፡ የትምሕርት ፡ ቤቶች ፡ ተከፍተዋል ። የንጉሡ ፡ ልጆች ፡ እንኳ ፡ ወደ ፡ ፈረንሳዊ ፡ አገር ፡ ሔደው ፡ ኒስ ፡ በሚባል ፡ አገር ፡ ይማራሉ ፡ አሉኝ ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ እየተሰነባበትን ፡ ወደ ፡ ቤታቸው ፡ ሔዱ ። እኛ ፡ ግን ፡ ከተማውን ፡ እየዞርን ፡ ለማየት ፡ ከፈረንሳዊ ፡ እንደራሴ ፡ ጸሐፊ ፡ ጋራ ፡ በአውቶሞቢል ፡ ሆነን ፡ ሔድን ።

ከተማው ፡ እጅግ ፡ የተዋበ ፡ ነው ። መንገዱም ፡ የጠዳ ፡ የቤቱም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ባዲሱ ፡ ዘመን ፡ ብልሃት ፡ የተሠራ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በጣም ፡ ያምራል ።

ደግሞ ፡ ለከተማው ፡ ውበትና ፡ ጥዳት ፡ የሆነው ፡ የበታው ፡ ሰፋፊነት ፡ ነው ።



የካምቦድዥ ፡ ንጉሥ ፡ ግርማዊ ፡ ሲሶዋትህ ፡ ምኒቦንግ ።

ለያንዳንዱ ፡ ቤት ፡ በደጁ ፡ መስክም ፡ አበባም ፡ ዛፍም ፡ አለው ። ዛፉም ፡ አንድ ፡ ዓይነት ፡ ሳይሆን ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ዓይነት ፡ ነው ። ያውም ፡ በጣም ፡ የወፈፈረና ፡ ቅጠላም ፡ ነው ።

ደግሞ ፡ ከተማው ፡ የተሠራው ፡ መርከብ ፡ በሚያስሔድ ፡ በትልቅ ፡ ወንዝ ፡ ዳር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የከተማውን ፡ እድፍና ፡ ጉድፍ ፡ ለማጥራት ፡ ይመቻል ።

በዚሁም ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ማታ ፡ በ፲፩ሰዓት ፡ ግርማዊ ፡ ንጉሥን ፡ ለማየ ት ፡ ተፈቅዶልን ፡ ነበርና ፡ ፲ሰዓት ፡ ሲሆን ፡ ወደ ፡ ማረፊያ ፡ ቤታችን ፡ ተ መልሰን ፡ የማዕርግ ፡ ልብሳችንን ፡ ለብሰን ፡ ለ፲፩ሰዓት ፡ ሩብ ፡ ሲቀረው ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ጉዞ ፡ ጀመርን ።

በስተ ፡ ውጭ ፡ ባለው ፡ በቅጥሩ ፡ በር ፡ ስንደርስ ፡ ዘበኞቹ፡ጥሩምባ ፡ ነፍተው ፡ መድረሳችንን ፡ አስታወቁ ።

ወደ ፡ ውስጥም፡በገባን ፡ ጊዜ ፡ [illegible] ቅላይ ፡ ሚኒስትሩና ፡ የንጉሡ ፡ ኤ ዴካ ፡ የማዕርግ ፡ ልብሳቸውን ፡ ለብሰው ፡ ኒሻን ፡ አድርገው ፡ በበሩ ፡ ላይ፡ ቆመው ፡ ተቀበሉን ። ወዲያው ፡ ወደ ፡ እንግዳ ፡ መቀበያው ፡ አግብተው ከግርማዊ ፡ ንጉሥ ፡ ጋራ ፡ አገናኙን ።

የግርማዊ ፡ ንጉሥ ፡ ስማቸው ፡ ሲሶዋትህ ፡ ምኒቦንግ ፡ ነው ። የማዕር ጋቸው ፡ አጻጻፍ ፡ ግን ፡ ፔሬአ ፡ ባቶ ፡ ሳምዳሽ ፡ ፔሬአ ፡ እየተባለ ፡ ነው ።

እድሜያቸውም ፡ ሥልሳ ፡ ዓመት ፡ ነው ። ከነገሡም ፡ አምስተኛውን ዓመት ፡ ይዘዋል ። በወርቅ ፡ አምሮ ፡ የተጠለፈ ፡ ነጭ ፡ ኮት ፡ ለብሰው ፡ ነበር ። ሱሪያቸው ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ሀገራቸው ፡ ደንብ ፡ የቀይ ፡ ሐር ፡ ግል ድም ፡ ሆኖ ፡ እንደ ፡ ጕነፉ ፡ በእግር ፡ መካከል ፡ አልፎና ፡ ዞሮ ፡ በወገብ ፡ ላይ ፡ የታሠረ ፡ ነው ።

በእግራቸው ፡ ጥቁር ፡ ሹራብና ፡ ላዩ ፡ ክፍት ፡ የሆነ ፡ የማታ ፡ ጥቁር፡ ጫማ ፡ አድርገዋል ። ከወንበራቸውም ፡ ተነሥተው ፡ በእውነተኛ ፡ ትሕ ትና ፡ ተቀብለው ፡ በስተቀኛቸው ፡ ባለው ፡ ወንበር ፡ አስቀምጠው ፡ አገሬ ንና ፡እኔን፡ ለማየት ፡ በመምጣታችሁ ፡አመሰግናችኋለሁ ፡ ብለው ፡ ተናገሩ ።

እኔም ፡ ግርማዊ ፡ ሆይ ፡ መርከባችን ፡ ሳይጎን ፡ ላይ ፡ አራት ፡ ቀን ፡ ሙሉ ፡ የሚቆም ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የሀገርዎን ፡ መልካምነት ፡ ሰምቼ ፡ ነበርና ፡ አገሩንና ፡ ከተማውን ፡ ብቻ ፡ አይተን ፡ ለመሔድ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ ግር ማዊነትዎን ፡ ለማየት ፡ ይመቻል ፡ ብዬ ፡ ምንም ፡ አላሰብሁም ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ በትልቁ ፡ ደግነትዎ ፡ ግርማዊነትዎን ፡ ለማየት ፡ ስለ ፡ ፈ

ቀዱልኝ ፡ አመሰግንዎታለሁ ፡ ብዬ ፡ ስጨርስ ፡ ለመታሰቢያ ፡ ሆኖ ፡ የሚሰጥ ፡ አንድ ፡ ባለ ፡ ወርቅ ፡ ጣፋ ፡ ጋሻ ፡ ይገዙ ፡ ነበርና ፡ ያንን ፡ አቅርቤ ፡ ይህ ፡ የወርቅ ፡ ጣፋ ፡ ጋሻ ፡ ባገራችን ፡ እንደ ፡ ዛሬ ፡ ዘመን ፡ የጠመንጃ ፡ ነገር ፡ ሳይለመድ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ትልልቅ ፡ አርበኞች ፡ ወደ ፡ ጦርነት ፡ እየገቡ ፡ ሲዋጉ ፡ የጠላት ፡ ጦርና ፡ ጐራዴ ፡ የሚከላከሉበት ፡ ነው ። መልካሙን ፡ አገርዎንና ፡ ግርማዊነትዎን ፡ ለማየቴ ፡ መታሰቢያ ፡ ሆኖ ፡ በቤተ ፡ መንግሥትዎ ፡ እንዲቀመጥ ፡ እለምናለሁ ፡ ብዬ ፡ ሰጠኋቸው ። ግርማዊነታቸውም ፡ በታላቅ ፡ ደስታ ፡ ተቀብለው ፡ በክንዳቸው ፡ እያገቡ ፡ አያያዙን ፡ ከፈተኑ ፡ በኋላ ፡ ጠቅላይ ፡ ሚኒስትሩ ፡ ተቀብለው ፡ በፊታቸው ፡ በጠረጴዛው ፡ ላይ ፡ አኖረው ።

ግርማዊነታቸውም ፡ ለእኔ ፡ ለመስጠት ፡ ያዘጋጁትን ፡ የዝሆን ፡ ጥርስና ፡ ወርቅ ፡ እየተፈለፈለ ፡ የገባበት ፡ እጅግ ፡ ያጌጠና ፡ ያማረ ፡ ከዘራ ፡ አስመጥተው ፡ አገሬን ፡ ለማየት[illegible]ታሰቢያ ፡ እንዲሆን ፡ ብለው ፡ ሰጡኝና ፡ ተቀበልሁ ።

ቀጥሎም ፡ ሎሚናት ፡ የሚመስል ፡ መጠጥ ፡ ቀርቦ ፡ ወደ ፡ ሀገራችሁ ፡ በደህና ፡ ያግባችሁ ፡ ብለው ፡ መርቀው ፡ ከጠጣን ፡ በኋላ ፡ የጽሕፈት ፡ ቤቱንና ፡ ሌላውንም ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ላሳያችሁ ፡ ብለው ፡ እርሳቸው ፡ እየተቀደሙ ፡ እየገቡ ፡ የመኝታ ፡ ቤታቸው ፡ ሳይቀር ፡ ሁሉንም ፡ አሳዩን ። እውነተኛ ፡ ትሕትና ፡ ማለት ፡ እንደዚህ ፡ ነው ። የበታች ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ የበላዩን ፡ ቢያከብር ፡ አይደነቅም ። የበላይ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ የበታቹን ፡ ቢያከብር ፡ እጅግ ፡ ያስመሰግነዋል ።

ግርማዊነታቸው ፡ ለእኛ ፡ የትሕትና ፡ ሥራ ፡ የሠሩልን ፡ ቢበዛ ፡ ፳ ደቂቃ ፡ ይሆናል ። እኛ ፡ ግን ፡ ይህን ፡ መልካሙን ፡ ሥራቸውን ፡ እስከ ፡ እድሜ ፡ ልካችን ፡ ልንረሳውና ፡ ልንዘነጋው ፡ አንችልም ።

ከቤተ ፡ መንግሥቱም ፡ ከተመለስን ፡ በኋላ ፡ በእግር ፡ ሆነን ፡ ከተማውን ፡ ስናይ ፡ አመሸን ። ከማታውም ፡ በ፫ሰዓት ፡ ተኩል ፡ የካምቦድዥ ፡ ሰዎች ፡ ትያትር ፡ ሲጫወቱ ፡ እናሳያችሁ ፡ ብለው ፡ ወሰዱን ። በደረስንም ፡ ጊዜ ፡ ጨዋታው ፡ ተጀምሮ ፡ አገኘነው ። ጨዋታው ፡ በንግግርም፤ በመጨፈርም ፤ በመዝፈንም ፤ ነበር ። የዘፈኑ ፡ ዜማ ፡ ግን ፡ ባገራችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ ላሊበሎች ፡ ገንዘብ ፡ ለመለመን ፡ ሌሊት ፡ እንደ ፡ የሚጮሁት ፡ ዜማ ፡ ነው ።





ልዑል ፡ መርድ ፡ አዝማች ፡ አስፋ ፡ ወሰን ፡
የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ አልጋ ፡ ወራሽ ።

ይህንም ፡ የላሊበሎች ፡ ዜማ ፡ በመስማታችን ፡ ሰሎሞን ፡ ከፀሐይ ፡ በታች ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ የለም ፡ ያለውን ፡ ቃል ፡ እያሰብን ፡ አደነቅን ፡፡

በማግሥቱም ፡ በ፩ሰዓት ፡ ከካምቦድዥ ፡ ከተማ ፡ ተነሥተን ፡ በ፫ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ሳይጎን ፡ ደረስን ፡፡ በዜሁም ፡ ቀን ፡ ማታ ፡ በሁለት ፡ ሰዓት ፡ የሳይጎን ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ ለእራት ፡ ጋብዘን ፡ ነበርና ፡ በዚያ ፡ አ ምሽተን ፡ ወደ ፡ መርከባችን ፡ ተመለስን ፡፡ ስንመለስም ፡ በሳይጎን ፡ የ ሚኖሩ ፡ ፈረንሣዎች ፡ ወንዶቹም ፡ ሴቶቹም ፡ በመርከቡ ፡ ተሰብስበው ፡ መተላለፊያ ፡ እንኳ ፡ አላገኘንም ፡፡ ምክንያቱንም ፡ ብንጠይቅ ፡ ይህ ፡ እ ስፊንክስ ፡ የሚባለው ፡ መርከብ ፡ ከእንግዴህ ፡ ወዴህ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ አገር ፡ መመላለሱ ፡ ቀርቶ ፡ በእርሱ ፡ ምትክ ፡ ሌላ ፡ መርከብ ፡ ሊመላ ለስ ፡ ነውና ፡ መርከቡንና ፡ የመርከቡን ፡ ሹሞች ፡ ለመሰነባበት ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ነገሩን ፡፡ አገረ ፡ ገዥው ፡ እንኳ ፡ ሳይቀር ፡ ከራት ፡ በኋላ ፡ መጥቶ ፡ በዚሁ ፡ መርከብ ፡ ላይ ፡ አምሽቶ ፡ ሔደ ፡፡ በጥር ፡ ፫ቀን ፡ ከሌሊቱ ፡ በ ፲፩ሰዓት ፡ መርከባችን ፡ ወደ ፡ ሲንጋፑር ፡ ጉዞ ፡ ጀመረ ፡፡ ከጧቱ ፡ በ፩ሰ ዓት ፡ ተኩል ፡ በሳይጎን ፡ ያለው ፡ የአይሮፕላን ፡ ሹም ፡ በአይሮፕላን ፡ መ ርከቡን ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ ዞሮ ፡ የስንብት ፡ ሰላምታ ፡ ሰጥቶ ፡ ተመለሰ ፡፡

---

## ምዕራፍ ፡ ፴፱ ፡፡

በጥር ፡ ፰ ፡ ቀን ፡ ከጧቱ ፡ በ፩ ፡ ሰዓት ፡ ሲንጋፑር ፡ ገባን ፡፡ መርከቡ ም ፡ እንደቆመ ፡ የፈረንሳዊ ፡ ቆንስልና ፡ የጃፓን ፡ ቆንስል ፡ መጥተው ፡ እ ንኳን ፡ ደህና ፡ መጣችሁ ፡ ብለው ፡ ተገናኙን ፡፡ ሆንግኮንግ ፡ ላይም ፡ ቀ ርተው ፡ የነበሩት ፡ ሁለቱን ፡ የጃፓን ፡ ሰዎች ፡ በዚያው ፡ አገኘናቸው ፡፡ መ ርከቡም ፡ ሲንጋፑር ፡ ላይ ፡ ፳ ፡ ሰዓት ፡ ይቆም ፡ ነበርና ፡ ከመርከብ ፡ ወር ደን ፡ በከተማው ፡ የሚታየውን ፡ ማለፊያ ፡ ማለፊያውን ፡ ቦታ ፡ በአውቶሞ ቢል ፡ እየዞርን ፡ ስናይ ፡ ቆይተን ፡ ወደ ፡ መርከባችን ፡ ተመለስንና ፡ መር ከቡ ፡ በ፱ ፡ ሰዓት ፡ ጉዞ ፡ ጀመረ ፡፡ በዚሁም ፡ ቀን ፡ የራዲዮ ፡ ማስታወቂ ያ ፡ የተሰቀለበትን ፡ ስንመለከት ፡ ልዑል ፡ አልጋ ፡ ወራሽ ፡ መርድ ፡ አዝ ማች ፡ አስፋ ፡ ወሰን ፡ ከእኅታቸው ፡ ከልዕልት ፡ ተናኘ ፡ ወርቅ ፡ ጋራ ፡ ሎ ንዶን ፡ መድረሳቸውንና ፡ በሎንዶንም ፡ እስከ ፡ ፲ ፡ ቀን ፡ በአፈሴል ፡ ለመ ቆየት ፡ መታሰቡን ፡ ተጽፎ ፡ አየን ፡፡

ከዚህ ፡ ቀደም ፡ በራዲዮ ፡ ያገኘነው ፡ ቃል ፡ ልዑል ፡ አልጋ ፡ ወራሽ ፡ ብቻ ፡ ፓሪስ ፡ ገቡ ፡ የሚል ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ እኅታቸው ፡ አብረዋቸው ፡ መ

ሆናቸውን ፡ አያስታውቅም ፡ ነበርና ፡ አሁን ፡ አዲስ ፡ ወሬ ፡ በማግኘታችን ፡ ደስ ፡ አለን ።

በጥር ፡ ፲ ፡ ቀን ፡ ከጧቱ ፡ በ፲፪ ፡ ሰዓት ፡ ኮሎምቦ ፡ ገባን ። በኮሎምቦም ፡ ሁለት ፡ የፈረንሳዊ ፡ ሱማሪዎች ፡ (የጦር ፡ መርከቦች ፡ ) ቆመው ፡ ነበርና ፡ ኮማንዳው ፡ በኮሎምቦ ፡ ካለው ፡ ከሜሳጀሪ ፡ ማሪቲም፡ኩምፓንያ፡ ወኪል ፡ ጋራ ፡ መጥቶ ፡ ተዋወቀን ። ወዲያውም ፡ ሱማሪን ፡ የሚባለውን፡ በባሕር ፡ ውስጥ ፡ የሚጠልቀውን ፡ መርከብ ፡ እንድናይለት ፡ ለመነንና ፡ በ፱ ፡ ሰዓት ፡ ሔደን ፡ አየን ።

ወደ ፡ ማታም ፡ በከተማው ፡ የሚታየውን ፡ ማለፊያ ፡ ማለፊያውን ፡ ቦታ ፡ ስናይ ፡ ቆይተን ፡ ወደ ፡ መርከባችን ፡ ተመለስን ። ፀሐይም ፡ ስትጠልቅ ፡ መርከባችን ፡ ጒዞ ፡ ጀመረ ።

በማግሥቱም ፡ ጧት ፡ የራዲዮ ፡ ቴሌግራም፡ወደ፡ተሰቀለበት፡ ሔደን ፡ ስንመለከት ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ አልጋ ፡ ወራሽ ፡ ልዑል ፡ መርድ፡ አዝማች ፡ አስፋ ፡ ወሰን ፡ ሮማ ፡ ገቡ ፡ የሚል ፡ ቃል ፡ ተጽፎ ፡ ስላየን ፡ ሮማ ፡ መድረሳቸው ፡ ወደ ፡ ሀገራቸው ፡ የሚመለሱበት ፡ ጊዜው ፡ መድረሱን ፡ የሚያመለክት ፡ ነውና ፡ ከጥቂት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ላይ ፡ ልዑልነታቸውን ፡ እናያለን ፡ በማለት ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አለን ።

በጥር፲፯ ቀን ፡ ከጧቱ ፡ በ፫ሰዓት ፡ ጂቡቲ፡ከተማ ፡ ገባን ። የጂቡቲም፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ ዋና ፡ ጸሐፊ ፡ መጥቶ ፡ ያገረ ፡ ገዥውን ፡ ሰላምታ ፡ ነግሮ ፡ ወዲያውም ፡ ለራት ፡ መጋበዙን ፡ አስታወቀን ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ከመርከብ ፡ ወርደን ፡ በኢትዮጵያ ፡ ቆንስላታችን ፡ ጥቂት ፡ ካረፍን ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ገባን ።

---

## ምዕራፍ ፡ ፵ ።

ወደ ፡ ፊት ፡ ከኢትዮጵያ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ አገር ፡ ለሚሔዱ ፡ ሰዎች ፡ ማስታወቂያ ፡ እንዲሆን ፡ ፡ ከጂቡቲ ፡ እስከ ፡ ጃፓን ፡ የወደብ ፡ ከተማ ፡ እስከ ፡ ኮቤ ፡ የሔድነውን ፡ የባሕሩን ፡ ርዝመት ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ፡ እንዳለው ፡ አድርጌ ፡ ጽፌአለሁ ።

ከጂቡቲ ፡ እስከ ፡ ኮሎምቦ ፡ .......... ፬ሺ ፪፳ ፡ ኪ ፡ ሜ፡፳፪፹፬ሜትር፡
ከኮሎምቦ ፡ እስከ ፡ ሲንጋፑር ፡ .........፪ሺ፱፪፯ ፡ ኪ ፡ ሜ፡፯፪፵ ሜትር፡
ከሲንጋፑር ፡ እስከ ፡ ሳይጎን ፡ .........፩ሺ፪፪ ፡ ኪ ፡ ሜ፡ ፺፯ሜትር፡

ከሳይጎን ፡ እስከ ፡ ሆንግኮንግ ፡ . ...... ፩ሺ፺፻፳፱፡ኪ. ፡ ሜ ፡ ፱፻፳፫ሜትር፡
ከሆንግኮንግ ፡ እስከ ፡ ሻንጋሂ ፡ ..........፩ሺ፰፻፳፯፡ኪ. ፡ ሜ ፡ ፵፫ሜትር፡
ከሻንጋሂ ፡ እስከ ፡ ኮቤ ፡ ..................፩ሺ፬፻፴፰፡ኪ. ፡ ሜ ፡ ፫፻ ሜትር፡

በድምሩ ፡ ከጂቡቲ ፡ እስከ ፡ ኮቤ ፡ ፲፪ሺ ፡ ፱፻፬ ፡ ኪሎ ፡ ሜትር ፡ ፱፻፴፯ ፡ ሜትር ፡ ነው ፡፡

፩ኪሎ ፡ ሜትር ፡ ፩ሺ ፡ ሜትር ፡ ነው ፡፡ እንደዚህም ፡ ሲሆን ፡ ከጂቡቲ ፡ እስከ ፡ ኮቤ ፡ ፲፪ሚሊዮን ፡ ፱፻፬ሺ ፡ ፱፻፴፯ ፡ ሜትር ፡ መሆኑ ፡ ነው ፡፡

፩ሜትር ፡ ፪ክንድ ፡ ነው ፡፡ እንደዚህም ፡ ሲሆን ፡ ከጂቡቲ ፡ እስከ ፡ ኮቤ ፡ ፳፭ሚሊዮን ፡ ፰፻፱ ፡ ፬፻፷፪ ፡ ክንድ ፡ መሆኑ ፡ ነው ፡፡

ከጂቡቲ ፡ እስከ ፡ ማርሲይ ፡ ግን ፡ ፲ሚሊዮን ፡ ፱፻፷፬ሺ ፡ ፪፻፳፬ ፡ ክንድ ፡ ነው ፡፡ እንደዚህም ፡ ሲሆን፡ብልጫው፡፲፭ ሚሊዮን ፡ ፱፻፵፫ሺ ፡ ፪፻፵፫ ክንድ ፡ መሆኑ ፡ ነው ፡፡

ይህም ፤ እጅግ ፡ የረዘመ ፡ የባሕር ፡ መንገድ ፡ የጽሕፈት ፡ ወይም ፡ ሌላ ፡ የእጅ ፡ ሥራ ፡ ለማያውቅ ፡ ሰው ፡ በጣም ፡ የሚሻለች ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ጊዜውን ፡ ለማሳለፍ ፡ እጅግ ፡ ያስጨንቃል ፡፡

እኛ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሰዎች ፡ እስካሁን ፡ አለመድነውም ፡ እንጂ ፡ ሌሎቹ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ከጽሕፈትና ፡ ከእጅ ፡ ሥራ ፡ በቀር ፡ ሙዚቃ ፡ በመስማትና ፡ ዳንስ ፡ (ዘፈን)በማድረግ ፡ ብዙውን ፡ ሰዓት ፡ ያሳልፉታል ፡፡

ከ፩ ሰዓት ፡ እስከ ፡ ፫ ሰዓት ፡ የቁርስ ፡ ጊዜ ፡ ነው ፡፡ ከ፫ ሰዓት ፡ እስከ ፭ሰዓት ፡ የጽሕፈትና ፡ የእጅ ፡ ሥራ ፡ ጊዜ ፡ ነው ፡፡ ከ፭ ሰዓት ፡ እስከ ፡ ፮ሰዓት ፡ ሙዚቃ ፡ የመስሚያ ፡ ጊዜ ፡ ነው ፡፡

ከ፮ ሰዓት ፡ እስከ ፡ ፯ ሰዓት ፡ የምሳ ፡ ጊዜ ፡ ነው ፡፡ ከ፯ ሰዓት ፡ እስከ ፡ ፲፩ሰዓት ፡ የዕረፍት ፡ ወይም ፡ የጽሕፈትና ፡ የእጅ ፡ ሥራ ፡ ጊዜ ፡ ነው ፡፡

ከ፲፩ ሰዓት ፡ እስከ ፡ ፲፪ ሰዓት ፡ ሙዚቃ ፡ የመስሚያ ፡ ጊዜ ፡ ነው ፡፡

ከማታው ፡ ከ፩ ሰዓት ፡ እስከ ፡ ፪ ሰዓት ፡ የራት ፡ ጊዜ ፡ ነው ፡፡ ከ፪ሰዓት ፡ እሰከ ፡ ፫ ሰዓት ፡ ዕረፍት ፡ ነው ፡፡ ከ፫ ሰዓት ፡ እስከ ፡ ፮ ሰዓት ፡ ዳንስና ፡ የሙዚቃ ፡ ጫዋታ ፡ ነው ፡፡ ይህን ፡ በመሰለ ፡ በሥራና ፡ በደስታ ፡ ጊዜውን ፡ ባያሣልፉት ፡ በጣም ፡ ችግር ፡ ይሆንባቸው ፡ ነበር ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፵፩ ።

በጥር ፡ ፲፰ ቀን ፡ ከጅቡቲ ፡ ተነሥተን ፡ ወደ ፡ ድሬዳዋ ፡ ተጓዝን ። በ፲፩ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ድሬዳዋ ፡ ገባተን ፡ በማግሥቱ ፡ አዋሽ ፡ አደርን ። ከአዋሽም ፡ በ፩ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ተነሥተን ፡ በጥር ፡ ፳ ቀን ፡ ወደ ፡ ማታ ፡ በ፲ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ በአዲስ ፡ አበባ ፡ ባቡር ፡ ማቆሚያ ፡ ደረስን ።

በባቡር ፡ መቋሚያም ፡ መሳፍንቱና ፡ መኳንንቱ ፤ ሌሎችም ፡ አብሮ ፡ አደጎቼና ፡ ባልንጀሮቼ ፤ ከውጭ ፡ አገርም ፡ ሰዎች ፡ ወዳጆቼ ፡ የሆኑት ፡ በብዙ ፡ ተሰብስበው ፡ ይጠብቁኝ ፡ ነበርና ፡ ተሰልፈው ፡ የነበሩት ፡ የከተማ ፡ ዘበኞች ፡ የሰላምታ ፡ ጥሩምባ ፡ መንፋት ፡ ሲጀምሩ ፡ በፍጥነት ፡ ከባቡሩ ፡ ወርጄ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱን ፡ መላክተኛ ፡ አክብረው ፡ ለመቀበል ፡ ወደ ፡ መጡት ፡ ወደ ፡ ልዑል ፡ ራስ ፡ ኃይሉና ፡ ወደ ፡ ልዑል ፡ ራስ ፡ ስዩም ፡ ቀርቤ ፡ እጅ ፡ ነሥቼ ፡ ተገናኘሁ ። የቀሩትም ፡ ወዳጆቼና ፡ ዘመዶቼ ፡ በየተራ ፡ እየቀረቡ ፡ ሰላምታ ፡ ሰጡኝ ።

በማረፊያው ፡ ቤት ፡ ፭ ደቂቃ ፡ ያህል ፡ አርፌ ፡ ስወጣ ፡ ጃንሆይ ፡ በቸርነታቸው ፡ ልዩ ፡ አውቶሞቢል ፡ አዘውልኝ ፡ ኑሮ ፡ በልዩ ፡ አውቶሞቢል ፡ ተቀምጬ ፡ ወደ ፡ ጃንሆይ ፡ ሔድሁ ።

በጃንሆይም ፡ ፊት ፡ በደረስሁ ፡ ጊዜ ፡ መሬቱንና ፡ ጫማቸውን ፡ ስሜ ፡ ከቆምሁ ፡ በኋላ ፡ በጃፓን ፡ አገር ፡ የተደረገልኝን ፡ የክብር ፡ አቀባበልና ፡ ደስታዬን ፡ ባጭሩ ፡ አድርጌ ፡ ተናገርሁና ፡ ተሰናብቼ ፡ ወጣሁ ።

ወደ ፡ ቤቴም ፡ በደረስሁ ፡ ጊዜ ፡ ቤተ ፡ ዘመዶቼ ፡ ሁሉ ፡ ተሰብስበው ፡ ይጠብቁ ፡ ነበርና ፡ ገና ፡ ከአውቶሞቢል ፡ ስወርድ ፡ ታላቅ ፡ ደስታና ፡ እልልታ ፡ አደረጉ ።

እኔም ፡ ወደ ፡ ሀገሬ ፡ ተመልሼ ፡ ከቤተ ፡ ዘመዶቼ ፡ ጋራ ፡ በደህና ፡ ስለ ፡ ተገናኘሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰገንሁ ።

ተጨረሰ ።